የሚቀር ፡ ንጹሕና ፡ ቅዱስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡፡ በመጨረሻ ፡ እንድንደርስ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ደስታው ፡፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

በመጨረሻ ፡ ያለ ፡ ‘አሜን’ ፡ ጉባኤ ፡ ሁለግዜ ፡ ከቄስ ፡ ጋራ ፡ ልትበል ፡፡ ከዚህም ፡ ወዲያ ፡ ቄስ ፡ በጉልበቱ ፡ ይምበርከክ ፡፡ በምትሰማም ፡ ድምጽ ፡ የጌታችንን ፡ ጸሎት ፡ ይጸልይ ፡፡ ሕዝብ ፡ ደግመው ፡ ተንበርክከው ፡ ሳሉ ፡ ይህችን ፡ ጸሎት ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይሉ ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችንን ፡ የሚበቃንን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ፡፡ ይቀር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቀር ፡ እንደምንል ፡ ለኛ ፡ ያለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጅ ፡፡ ያንተ ፡ ነውና ፡ መንግሥት ፡፡ ኃይልም ፡፡ ምስጋናም ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ይበል ፡፡

አቤቱ ፡ ከንፈራችንን ፡ ክፈት ፡፡

ምላሽ ፡፡ አፋችንም ፡ ምስጋናህን ፡ ይገልጻል ፡፡

ቄስ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ፈጥነህ ፡ አድነን ፡፡

ምላሽ ፡፡ አቤቱ ፡ ቶሎ ፡ እርደን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁላቸው ፡ ተነሥተው ፡ ቄስ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

ምላሽ ፡፡ በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ፡፡ ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ቄ ፡፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡፡

ም ፡፡ የእግዚአብሔር ፡፡ ስም ፡ ይመስገን ፡፡



የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ይህችን ፡ ከዚህ ፡ የምትከተለውን ፡ መዝሙር ፡ ያንብቡ ፡ በፋሲካ ፡ እንጅ ፡፡ በርሱ ፡ ሌላ ፡ መዝሙር ፡ ይነበባልና ፡፡ በወር ፡ በወርም ፡ በ፲፱ኛ ፡ ቀን ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ አያንብቡት ፡ ከሌሎች ፡ መዝሙራት ፡ ጋራ ፡ እንጅ ፡ እንደ ፡ ሥርዓታቸው ፡፡

መዝሙር ፡ ፺፭፡፡

ኑ ፡ ደስ ፡ ይበለን ፡ በእግዚአብሔር ፡፡ እልልም ፡ እንበል ፡ ለመድኃኒታትን ፡ መጸጀ ፡፡

ወደ ፡ ፊቱ ፡ እንድረስ ፡ በምስጋና ፡፡ በዝማሬም ፡ እልል ፡ እንበልለት ፡፡

እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡፡ ታላቅ ፡ ንጉሥም ፡ ባማልክት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡፡

የምድር ፡ ማእዝን ፡ በጁ ፡ ነውና ፡፡ ረጅሞችም ፡ ተራሮች ፡ ለርሱ ፡ ናቸው ፡፡

ባሕርም ፡ የርሱ ፡ ነውና ፡ እርሱም ፡ ፈጠረው ፡፡ እጆቹም ፡ ደርቅን ፡ ፈጠሩ ፡፡

ኑ ፡ እንስገድ ፡ እንገዛም ፡፡ በፈጠረነም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በጉልበታችን ፡ እንበርከክ ፡፡

እርሱ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ፡፡ እኛም ፡ የመሰማርያው ፡ ሕዝብ ፡ ነነ ፡ የጁም ፡ በጎች ፡፡

ዛሬ ፡ እላንት ፡ ድምጹን ፡ ከሰማችሁ ፡ ልባችሁን ፡ አታጽኑ ፡፡ በቍጣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡ በፈተናም ፡ ቀን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡

አባቶቻችሁ ፡ በፈተኑኝ ፡ ጊዜ ፡፡ ፈተኑኝ ፡ ስራየንም ፡ አዩ ፡፡

ያችን ፡ ትውልድ ፡ አርብዓ ፡ አመት ፡ ተቈጣሁ ፡ አልሁም ፡፡ ይህች ፡ ሕዝብ ፡ በልባቸው ፡ ደስታሉ ፡፡ እርሳቸውስ ፡ መንገዴን ፡ አያውቁም ፡፡

በቍጣየም ፡ ማልሁባቸው ፡ ወደ ፡ ዕረፍቴ ፡ እንዳ ይገቡ ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንደሆነ ፡፡ ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ከዚያም ፡ ወደ ያ ፡ የመዝሙራት ፡ ማንበብ ፡ ይከተል ፡ እንደ ፡ ሥርዓታቸው ፡፡ በመዝሙር ፡ ሁሉም ፡ በመጨረሻው ፡ ይህ ፡ ይከተል ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንደሆነ ፡፡ ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ፊተኛውን ፡ ማንበብ ፡ ከብሉይ ፡ ሥርዓት ፡ ያንበብ ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ሰሙት ፡ እንደ ያስተውሉትም ፡፡ ከዚያም ፡ ወደ ያ ፡ ይህች ፡ ምስጋና ፡ ትከተል ፡፡

እኛ ፡እናመሰግንሃለን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ እናስታውቃለን ፡፡

ምድር ፡ ሁሉ ፡ ትሰግድልሃለች ፡ ለዘላለም ፡ አባት ፡፡

ወደንተ ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፡ ሰማያትም ፡፡ በርሳቸውም ፡ ያሉ ፡ ሥልጣናት ፡ ሁሉ ፡ ይጸራሉ ፡፡

ወደንተ ፡ ኪሩቤልና ፡ ሱራፊል ፡ ለዘወትር ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ይጸራሉ ፡፡

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡፡

ሰማይና ፡ ምድር ፡ በክብርህ ፡ ምስጋና ፡ ይመላሉ ፡፡

የሐዋርያት ፡ የከበረች ፡ ጉባኤያቸው ፡ ያመሰግኑሃል ፡፡

የነቢያትም ፡ የተባረከች ፡ አንድነት ፡ ያመሰግኑሃል ፡፡

የተመሰገኑም ፡ የሰማዕቶች ፡ ሠራዊት ፡ ያመሰግኑሃል ፡፡

ባለምም ፡ ሁሉ ፡ ያለች ፡ ቅድስት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያን ፡ ታስታውቅሃለች ፡፡

ምስጋናህ ፡ ያልወሰነች ፡ አንተን ፡ አብ ፡ ሆይ ፡፡



የከበረውንም ፡ እውነተኛውንም ፡ አንደኛውንም ፡ ልጅህ ፡፡

ጰራቅሊጦስም ፡ የሚሆነውን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡፡

አንተ ፡ የምስጋና ፡ ንጉሥ ፡ ነህ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡፡

አንተ ፡ የአብ ፡ የዘላለም ፡ ልጁ ፡ ነህ ፡፡

ሰውን ፡ ታድን ፡ ዘንድ ፡ በፈቀድህ ፡ጊዜ ፡ የድንግልን ፡ ማኅፀን ፡ አልናቅህም ፡፡

የሞትን ፡ ስለት ፡ ባሸነፍህ ፡ ጊዜ ፡ መንግሥት ፡ ሰማያትን ፡ ለምእምናን ፡ ሁሉ ፡ ከፈትህ ፡፡

አንተ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ በአብም ፡ ምስጋና ፡ ትቀመጣለህ ፡፡

ፈራጃችን ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ እንድትመጣ ፡ እናምናለን ፡፡

ስለዚህም ፡ እንለምንሃለን ፡፡ በከበረ ፡ ደምህ ፡ የተበጀሃቸውን ፡ ባሮችህ ፡ ትረዳ ፡ ዘንድ ፡፡

ከቅዱሳንህ ፡ ጋራ ፡ አስቍጠራቸው ፡ በዘላለም ፡ ምሰጋና ፡፡

አቤቱ ፡ ሕዝብህን ፡ አድን ፡፡ ርስትህንም ፡ ባርክ ፡፡

ጠብቃቸው ፡፡ ለዘላለምም ፡ ከፍ ፡ አድርጋቸው ፡፡

ዕለት ፡ ዕለት ፡ እናከብርሃለን ፡፡

ለስምህም ፡ ለዘላለም ፡ እንገዛለን ፡፡

ፍቀድ ፡ አቤቱ ፡ ዛሬ ፡ ከኃጢአት ፡ ትጠብቀን ፡ ዘንድ ፡፡

ማረን ፡ አቤቱ ፡ ማረን ፡፡

አቤቱ ፡ ምህረትህን ፡ አብራልን ፡፡ ባንተ ፡ እንደመነ ፡፡

አቤቱ ፡ ባንተ ፡ ታመንሁ ፡፡ ለዘላለም ፡ አታሳፍረኝ ፡፡

ቄስም ፡ ከዚያ ፡ ወደ ያ ፡ ሁለተኛውን ፡ ማንበብ ፡ ያንብብ ፡ ካደስ ፡ ኪዳን ፡ የተያዘውን ፡፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ይችን ፡ የዘካርያስን ፡ ምስጋና ፡ ይበሉ ፡፡ ሉቃስ ፡ ፩፡ ፷፰፡፡

የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ፡፡ ሕዝቡን ፡ ጐብኝትዋልና ፡ መድኃኒትንም ፡ አድርጎላቸዋልና ፡፡

የመድኃኒትም ፡ ቀንድ ፡ አስነሣልን ፡ በባርያው ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡፡

ካለም ፡ ፍጥረት ፡ ጀምሮ ፡ በነበረት ፡ በቅዱሳን ፡ በነቢያ
ቱ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡፡
ከጸላቶቻችን ፡ እንድን ፡ ዘንድ ፡ ከሚጸሉነም ፡ ሁሉ ፡
እጅ ፡፡
ላባቶቻችንም ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ ምህረቱን ፡ ይ
ፈጽም ፡ ዘንድ ፡፡ የተቀደሰቸውንም ፡ ሥርዓቱን ፡ ያስብ ፡
ዘንድ ፡፡
ላባታችንም ፡ ላብርሃም ፡ የማለለቱን ፡ መሐላውን ፡፡
ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ከጸላቶቻችን ፡ እጅ ፡ ድነን ፡ እናገለግ
ለው ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ ፍርሃት ፡፡
በቅድስና ፡ በጽድቅም ፡ በፊቱ ፡ የሕይወታችን ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡፡
አንተም ፡ ሕፃን ፡ ሆይ ፡ የልዑል ፡ ነቢይ ፡ ትባላለህ ፡፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትሔደለህና ፡ መንገዱን ፡ ላማስንደት ፡፡
የመድኃኒትን ፡ ዕውቀት ፡ ለሕዝቡ ፡ ሰጥተህ ፡ በኃጢአታ
ው ፡ ስርየት ፡፡
በአምላካችን ፡ መሬራት ፡ በምህረቱም ፡፡ በርስዋ ፡ የጉ
በኘነበት ፡ ከላይ ፡ የወጣ ፡ ነግህ ፡፡
በጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጽላ ፡ ለተቀመጡት ፡ ያበራ ፡ ዘ
ንድ ፡፡
እግሮቻችነንም ፡ በሰላም ፡ መንገድ ፡ ያቀና ፡ ዘንድ ፡፡
ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

ወይስ ፡ ይህችን ፡ መዝሙር ፡፡ ፱፤

ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፡፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በይ ፡፡ ለ
እግዚአብሔር ፡ ተገዙ ፡ በደስታ ፡፡ በፊቱም ፡ ግቡ ፡ በልልታ ፡፡
እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እ
ወቁ ፡፡ እርሱ ፡ ፈጠረን ፡ እኛም ፡ አይደለነም ፡፡ እኛስ ፡ ወገ
ኖቹ ፡ ነን ፡ የመሰማርያውም ፡ በጎች ፡፡
ወደ ፡ ደጆቹ ፡ በመገዛት ፡ ግቡ ፡ ወደ ፡ ቤቶቹም ፡ በምስጋ
ና ፡ ስብሃትን ፡ ስጡት ፡፡ ስሙንም ፡ አመስግኑ ፡፡



እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነውና ፡፡ ምህረቱም ፡ ለዘላለም ፡
ነው ፡፡ እውነቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡፡
ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ቄስ ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ ቁመው ፡
የሐዋርያትን ፡ ስምዮሉን ፡ ይበሉ ፡ እንደዚህ ፡
ሲሉ ፡፡

እኔ ፡ አምናለሁ ፡ ሁሉን ፡ በሚችል ፡ በእግዚአብሔር ፡
አብ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ፈጣሪ ፡፡
ባንድ ፡ ልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ የተረገዘ ፡
በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡ የተወለደም ፡ ከማርያም ፡ ድንግል ፡፡
መከራም ፡ የተቀበለ ፡ በጲላጦስ ፡ በጴንጤናዊ ፡ ዘመን ፡፡ የ
ተሰቀለም ፡፡ የሞተም ፡፡ የተቀበረም ፡፡ ወደ ፡ ሲኦልም ፡ የ
ወረደ ፡፡ በሶስተኛውም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ የተነሣ ፡፡ ወደ ፡
ሰማይም ፡ የወጣ ፡፡ ሁሉንም ፡ ወደ ፡ ሚችል ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ቀኙ ፡ የተቀመጠ ፡፡ ከዚያም ፡ የሚ
መለስ ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ሊፈርድ ፡፡
አምናለሁም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡ ባንዲትም ፡ ቅድስ
ትና ፡ ካቶሊካዊት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡፡ በቅዱሳንም ፡ አን
ድነት ፡፡ በኃጢአትም ፡ ስርየት ፡፡ በሥጋውም ፡ ትንሣኤ ፡፡
በዘላለምም ፡ ሕይወት ፡፡ አሜን ፡፡

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ሁላቸው ፡ በጉልበታቸው ፡ ወ
ድቀው ፡ ይጸልዩ ፡፡ ቄስም ፡ በጽሩ ፡ ድምጽ ፡ እን
ደዚህ ፡ ይበል ፡፡

እግዚአብሔር ፡ ከላንተ ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡፡
ምላሽ ፡፡ ከመንፈስህም ፡ ጋራ ፡፡
ቀ ፡፡ እንጸልይ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረን ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡
አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡

መንግሥትህ : ትምጻ :: ፈቃድህ : በምድር : ትሁን : እንደ : ሆነች : በሰማይ :: እንጀራችንን : የሚበቃነን : ስጠነ፡ ዛሬ :: ደቅር : በለነ : በኛ : ያለውን :: እኛ : ደግመን : ደቅር : እንደ ምንል : ልኛ : ያለባቸውን :: ወደ : ፈተናም : አታግባን :: ከክፉ : አድነን : እንጅ :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ተነሥቶ : እንደህ : ደበል ::

አቤቱ : ምህረትህን : ገልጽልነ ::
ም :: መድኃኒትህንም : ስጠነ ::
ቄ :: አቤቱ : ንግሥትን : ጠብቅ ::
ም :: በምህረትህም : ስማነ : ወደንተ : ስንጸራ ::
ቄ :: አገልጋዮችህን : ጽድቅን : አልበሳቸው ::
ም :: የመረጽሀውንም : ሕዝብህ : ደስታ : ምላባቸው ::
ቄ :: አቤቱ : ሕዝብህን : አድን ::
ም :: ርስትህንም : ባርክ ::
ቄ :: ዕርቅን : ሰጥ : በዘመናችን : አቤቱ ::
ም :: የሚዋጋልን : የለምና : ካንተ : በቀር : አቤቱ ::
ቄ :: እግዚአብሔር : ሆይ : በውሥጣችን : ንጹሕ : ልብ : ፈጠርልን ::
ም :: ቅዱስ : መንፈስህንም : ከኛ : አታውጣ ::

ከዚያ : ወዲያም : ሶስት : ልመኖች : ይከተሉ :: መጀመርያቸውም : የሁድ : ወደስ : የባል : ልመና : በየጊዜው : ያለ :: ሁለተኛደታቸውም : ስለ : ዕርቅ :: ሶስተኛደታቸውም : ስለ : ጸጋ :: ሁላቸውም : ሲለምኑ : ጊዜ : ደንበርክኩ ::

## ሁለተኛ : ልመና ::

## ስለ : ዕርቅ ::

አምላክ : ሆይ :: አንተ : የርቅ : ፈጣሪ : ያንድነትም : ወደጅ : የምትሆን :: ዕውቀትህ : የዘላለም : ሕይወታችን : ናትና :: ባርነትህም : ፍጽምት : አርነት :: እኛን : ገሮች : ባሮችህን : ከጸላቶቻችን : ጸላትነት : ሁሉ : ጠብቅን :: እኛ :



በመጠበቅህ : በውነት : ታምነን : ከጸላት : ሁሉ : ኃይል : እንደንፈራ : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ኃይል :: አሜን ::

## ሶስተኛ : ልመና ::

## ስለ : ጸጋ ::

አቤቱ : ሰማያዊ : አባታችን :: ሁሉንም : የምትችል : ለዘላለምም : የምትኖር : እግዚአብሔር :: አንተ : በደህንነት : ወደዚህ : ቀን : መጀመርያ : አድርሰህናልና :: ዛሬ : በብርቱ : ኃይልህ : ጠብቀን : በኃጢአት : እንደንወድቅ :: ወደ : ፈተናም : እንደንሮጥ :: ስራችን : ሁሉ : ለፈቃድህ : ትገዛ : ዘንድ :: እኛም : በፊትህ : ጽድቅ : የሚሆነውን : ነገር : ሁለግዜ : እናደርግ : ዘንድ :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

ሊጣኒያ : የሚሉት : ሲነበብ : እርሱ : ከዚህ : ይከተል :: በሌላ : ጊዜ : ደህ : ደከተል ::

## ስለ : ንግሥት ::

አቤቱ : ሰማያዊ : አባታችን : ልዑልና : ኃይለኛ :: የነገሥታት : ንጉሥ : የጌቶችም : ጌታ :: ገዦችንም : አንተ : ብቻህን : የምትገዛቸው :: ከዙፋንህም : የምትመለከት : በምድር : ላይ : ወደ : ሚኖረት : ሁሉ :: ከለልባችን : እንለምንሃለን : በጸጋ : እንድትመለከት : ወደ : እመቤታችን : ወደ : ቢክቶርያ : ወደ : ንግሥታችን :: መንፈስ : ቅዱስህን : እንደህ : እንድትመላባት : እርስዋ : ለፈቃድህ : እንድትዘነብል :: በመንገድህም : እንድትመላለስ : ሁለግዜ :: ሰማያዊ : ስጥወታህን : መልተህ : አልብሳት :: በደህንነትም : በባለጠግነትም : እኑራት : ለብዙ : ዘመን :: ኃይልንም : ስጣት : ጸላቶችዋን : ሁሉን : ታሸንፈቸው : ዘንድ :: ከዚች : ሕይወትም : በኋላ : ወደ : ዘላለም : ደስታና : ደህንነት : አድርሳት :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

## ስለ : ንግሥት : ዘመዶች ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : የበጎ : ነገር : ሁሉ : ምን

ጭ ። እኛ ፡ ኢቴጌ ፡ አድላይድን ፡ ገዢ ፡ አልበርትንም ፡ የዌልስንም ፡ ገዢ ፡ የንግሥትንም ፡ ዘመዶች ፡ ሁሉ ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ በትሕትና ፡ እንለምነሃለን ። መንፈስ ፡ ቅዱስህን ፡ አልበሳቸው ። ሰማያዊት ፡ ጸጋህንም ፡ ምላባቸው ። በደስታም ፡ ሁሉ ፡ አክናውናቸው ። ወደ ፡ ዘላለምም ፡ መንግሥትህ ፡ አድርሳቸው ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

ስለ ፡ ካህናት ፡ ስለ ፡ ሕዝብም ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ። አንተ ፡ ብቻ ፡ ታላቅ ፡ ታምራት ፡ የምታደርግ ። ለጳጳሳታችን ፡ ለቀሳውስታችንም ፡ እርሳቸውም ፡ ለታመኑባቸው ፡ ለማኅበሮች ፡ ሁሉ ፡ የደህንነትህን ፡ የጸጋህንም ፡ መንፈስ ፡ ስደድላቸው ። እርሳቸውም ፡ በውነት ፡ ደስ ፡ ያሰኙህ ፡ ዘንድ ፡ የማትጨርሰውን ፡ የበረከትህን ፡ ጠል ፡ አፍስስባቸው ። ይህነን ፡ ስጥ ፡ አቤቱ ፡ ስለ ፡ ጰራቅሊጦሳችን ፡ ስለ ፡ መኻከለኛችንም ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ምስጋና ። አሜን ።

የአፈ ፡ ወርቅ ፡ ጸሎት ፡

ስለ ፡ ተሰበሰቦች ፡ ጉባኤ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ልመናችነን ፡ ወደንተ ፡ እንደደረግነ ፡ ጸጋህን ፡ ሰጥተህናልና ። ሁለት ፡ ወይስ ፡ ሶስትም ፡ በስምህ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ልመናቸውን ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስደርገህልናልና ። የባሮችህን ፡ መሻትና ፡ ልመናን ፡ አሁን ፡ ፈጽም ፡ በጅ ፡ እንደሚላቸው ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ የውነትህን ፡ ዕውቀት ። በሚመጣውም ፡ ዓለም ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ስትሰጠነ ። አሜን ።

የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ። የእግዚአብሔርም ፡ ፍቅር ። የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አንድነት ። ከሁላችን ፡ ጋራ ፡ ይሁን ። ለዘላለም ። አሜን ።

## የማታ ፡ ጸሎት ፡ ሥርዓት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ባመት ፡ ሁሉ ፡ ለመጸለይ ።

በማታ ፡ ጸሎት ፡ በመጀመርያው ፡ አገልጋይ ፡ በታላቅ ፡ ድምጽ ፡ አንድ ፡ ወይስ ፡ አያሌን ፡ ከዚህ ፡ ከሚከተሉ ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ነቍጦች ፡ ያንብብ ። ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ከለዚህ ፡ ነቍጦች ፡ በኋላ ፡ የተጻፈውን ፡ ነገር ፡ ያንብብ ።

ኃጥእ ፡ ከሰራው ፡ ከኃጢአቱ ፡ ቢመለስ ። ቅኑና ፡ ጽድቅንም ፡ ቢያደርግ ። ነፍሱን ፡ ያድናታል ። ሕዝቅኤል ፡ ም ፡ ፲፰፡ ፳፯።

እኔ ፡ ዓመፃዬን ፡ አውቃለሁ ። ኃጢአቴም ፡ ሁለግዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ። መዝሙር ፡ ፶፩፡ ቍ ፡ ፫።

ከኃጢአቴ ፡ ፊትህን ፡ መልስ ። በደሌንም ፡ ሁሉን ፡ ደምስስ ። መዝሙር ፡ ፶፩፡ ቍ ፡ ፱፡

የእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ የተሰበረ ፡ መንፈስ ፡ ነው ። የተሰበረውን ፡ የተደቈሰውንም ፡ ልብ ፡ አትንቅም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ። መዝሙር ፡ ፶፩፡ ፲፯።

ልባችሁን ፡ ቅደዱ ፡ ልብሳችሁንም ፡ አይደለም ። ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ አምላካችሁ ፡ ተመለሱ ። እርሱ ፡ ርኅሩኅና ፡ መሓሪ ፡ ነውና ። ለቍጣ ፡ የዘገየ ። ቸርነቱም ፡ ታላቅ ፡ ናት ። በክፋትም ፡ ያዝናል ። ዮኤል ፡ ፪፡ ፲፫።

ምህረትና ፡ ይቅርታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ላምላካችን ፡ ነው ፡ እኛ ፡ እንኳ ፡ በላየው ፡ በተነሣነ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ የአምላካችንን ፡ ቃል ፡ ባልሰማነ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ በፊታችን ፡ ባኖራቸው ፡ በሕጋጋቱ ፡ እንመላለስ ፡ ዘንድ ። ዳንኤል ፡ ፱፡ ፱፡ ፲።

አቤቱ ፡ አትቅሠፈኝ ፡ በፍርድ ፡ እንጅ ፡ በቍጣህም ፡ አይደለም ፡ እንደታጠፋኝ ። ኤርምያስ ፡ ፲፡ ፳፬። መዝሙር ፡ ፮፡ ፩።

ንስሓ : ግቡ :: መንግሥተ : ሰማያት : ቀርባለችና :: ማቴዎስ : ፫፤ ፪::

ልነሣና : ልሒድ : ወደባቴ : ልበለውም :: አባቴ : ሆይ : በሰማይ : በፊትህም : በደልሁ :: ደግሞም : ልጅህ : እባል : ዘንድ : አይገባኝም :: ሉቃስ : ፲፭፤ ፲፰፤ ፲፱::

ከባርያህ : ጋራ : ወደ : ፍርድ : አትግባ : አቤቱ :: ሕያው : ሁሉ : በፊትህ : ጻድቅ : አይደለምና :: መዝሙር : ፻፵፪፤ ፪::

ኃጢአት : የለብንም : ብንል : እኛ : ራሳችንን : እናስታለን : እውነትም : የለነም :: በኃጢአታችን : ግን : ብንናዘዝ : እርሱ : የታመነ : ጻድቅም : ነው :: ኃጢአታችንን : ይቅር : ይለነ : ዘንድ : ከግፍም : ሁሉ : ያነጻነ : ዘንድ :: የዮሐንስ : ፩፤ መልእክት : ፩፤ ም : ፰፤ ፱፤ ቍ ::

እጅግ : የተወደዳችሁ : ወንድሞቼ : ሆይ :: መጽሐፍ : ቅዱስ : በልዩ : ልዩ : ስፍራው : የኃጢአታችንን : ያመፃችንንም : ብዛት : ልናውቅ : ልናስታውቀውም : ይመክረናል :: ሁሉንም : በሚችል : በእግዚአብሔር : በሰማያዊ : አባታችን : ፊት : አንደንከድነው : እንደንሰውረውም :: በትሑትና : በነገር : በሚያዝንም : በሚሰማም : ልብ : እንድናስታውቀው : እንጂ :: ባልተወሰነች : በቸርነቱ : በምህረቱም : ስርየቱን : እንቀበል : ዘንድ :: ኃጢአታችንንስ : በትሕትና : ማስታወቅ : ሁለግዜ : ይገባናል :: ከሁሉ : ይልቅ : ግን : ከጁ : ስለ : ተቀበልነ : ስለ : ስጥወታው : ሁሉ : እናመሰግነው : ዘንድ : በሁሉም : የሚገባውን : ምስጋና : እንገልጽ : ዘንድ :: ቅዱስ : ቃሉንም : እንሰማ : ዘንድ :: ለሥጋችንና : ለነፍሳችንም : የሚገባነን : የምንሻውንም : ነገር : ሁሉ : ከርሱ : እንለምን : ዘንድ : በተሰበሰብነ : ጊዜ :: ስለዚህ : ከዚህ : የተሰበሰባችሁትን : ሁላችሁን : እለምናችኋለሁ : በትሑት : ልብ : በታናሽም : በጽሩም : ድምጽ : ወደ : ሰማያዊ : ወደ : ጸጋ : ዙፋን : እንድትከተሉኝ : ከኔ : በኋላ : ስትሉ ::

አሁን : ሁላቸው : በጉልበታቸው : ተንበርክከው :: ጉባኤም : ሁሉ : ቄስን : ተከትለው : እንዴህ : ይበሉ ::



ሁሉን : የምትችል : በሁሉም : መሓሪ : ያለህ : አባታችን : ሆይ :: እኛ : እንደ : ጠፉ : በጎች : መንገድህን : ትተን : ሳትነ :: እንደልተገባነም : የልባችንን : ምክርና : መመኞት : ተከተልነ :: በተቀደሱም : ትእዛዛትህ : ላይ : በደልነ :: እኛ : እናደርገው : ዘንድ : የሚገባነውን : ነገር : አላደረግነም :: ላናድርገውም : የሚገባነን : ነገር : አደረግነ :: በመንፈሳችንም : ጤና : የለነም :: አንተ : ግን : አቤቱ : ማረነ : ቸጋረኞችን : በደለኞችንም :: በኃጢአታችን : አስታውቀንዛልና : እዘንለን :: ንስሓም : ገብተናልና : አድነን :: ተስፋ : እንደ : አስደረግህ : ለሰው : ወገን : ሁሉ : በክርስቶስ : የሱስ : በጌታችን :: በርሱም : መክንያት : መሓሪ : አባት : ሆይ : ስጠነ :: ከንግዴህ : ወዴህ : በበጎ : በጸደቀችም : በተቀደሰችም : ሕይወት : እንኖር : ዘንድ :: ለቅዱስ : ስምህ : ለምስጋና :: አሜን ::

ከዚያም : ወዲያ : ቄስ : ተነሥቶ : ሕዝብ : ገና : በጉልበታቸው : ሳሉ :: እርሱ : ብቻውን : የፍትሐትን : ነገር : ይናገር : እንዴህ : ሲል ::

ሁሉን : የሚችል : እግዚአብሔር : የጌታችን : የየሱስ : ክርስቶስ : አባት :: የኃጢአተኛውን : ሞት : የማይሻ :: ካመፃው : እንዲመለስ : እንዲድንም : እንጂ :: ሥልጣንንም : ትእዛዝንም : የሰጠ : ላገልጋዮቹ :: ለሚያዝኑ : ለሕዝቡ : የኃጢአታቸውን : ፍትሐትና : ስርየት : ይገልጹላቸው : ይናገርዋቸውም : ዘንድ :: እርሱ : በውነት : ንስሓ : ለሚገቡ : በቅዱስ : ወንጌሉም : ያለ : መጠራጠር : ለሚያምኑ : ኃጢአታቸውን : ያስቀርላቸዋል : ይፈታቸውማል :: ስለዚህ : እንለምነው : እውነተኛ : ንስሓ : መግባትን : መንፈስ : ቅዱሱንም : እንዲሰጠነ :: አሁን : የምናደርገው : ደስ : ያሰኘው : ዘንድ :: ከዚህም : ወዲያ : ከሕይወታችን : የሚቀር : ንጹሕና : ቅዱስ : ይሆን : ዘንድ :: በመጨረሻ : እንድንደርስ : ወደ : ዘላለም : ደስታው :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ቄስ ፡ ደግሞ ፡ በጉልበቱ ፡ ይምበ
ርክክ ፡፡ በምትሰማም ፡ ድምጽ ፡ የጌታችንን ፡ ጸ
ሎት ፡ ይበል ፡፡ ሕዝብም ፡ ተንበርክከው ፡ ይህች
ን ፡ ጸሎት ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይበሉ ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችንን ፡ የሚበቃንን ፡ ስጠን ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅር ፡ በለን ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቀር ፡ እንደ ምንል ፡ ልኛ ፡ ያለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ፡፡ ያንተ ፡ ነውና ፡ መንግሥት ፡ ኃይል ም ፡ ምስጋናም ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ይበል ፡፡

አቤቱ ፡ ከንፈራችንን ፡ ክፈት ፡፡

ም ፡፡ አፋችንም ፡ ምስጋናህን ፡ ይገልጸል ፡፡

ቁ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ፈጥነህ ፡ አድነን ፡፡

ም ፡፡ አቤቱ ፡ ቶሎ ፡ እርዳን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁላቸው ፡ ተነሥተው ፡ ቄስ ፡ እን
ደህ ፡ ይበል ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱ ስም ፡፡

ም ፡፡ በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንዲሆ
ን ፡፡ ለዘወተርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ቁ ፡፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡፡

ም ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይመስገን ፡፡

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ መዝሙራት ፡ እንደ ፡ ተከፈሉ ፡
ይነበቡ ፡፡ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ከብሉይ ፡ ሥርዓት ፡
አንድ ፡ ምዕራፍ ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡፡ ከዚያም ፡
ወዲያ ፡ የማርያም ፡ ምስጋና ፡ ትከተል ፡ ሉ
ቃስ ፡ ፩።

ነፍሴ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታላቅ ፡ ታደርገዋለች ፡፡ መንፈሴ ም ፡ በእግዚአብሔር ፡ በመድኃኒቴ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡፡



የባርያዪቱን ፡ መዋረድ ፡ አይቶዋልና ፡፡

እነሆ ፡ ከዛሬ ፡ጀምሮ ፡ ትውልድ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑኛልና ፡፡

ብርቱው ፡ ድንቅ ፡ አድርጎልኛልና ፡፡ ስሙም ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፡፡

ምህረቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ለሚፈሩት ፡፡

ኃይል ፡ በክንዱ ፡ አደረገ ፡፡ ትዕቢተኞችንም ፡ በልባቸው ፡ አሳብ ፡ በተነ ፡፡

ኃያላንንም ፡ ከዙፋናቸው ፡ አወረደ ፡፡ የተዋረዱትንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ፡፡

የተራቡትንም ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ አጸገባቸው ፡፡ ባለጠጎችን ም ፡ ባዶ ፡ ሰደዳቸው ፡፡

እሥራኤልን ፡ ባርያውን ፡ ረዳው ፡፡ ምህረቱንም ፡ አሰበ ፡ ላባቶቻችን ፡ እንደለ ፡ ላብርሃምና ፡ ለዘሩ ፡ ለዛላለም ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡

በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

ወይስ ፡ ይህች ፡ መዝሙር ፡ በወር ፡ በወር ፡ በ፲፪
ቀን ፡ እንጅ ፡፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በመዝሙራት ፡ ሥር
ዓት ፡ ተከትላለችና ፡፡

መዝመር ፡ ፺፯፡፡

እግዚአብሔርን ፡ ባዲስ ፡ ምስጋና ፡ አመስግኑት ፡፡ እር ሱ ፡ ድንቅ ፡ አድርጓልና ፡፡

ቀኙ ፡ አሸንፈለችና ፡ የተቀደሰችም ፡ ክንዱ ፡፡

እግዚአብሔር ፡ ማደኑን ፡ አሳየ ፡፡ ባሕዛብም ፡ ፊት ፡ ጽ ድቁን ፡ ገለጸ ፡፡

ምህረቱንና ፡ እውነቱንም ፡ ለእሥራኤል ፡ ቤት ፡ አሰበ ፡፡ የምድር ፡ ዳርም ፡ ሁሉ ፡ የአምላካችንን ፡ ማደን ፡ አዩ ፡፡

አንቺ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እልል ፡ ብዪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡፡ አዝመሪ ፡፡ ደስም ፡ ይበለሽ ፡፡ ዝማሬም ፡ አቅረቢ ፡፡

በመሰንቆ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዝማሬ ፡ አዝመሩ ፡፡ በመ ሰንቆ ፡ በዝማሬም ፡ ድምጽ ፡፡

በመለከትም ፡ በቀንድም ፡ ድምጽ ፡ በንጉሥ ፡ በእግዚአ ብሔር ፡ ፊት ፡ እልል ፡ በሉ ፡፡

ባሕርም ፡ ትጩኽ ፡ ያለባትም ፡ ሁሉ ፡ ዓለምም ፡ የሚኖ
ረበትም ፡፡
ፈሳሾች ፡ እጃቸውን ፡ ይጨብጭቡ ፡፡ ተራሮችም ፡ አብረ
ው ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡፡ በምድር ፡ ለመፍረድ ፡ ይመጻ
ልና ፡፡
ዓለምን ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርዷል ፡፡ አሕዛብንም ፡ በቅን ፡፡
ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ያዲስ ፡ ሥርዓት ፡ ማንበብ ፡ ይ
ከተል ፡ እንደ ፡ ተከፈለ ፡፡ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ የ
ስምዖን ፡ ምስጋና ፡ ሉቃስ ፡ ፪፤ ፳፱፡፡

ዛሬ ፡ ባርያህን ፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ነገርህ ፡ በሰላም ፡ ታሰናብ
ታለህ ፡፡
ዓይኖቼ ፡ ማደንህን ፡ አይተዋልና ፡፡
ያዘጋጀህውን ፡ ባሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡፡
ብርሃን ፡ ሁኖ ፡ አሕዛብን ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፡ ለወገንህም ፡
ለእሥራኤል ፡ ክብር ፡ ሊሆን ፡፡
ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

ወይስ ፡ ይህች ፡ መዝሙር ፡ ፷፯፡፡

እግዚአብሔር ፡ ይማርነ ፡ ይባርክነም ፡፡ ፊቱንም ፡ ያበራል
ነ ፡ ይማርነም ፡፡
መንገድህ ፡ በምድር ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡፡ መድኃኒትህ
ም ፡ ላሕዛብ ፡ ሁሉ ፡፡
አሕዛብ ፡ ይገዙልህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡፡ ይገዙልህ ፡
አሕዛብ ፡ ሁላቸው ፡፡
አሕዛብ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሴትም ፡ ያድርጉ ፡፡ ባሕዛ
ብ ፡ በጽድቅ ፡ ትፈርዷለህና ፡፡ አሕዛብንም ፡ በምድር ፡ ትመ
ራለህና ፡፡
አሕዛብ ፡ ይገዙልህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡፡ ይገዙልህ ፡
አሕዛብ ፡ ሁላቸው ፡፡



የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ምድር ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ፡፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ አምላካችን ፡ ይባርክናል ፡፡
ይባርክናል ፡ እግዚአብሔር ፡፡ የምድርም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡
ይፍሩት ፡፡
ምስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ቄስ ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ የሐዋርያት
ን ፡ ሃይማኖት ፡ ይበል ፡፡

እኔ ፡ አምናለሁ ፡ ሁሉን ፡ በሚችል ፡ በእግዚአብሔር ፡ አ
ብ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ፈጣሪ ፡፡
ባንድ ፡ ልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ የተረገ
ዘ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡ የተወለደም ፡ ከማርያም ፡ ድንግ
ል ፡፡ መከራም ፡ የተቀበለ ፡ በጲላጦስ ፡ በጴንጤናዊ ፡ ዘመ
ን ፡፡ የተሰቀለም ፡፡ የሞተም ፡፡ የተቀበረም ፡፡ ወደ ፡ ሲኦል
ም ፡ የወረደ ፡፡ በሶስተኛም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ የተነሣ ፡፡ ወ
ደ ፡ ሰማይም ፡ የወጣ ፡፡ ሁሉንም ፡ ወደ ፡ ሚችል ፡ ወደ ፡ እ
ግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ቀኙ ፡ የተቀመጠ ፡፡ ከዚያም ፡ የ
ሚመለስ ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ሊፈርድ ፡፡
አምናለሁም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡ ባንዲትም ፡ ቅድስት
ና ፡ ከቶሊካዊት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡፡ በቅዱሳንም ፡ አንድ
ነት ፡፡ በኃጢአትም ፡ ስርየት ፡፡ በሥጋውም ፡ ትንሣኤ ፡ በዘ
ላለምም ፡ሕይወት ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ከጉባኤ ፡ ጋራ ፡ በጉልበቱ ፡
ተምበርክኮ ፡ በጽሩ ፡ ድምጽ ፡ ይጸልይ ፡ እንዲ
ህ ፡ ሲል ፡፡

እግዚአብሔር ፡ ከላንተ ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡፡
ም ፡፡ ከመንፈስህም ፡ ጋራ ፡፡
ቄ ፡፡ እንጸልይ ፡፡ አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረነ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡
አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡

መንግሥትህ ፡ ትምጸ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችነን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ልኛ ፡ ያለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጅ ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ተነሥቶ ፡ እንደዩ ፡ ይበል ፡፡

አቤቱ ፡ ምህረትህን ፡ ገልጽልነ ፡፡
ም ፡፡ መድኃኒትህንም ፡ ስጠነ ፡፡
ቄ ፡፡ አቤቱ ፡ ንግሥትን ፡ ጠብቅ ፡፡
ም ፡፡ በምህረትህም ፡ ስማነ ፡ ወደንተ ፡ ስንጸራ ፡፡
ቄ ፡፡ አገልጋዮችህን ፡ ጽድቅን ፡ አልበሳቸው ፡፡
ም ፡፡ የመረጽሀውንም ፡ ሕዝብህ ፡ ደስታውን ፡ ምላቸው ፡፡
ቄ ፡፡ አቤቱ ፡ ሕዝብህን ፡ አድን ፡፡
ም ፡፡ ርስትህንም ፡ ባርክ ፡፡
ቄ ፡፡ ዕርቅን ፡ ስጥ ፡ በዘመናችን ፡ አቤቱ ፡፡
ም ፡፡ ለኛ ፡ የሚዋጋ ፡ የለምና ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡ አቤቱ ፡፡
ቄ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ልባችነን ፡ ንጹሕ ፡ አድርግልነ ፡፡
ም ፡፡ ቅዱስ ፡ መንፈስህንም ፡ ከኛ ፡ አታውጣ ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሶስት ፡ ልመናች ፡ ይከተሉ ፡፡ መጀመርያቸውም ፡ የሁድ ፡ ወይስ ፡ የበዓል ፡ ልመና ፡ በየጊዜው ፡ ያለ ፡፡ ሁለተኛቸውም ፡ ስለ ፡ ዕርቅ ፡፡ ሶስተኛቸውም ፡ በመከራ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ረዲት ፡ ከዚህ ፡ እንደሚከተል ፡፡

አቤቱ ፡ የተቀደሰ ፡ ፈቃድ ፡ በጎ ፡ ምክርም ፡ የሚገባ ፡ ስራም ፡ ሁሉ ፡ ካንተ ፡ ወጥትዋልና ፡፡ ዓለም ፡ ይሰጣት ፡ ዘንድ ፡ የማይቻለውን ፡ ሰላም ፡ ለባሮችህ ፡ ስጥ ፡፡ ልባችን ፡ ለትእዛዛትህ ፡ ለመታዘዝ ፡ ይቀና ፡ ዘንድ ፡፡ ከጸላቶቻችንም ፡ ፍርሃት ፡ በጅህ ፡ ተጠብቀን ፡ ዘመናችነን ፡ በረፍትና ፡ በርቅ ፡ እናሳልፍ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ ምግባር ፡፡ አሜን ፡፡



ስለ ፡ ረዲት ፡ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡፡

ጨለማችነን ፡ እንድታበራ ፡ እንለምንሃለን ፡ አቤቱ ፡፡ በዚች ፡ ሌሊትም ፡ ካለ ፡ ከመከራና ፡ ከፈተና ፡ ሁሉ ፡ በታላቅ ፡ ምህረትህ ፡ ጠብቅን ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ልጅህ ፡ ስለ ፡ መድኃኒታችን ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ፍቅር ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ንግሥት ፡፡

አቤቱ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ልዑልና ፡ ኃይለኛ ፡፡ የነገሥታት ፡ ንጉሥ ፡ የጌቶችም ፡ ጌታ ፡፡ ገዦችንም ፡ አንተ ፡ ብቻህን ፡ የምትገዛቸው ፡፡ ከዙፋንህ ፡ የምትመለከት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡፡ ከለልባችን ፡ እንለምንሃለን ፡ በጸጋ ፡ እንድትመለከት ፡ ወደ ፡ እመቤታችን ፡ ወደ ፡ ቢክቶርያ ፡ ወደ ፡ ንግሥታችን ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህን ፡ እንዲህ ፡ እንድትመላባት ፡ እርስዋ ፡ ለፈቃድህ ፡ እንድትዘነብል ፡፡ በመንገድህም ፡ እንድትመላለስ ፡ ሁልግዜ ፡፡ ሰማያዊ ፡ ስጥወታህን ፡ መልተህ ፡ አልብሳት ፡፡ በደህንነትም ፡ በባለጠግነትም ፡ እኑራት ፡ ለብዙ ፡ ዘመን ፡፡ ኃይልንም ፡ ስጣት ፡ ጸላቶችዋን ፡ ሁሉን ፡ ታሸንፈቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ከዚች ፡ ሕይወትም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ደስታና ፡ ደህንነት ፡ አድርሳት ፡፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ንግሥት ፡ ዘመዶች ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ የበጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምንጭ ፡፡ እኛ ፡ ኢቴጌ ፡ አድላይድን ፡ ገዢ ፡ አልበርትንም ፡ የዌልስንም ፡ ገዢ ፡ የንግሥትንም ፡ ዘመዶች ፡ ሁሉ ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ በትሕትና ፡ እንለምነሃለን ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህን ፡ አልበሳቸው ፡፡ ሰማያዊት ፡ ጸጋህንም ፡ ምላባቸው ፡፡ በደስታም ፡ ሁሉ ፡ አክናውናቸው ፡ ወደ ፡ ዘላለምም ፡ መንግሥትህ ፡ አድርሳቸው ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ካህናት ፡ ስለ ፡ ሕዝብም ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡፡ አንተ ፡ በቻ ፡ ታላቅ ፡ ታምራት ፡ የምታደርግ ፡፡ ለጳጳሳታችን ፡ ለቀሳውስታችንም ፡ እርሳቸውም ፡ ለታመኑባቸው ፡ ለማኅበሮች ፡ ሁሉ ፡ የደህንነትህን ፡ የጸጋህንም ፡ መንፈስ ፡ አውረድላቸው ፡፡

እርሳቸውም ፡ በውነት ፡ ደስ ፡ ያሰኙህ ፡ ዘንድ ፡ የማትጨርሰውን ፡ የበረከትህን ፡ ጠል ፡ አፍሰስባቸው ፡፡ ይህንን ፡ ስጥ ፡ አቤቱ ፡ ስለ ፡ ጰራቅሌጦሳችን ፡ ስለ ፡ መኻከለኞችንም ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ምስጋና ፡፡ አሜን ፡፡

የአፈ ፡ ወርቅ ፡ ጸሎት ፡

ስለ ፡ ተሰበሰበች ፡ ጉባኤ ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ፡፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ልመናችንን ፡ ወደንተ ፡ እንደደረግነ ፡ ጸጋህን ፡ ሰጥተህናልና ፡፡ ሁለት ፡ ወይስ ፡ ሦስትም ፡ በስምህ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ልመናቸውን ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስደርገህልናልና ፡፡ የባሮችህን ፡ መሻትና ፡ ልመናን ፡ አሁን ፡ ፈጸም ፡ በጅ ፡ እንደሚላቸው ፡፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የውነትህን ፡ ዕውቀት ፡፡ በሚመጣውም ፡ ዓለም ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ስትሰጠን ፡፡ አሜን ፡፡

የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ፍቅር ፡፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አንድነት ፡፡ ከሁላችን ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

---

በጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

በልደት ፡ በእጲፋንያስም ፡ በቅዱስ ፡ ማትያስም ፡ በፋሲካም ፡ በርገትም ፡ በጰራቅሊጦስም ፡ በዮሐንስ ፡ መጥመቅም ፡ በቅዱስ ፡ ያዕቆብም ፡ በቅዱስ ፡ በርቶሎሚዎስም ፡ በቅዱስ ፡ ሲሞንና ፡ ቅዱስ ፡ ይሁዳም ፡ በቅዱስ ፡ እንድርያስም ፡ በሥላሴም ፡ በዓለት ፡ በጽዋት ፡ ጸሎት ፡ በሐዋርያት ፡ ስምቦሎን ፡ ፈንታ ፡ ይህች ፡ የቅዱስ ፡ አተናቴዎስ ፡ ስምቦሎን ፡ የምትባል ፡ የክርስቲያን ፡ ሃይማኖታችን ፡ ስምቦሎን ፡ ትደግም ፡ ቄስና ፡ ሕዝብ ፡ ቁመው ፡ እንደዚህ ፡ ሲሉ ፡፡

ይድን ፡ ዘንድ ፡ የሚሻ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከቶሊካዊትን ፡ ሃይማኖት ፡ እንዲጠብቅ ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ይፈለግበታል ፡፡



ይህችንም ፡ ሃይምኖት ፡ ደህና ፡ ያለ ፡ መለወጥም ፡ ኑራ ፡ የማይጠብቃት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ሳይጠፋ ፡ አይቀርም ፡፡

ከቶሊካዊት ፡ ሃይማኖትም ፡ ይህች ፡ ናት ፡፡ አንዱን ፡ አምላክ ፡ በሥላሴ ፡ ሥላሴንም ፡ ባንድነት ፡ እንድናመልክ ፡፡

አካላትን ፡ ሳንደበልቅ ፡ ህላዌንም ፡ ሳንከፍል ፡፡

አንድ ፡ አካል ፡ ለአብ ፡ ነውና ፡ ሌላውም ፡ ለወልድ ፡ ሌላውም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡

ነገር ፡ ግን ፡ የአብ ፡ የወልድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ መለኮትነት ፡ ሁሉ ፡ አንዲት ፡ ናት ፡፡ ክብራቸውም ፡ እኩል ፡ ግርማቸውም ፡ ያንዲት ፡ ዘላለምና ፡ ናት ፡፡

አብ ፡ እንደለ ፡ እንዲሁም ፡ ወልድ ፡ እንዲሁም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፡፡

አብ ፡ አልተፈጠረም ፡ ወልድም ፡ አልተፈጠረም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አልተፈጠረም ፡፡

አብን ፡ አናስታውልም ፡ ወልድንም ፡ አናስታውልም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ አናስታውልም ፡፡

አብ ፡ የዘላለም ፡ ወልድም ፡ የዘላለም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ የዘላለም ፡ ነው ፡፡

ነገር ፡ ግን ፡ የዘላለም ፡ ያሉ ፡ ሦስት ፡ አይደሉም ፡ አንድ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡፡

እንዲሁም ፡ የማናስታውላቸው ፡ ሦስት ፡ አይደሉሞ ፡፡ ያልተፈጠሩም ፡ ሦስት ፡ አይደሉም ፡ ያልተፈጠረ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡ የማናስታውለውም ፡ አንድ ፡፡

እንዲሁም ፡ አብ ፡ ሁሉን ፡ቻይ ፡ ነው ፡፡ ወልድም ፡ ሁሉን ፡ ቻይ ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ሁሉን ፡ ቻይ ፡፡

ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ ቻዮች ፡ ሦስት ፡ አይደሉም ፡፡ ሁሉን ፡ ቻይ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡፡

እንዲሁም ፡ አብ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡፡ ወልድም ፡ አምላክ ፡ ነው ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አምላክ ፡ ነው ፡፡

እርሳቸው ፡ ግን ፡ ሦስት ፡ አማልክት ፡ አይደሉም ፡፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡፡

እንዲሁም ፡ አብ ፡ ጌታ ፡ ነው ፡፡ ወልድም ፡ ጌታ ፡፡ መንፈ

ስ ፡ ቅዱስም ፡ ጌታ ፡፡

ነገር ፡ ግን ፡ ሦስት ፡ ጌቶች ፡ አይደሉም ፡ አንድ ፡ ጌታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡፡

አካል ፡ ሁሉ ፡ ኢያንዳንዱ ፡ ለራሱ ፡ አምላክና ፡ ጌታ ፡ ነው ፡ በክርስቲያን ፡ እውነት ፡ ተንዛንዘን ፡ እንደምንለው ፡፡

እንደሁም ፡ ሦስት ፡ አማልክት ፡ ወይስ ፡ ሦስት ፡ ጌቶች ፡ አሉ ፡ ከማለት ፡ በከቶሊካዊት ፡ አምልኮት ፡ ተከልክለናልና ፡፡

አብ ፡ ከማንም ፡ አልተሰራም ፡፡ አልተፈጠረምም ፡፡ አልተወለደምም ፡፡

ወልድም ፡ ከአብ ፡ ብቻ ፡ አለ ፡፡ ተሰርቶ ፡ አይደለም ፡ ተፈጥሮም ፡ አይደለም ፡ ተወልደ ፡ እንጂ ፡፡

መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ከአብና ፡ ከወልድ ፡ አለ ፡፡ ተሰርቶ ፡ አይደለም ፡፡ ተፈጥሮም ፡ አይደለም ፡፡ ተወልደም ፡ አይደለም ፡፡ ይሠርጻል ፡ እንጂ ፡፡

እንኪያስ ፡ አንድ ፡ አብ ፡ አለ ፡ ሦስት ፡ አቦችም ፡ አይደሉም ፡፡ አንድ ፡ ወልድም ፡ ሦስት ፡ ወልዶችም ፡ አይደሉም ፡፡ አንድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ሦስት ፡ መናፍስት ፡ ቅዱሳንም ፡ አይደሉም ፡፡

በዚችም ፡ ሥላሴ ፡ የሚቀደደም ፡ የሚከታተልም ፡ የለም ፡፡ ከባልንጀራውም ፡ የሚበልጥ ፡ የሚያንስም ፡ የለም ፡፡

ሦስት ፡ አካላታቸው ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ያንድ ፡ ዘላለምና ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡፡ እርሱ ፡ በርሳቸውም ፡ የተካከሉ ፡ ናቸው ፡፡

እንኪያስ ፡ እንደ ፡ ተባለ ፡ በሥላሴ ፡ አንድነትን ፡ ባንድነትም ፡ ሥላሴን ፡ ያመልኩ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡፡

ይድንም ፡ ዘንድ ፡ የሚሻ ፡ ሁሉ ፡ እንደህ ፡ ያስብ ፡ በሥላሴ ፡፡

ደግሞም ፡ ለሰው ፡ ለዘላለም ፡ ደህንነቱ ፡ የጌታችንን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ትሥጉት ፡ እንደሚገባ ፡ ያምን ፡ ዘንድ ፡ ይፈለጋል ፡፡

አርቶደክሳዊት ፡ ሃይማኖት ፡ እንደህ ፡ ማመናችንና ፡ ማለታችን ፡ ናትና ፡፡ ጌታችን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡ ነው ፡፡



አምላክ ፡ ነው ፡ ከአብ ፡ ህላዌ ፡ ከዘላለም ፡ ተወልደ ፡፡ ሰውም ፡ ነው ፡ ከናቱ ፡ ህላዌ ፡ በዓለም ፡ ተወልደ ፡፡

ፍጹም ፡ አምላክ ፡ ፍጹም ፡ ሰውም ፡፡ በሰው ፡ ነፍስና ፡ በሰው ፡ ሥጋ ፡ ኑሮ ፡፡

በመለኮቱም ፡ ከአብ ፡ ጋራ ፡ እኩል ፡ ሁኖ ፡፡ በሰውነቱም ፡ ከአብ ፡ አንሶ ፡፡

ደሮ ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡ መሆኑ ፡ ሳይቀር ፡ እርሱ ፡ ሁለት ፡ አይደለም ፡ አንድ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡፡

አንድ ፡ ነው ፡ መለኮት ፡ ወደ ፡ ሥጋ ፡ እንደ ፡ ተለወጠች ፡ አይደለም ፡ ሰውነትን ፡ ወደ ፡ አምላክ ፡ በመቀበል ፡ እንጂ ፡፡

ፍጽሞ ፡ ተዋሐደ ፡፡ በባሕሪይ ፡ መደበለቅ ፡ አይደለም ፡ በአካል ፡ አንድነት ፡ እንጂ ፡፡

ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንደሌ ፡ እንደሁም ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ፡፡

እርሱም ፡ ለመድኃኒታችን ፡ መከራ ፡ ተቀበለ ፡፡ ወደ ፡ ሢኦልም ፡ ወረደ ፡፡ በሦስተኛም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ ተነሣ ፡፡

ወደ ፡ ሰማይም ፡ ወጣ ፡፡ ሁሉንም ፡ ወደ ፡ ሚችል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ተቀመጠ ፡፡ ከዚያም ፡ ይመለሳል ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ለመፍረድ ፡፡

እርሱም ፡ ሲመጣ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሥጋው ፡ ይነሣ ፡ ዘንድ ፡ ባደረገውም ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ ይቈጠርበት ፡ ዘንድ ፡ ጊዜ ፡ አለው ፡፡

በጎም ፡ ያደረጉ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ክፉም ፡ ያደረጉ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ እሳት ፡ ይገባሉ ፡፡

ከቶሊካዊት ፡ ሃይማኖት ፡ ይህች ፡ ናት ፡ ሰውም ፡ በጣም ፡ ባያምናት ፡ ይድን ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውም ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ፡ ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘለለም ፡ አሜን ፡፡

ሊጣኒያ ። የልመና ፡ ምሳሌ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
ስለ ፡ መሻታቸውም ፡ ሁሉ ፡ የሚጸለይ ።

---

እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባት ፡ ሆይ ። ማረን ። ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ወልድ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ወልድ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ ፡ ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ፡ ከአብና ፡ ከወልድ ፡ የምትወጣ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ፡ ከአብና ፡ ከወልድ ፡ የምትወጣ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

ቅዱስ ፡ ቡሩክም ፡ ምስጉንም ፡ ሥላሴ ፡ ሆይ ። ሶስት ፡ አካላት ፡ አንድ ፡ አምላክም ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

ቅዱስ ፡ ቡሩክም ፡ ምስጉንም ፡ ሥላሴ ፡ ሆይ ። ሶስት ፡ አካላት ፡ አንድ ፡ አምላክም ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

በደላችንን ፡ አታስብ ፡ አቤቱ ፡ ያባቶቻችንንም ፡ በደል ። ኃጢአታችንንም ፡ አትበቀል ። እዘንልን ፡ አቤቱ ። እጅግ ፡ በከበረ ፡ በደምህ ፡ ለተበዠሃት ፡ ሕዝብህ ፡ እዘን ። ለዘላለምም ፡ አትቈጣብን ።

እዘንልን ፡ አቤቱ ።

ከክፋት ፡ ከመጉደትም ፡ ሁሉ ። ከሰይጣንም ፡ ተንኰልና ፡ ከመፈተኑም ። ከቍጣህም ። ከዘላለምም ፡ ኵነኔ ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

ከልብ ፡ ዕውርነት ፡ ሁሉ ። ከትዕቢትም ። ክብርንም ፡ ከመመኘት ። ከግብዝነትም ። ከቅናትም ። ከጸላትነትም ፡ ከክፋትም ። ከፍቅርም ፡ መጉደል ፡ ሁሉ ።

አድነን ፡ አቤቱ ።



ከዝሙት ፡ ከሌላም ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ከሚያደርስ ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ። ከዓለምም ፡ ከሥጋችንም ፡ ከዲያብሎስም ፡ ማሳት ፡ ሁሉ ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

በመብረቅና ፡ በዓውሎ ፡ ከሚመጣ ፡ መጉደት ። ከቸነፈርም ። ከራብም ። ከሰልፍም ። ከመገደልም ፡ ሳንዘጋጅም ፡ በድንገት ፡ ከሚመጣብን ፡ ሞት ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

ከሁከት ፡ ሁሉ ። በበጎ ፡ ሥርዓትም ፡ ላይ ፡ በስውር ፡ ከሚደረግ ፡ መባበር ። ከሸፍጥም ፡ ሁሉ ። ካሰትም ፡ ትምህርት ። ከንፈቁም ። ከመለየትም ። ከልብም ፡ ድንዛዜ ። ቃልህንም ፡ ትእዛዛትህንም ፡ ከመናቅ ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

በተቀደሰ ፡ ሥጋ ፡ መልበስህ ። በተቀደሰችም ፡ ልደትህ ፡ በመገዘርህም ። በመጠመቅህም ። በመጾምህም ። በመፈተንህም ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

በመጋደልህ ። ደምም ፡ በመሰለ ፡ ወዝህ ። በመሰቀልህም ። በሕማማትህም ። በከበረ ፡ ሞትህም ። በመቀበርህም ። በተመሰገነችም ፡ ትንሣኤህ ። በዕርገትህም ። በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ መምጣት ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

በመከራችን ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ። በደኅንነታችንም ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ። በሞትም ፡ ሰዓት ። በፍርድም ፡ ቀን ።

አድነን ፡ አቤቱ ።

እኛ ፡ ኃጢአተኞች ፡ እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። እንድትወድም ፡ ቅድስትና ፡ ከቶሊካዊት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህን ፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ ትመራት ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ በውነተኛ ፡ ሃይማኖት ፡ በቅን ፡ ማምለክህም ፡ በሕይወትቀዋም ፡ ጽድቅ ፡ በቅድስናም ፡ ባርያህን ፡ ቢክቶርያ ፡ እመቤታችንና ፡ ንግሥታችንን ፡ ታቀናት ፡ ዘንድ ፡ ታጸናትም ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቃትም ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ልብዋን ፡ በሃይማኖትህ ፡ በፍርሃትህም ፡ በውድህም ፡ ትገዛ ፡ ዘንድ ፡ እርስዋ ፡ ሁለግዜ ፡ ባንተ ፡ እንድታምን ፡ ሁለግዜም ፡ ምስጋናህን ፡ ክብርህንም ፡ እንድትሻ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ትጠብቃት ፡ ዘንድ ፡፡ በጸላቶችዋም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ድል ፡ ትሰጣት ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ኢቴጌ ፡ አድለይድን ፡ ገዢ ፡ አልበርትንም ፡ የዌልስንም ፡ ገዢ ፡ ዖንግሥትንም ፡ ዘመዶች ፡ ሁሉ ፡ ትባርካቸው ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቃቸውም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ጳጳሳትን ፡ ቀሳውስትንም ፡ ዲያቆናትንም ፡ በቃልህ ፡ በውነተኛ ፡ ዕውቀቱ ፡ በማስተዋሉም ፡ ታበራቸው ፡ ዘንድ ፡፡ እርሳቸው ፡ በስብከታቸውና ፡ በሕይወታቸው ፡ ይገልጹት ፡ ዘንድ ፡ ያከብሩትም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ዖንግሥትን ፡ ሊቃውንትና ፡ አካበሮችን ፡ ሁሉ ፡ ጸጋውን ፡ ጥበብንም ፡ ማስተዋልንም ፡ ታለብሳቸው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኖ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ሹማምትን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቅም ፡ ዘንድ ፡፡ ቅንን ፡ ሊሰሩ ፡፡ እውነትንም ፡ ሊጠብቁ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ሕዝብህን ፡ ሁሉን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቅም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ላሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አንድነትን ፡ ዕርቅንም ፡ ፍቅርንም ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ የውድህን ፡ የፍርሃትህንም ፡ ልብ ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡፡ በኃይላችንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ትእዛዛትህ ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡



እንድትወድ ፡ ለሕዝብህ ፡ ሁሉ ፡ የጸጋህን ፡ መጨመርያ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ቃልህን ፡ በየውሃት ፡ እንዲሰሙ ፡፡ በንጹሕ ፡ ፍቅርም ፡ እንዲቀበሉት ፡፡ የመንፈስንም ፡ ፍሬ ፡ እንዲያፈሩ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ የሳቱትን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እውነት ፡ መንገድ ፡ ትመልሳቸው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ የሚቆሙትን ፡ ታበርታቸው ፡ ዘንድ ፡፡ በልባቸውም ፡ የደከሙትን ፡ ታጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ ትረዳቸውም ፡ ዘንድ ፡፡ የሚወድቁትንም ፡ ታስነሣቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ሰይጣንንም ፡ በመጨረሻ ፡ ከግራችን ፡ በታች ፡ ትቀጠቅጠው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንደትወድ ፡ በፈተና ፡ በድኅትም ፡ በመከራም ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ ትረዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ታጸናቸውም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ በምድር ፡ ወደስ ፡ በባሕር ፡ የሚሔዱትን ፡ ሁሉ ፡ የጸነሱትንም ፡ ሴቶች ፡፡ የታመሙትንመ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡፡ ታናሾችንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡፡ በግዞትም ፡ የሚቀመጡትን ፡ ሁሉ ፡ ትምራቸው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የሌላቸውን ፡ ልጆት ፡፡ ባልቴቶችንም ፡ ባሕታውያንንም ፡ ነዳያንንም ፡ ትጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ ትመግባቸውም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ሰውን ፡ ሁሉን ፡ ትምረው ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ለጸላቶቻችን ፡ ላሳደጆቻችንም ፡ ለሰደቦቻችንም ፡ ትሰርደላቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ልባቸውንም ፡ ትመልስ ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ የምድርን ፡ ፍሬ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡፡ ለመቀ

በላችንም ፡ ትጠብቀው ፡ ዘንድ ፡፡ በየጊዜው ፡ እስክንበላው ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ እውነተኛ ፡ ንስሓ ፡ መግባትን ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡፡ ኃጢአታችንንም ፡ ሀኬታችንንም ፡ አለማወቃችንንም ፡ ታስቀርልን ፡ ዘንድ ፡፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስህንም ፡ ጸጋ ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ሕይወታችንን ፡ እንደ ፡ ቅዱስ ፡ ቃልህ ፡ እንድንለውጥ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡፡ እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ በግ ፡ ሆይ ፡ ያለምን ፡ ኃጢአት ፡ ያስወገድሀው ፡፡

ሰላምህን ፡ ስጠን ፡፡

የእግዚአብሔር ፡ በግ ፡ ሆይ ፡ ያለምን ፡ ኃጢአት ፡ ያስወገድሀው ፡፡

ማረን ፡፡

ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ስማን ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ስማን ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረን ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረን ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡
አቤቱ ፡ ማረን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁላቸው ፡ የጌታችንን ፡ ጸሎት ፡ ባንድ ፡ ይጸልዩ ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችንን ፡ የሚበቃንን ፡ ስጠን ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅር ፡ በለን ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ልኛ ፡ የለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ፡ አሜን ፡፡



ቄስ ፡፡ እንደ ፡ ኃጢአታችን ፡ በኛ ፡ አትስራ ፡ አቤቱ ፡፡
ም ፡፡ እንደ ፡ በደላችንም ፡ አትክፈልልን ፡፡

እንጸልይ ፡፡

እግዚአብሔር ፡ መሐሪ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ የተደቈሰውን ፡ ልብ ፡ ልመና ፡ የሚያዝኑትንም ፡ መሻት ፡ አትንቅምና ፡፡ በመከራችንና ፡ በጭንቀታችን ፡ ጊዜ ፡ በፊትህ ፡ በምናደርገው ፡ በጸሎታችን ፡ እርደን ፡፡ በጸጋም ፡ ስማን ፡፡ የሰይጣን ፡ ወይስ ፡ የሰው ፡ ብልሐትና ፡ ተንኰል ፡ የሚሰራብን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይሻር ፡ ዘንድ ፡፡ በቸርነትህም ፡ መጠበቅ ፡ ይበተን ፡ ዘንድ ፡፡ እኛም ፡ ባሮችህ ፡ መሰደድ ፡ ሳይጐዳን ፡ በቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ እናመሰግንህ ፡ ዘንድ ፡ ሁለግዜ ፡፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡

ም ፡፡ አቤቱ ፡ ተነሣ ፡ እርደነም ፡ አድነንም ፡ ስለ ፡ ስምህ ፡ መክንያት ፡፡
ቄ ፡፡ አቤቱ ፡ በጆሮቻችን ፡ ሰማን ፡፡ አባቶቻችንም ፡ ነገሩን ፡፡ በዘመናቸው ፡ በድሮ ፡ ዘመንም ፡ የሰራሀውን ፡ የከበረውንም ፡ ስራ ፡፡
ም ፡፡ አቤቱ ፡ ተነሣ ፡ እርደነም ፡፡ ስለ ፡ ክብርህም ፡ አድነን ፡፡
ቄ ፡፡ መስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
ም ፡፡ በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡
ቄ ፡፡ ከጸላቶቻችን ፡ አድነን ፡ ክርስቶስ ፡፡
ም ፡፡ በጸጋ ፡ ወደ ፡ መከራችን ፡ ተመልከት ፡፡
ቄ ፡፡ በርኅራኄ ፡ የልባችንን ፡ አሳብ ፡ እይ ፡፡
ም ፡፡ የሕዝብህን ፡ ኃጢአት ፡ በምሕረትህ ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፡፡
ቄ ፡፡ በፍቅር ፡ በምህረትም ፡ ጸሎታችንን ፡ ስማ ፡፡
ም ፡፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ ማረን ፡፡
ቄስ ፡፡ አሁንና ፡ ወትሮ ፡ ፍቀድ ፡ ትሰማን ፡ ዘንድ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡፡
ም ፡፡ በጸጋ ፡ ስማን ፡ ክርስቶስ ፡፡ በጸጋ ፡ ስማን ፡ ጌታ ፡ ክርስቶስ ፡፡

ቁስ ። አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ ትገለጽልን ።
ም ። ባንተ ፡ እንደ ፡ አመነ ።

ቁ ። እንጸልይ ።

በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ በምሕረት ፡ ወደ ፡ ድካማችን ፡ እንድታይ ። ስለ ፡ ስምህም ፡ ምስጋና ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ በቅን ፡ የሚገባነውን ፡ ከኛ ፡ አርቀው ። ጸጋም ፡ ስጠን ፡ በመከራችን ፡ ሁሉ ፡ ማመናችንን ፡ ተስፋችንንም ፡ ሁሉ ፡ ምሕረትህን ፡ እናደርግ ፡ ዘንድ ። ሁለግዜም ፡ እንገዛልህ ፡ ዘንድ ፡ በቅድስና ፡ በሕይወትም ፡ ንጽሕና ፡ ለክብርህ ፡ ለምስጋናህም ። ባንድ ፡ መኻከለኛችን ፡ በጰራቅሊጦሳችንም ። በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የአፈ ፡ ወርቅ ፡ ጸሎት ። ስለ ፡ ተሰበሰበች ፡ ጉባኤ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ልመናችንን ፡ ወደንተ ፡ እንደደረግን ፡ ጸጋህን ፡ ሰጥተህናልና ፡ ሁሉት ፡ ወይስ ፡ ሶስትም ፡ በስምህ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ልመናቸውን ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስደርገህልናልና ። የባሮችህን ፡ መሻትና ፡ ልመና ፡ አሁን ፡ ፈጽም ፡ በጅ ፡ እንደሚሻላቸው ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ የውነትህን ፡ ዕውቀት ፡ በመጣውም ፡ ዓለም ፡ የዘለለሙን ፡ ሕይወት ፡ ስትሰጠን ። አሜን ።

የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ። የእግዚአብሔርም ፡ ፍቅር ። የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አንድነት ። ከሁላችን ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

---

ልመና ፡ ምስጋናም ፡ ስለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መክንያት ።

ልመና ።

ስለ ፡ ዝናም ፡ በድርቅ ፡ ዘመን ።

እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ። መንግሥትህንና ፡ ጽድቅዋን ፡ ለሚሹ ፡ ሁሉ ፡ ለሥጋቸው ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ትጨምርላቸው ፡ ዘንድ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ተስፋ ፡ አስደርገህላቸዋልና ። በዚህ ፡ መከራችን ፡ እንለምንሃለን ፡ የምድርን ፡ ፍሬ ፡ ለማውጣት ፡ የሚጠቅመውን ፡ ዝናም ፡ ታዘንምልን ፡ ዘንድ ፡ ለመጽናናታችንና ፡ ለምስጋናህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።



ስለ ፡ ጸሐይ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ በኖህ ፡ ዘመን ፡ በሰው ፡ ኃጢአት ፡ መክንያት ፡ ዓለምን ፡ ሁሉን ፡ ከስምንት ፡ ነፍስ ፡ በቀር ፡ አሠጠምሀው ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ደግሞ ፡ እንዲህ ፡ አድርገህ ፡ ከቶ ፡ እንዳታጠፋው ፡ በታላቅ ፡ ምህረትህ ፡ ተስፋ ፡ አስደረግህ ። እኛ ፡ በውነት ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችን ፡ የዝናምና ፡ የውኃ ፡ መቅሠፍት ፡ ይገባናል ። ደሮ ፡ ንስሐ ፡ ገብተን ፡ የምድርን ፡ ፍሬ ፡ በጊዜ ፡ ለመልቀም ፡ የሚጠቅመውን ፡ ጸሐይ ፡ እንድትሰድ ፡ በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ እኛ ፡ በመቅሠፍትህ ፡ ተምረን ፡ ሕይወታችንን ፡ እንለውጥ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምህረትህም ፡ እናመሰግንህ ፡ ዘንድ ፡ እናከብርህም ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

በራብ ፡ ዘመን ።

አቤቱ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ። የዝናም ፡ መውረድ ፡ የምድርም ፡ ፍሬ ፡ ማፍራት ፡ የእንስሳም ፡ መብዛት ፡ ሀብትህ ፡ ነውና ። እኛ ፡ የሕዝብህን ፡ መከራ ፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ በኃጢአታችን ፡ መክንያትም ፡ የሚገባነውን ፡ ራብ ፡ አንተ ፡ በቸርነትህ ፡ ምረህን ፡ ለምላትና ፡ ለጽጋብ ፡ ትለውጠው ፡ ዘንድ ፡ እንለምንሃለን ። ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ጌታችን ፡ ፍቅር ። ለርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ ይሁን ፡ አሁንና ፡ ለዘወትር ። አሜን ።

ወይስ ፡ ይች ፡ ልመና ።

አቤቱ ፡ የምህረት ፡ አባታችን ፡ ሆይ ። አንተ ፡ በኤልሣ ፡ በነቢይ ፡ ዘመን ፡ በሰማርያ ፡ ታላቅ ፡ ራብን ፡ በድንገት ፡ ለምላት

ና : ለጽጋብ : እንደ : ለወጥህ : እንደሁም : እኛ : ዛሬ : በኃጢአና : ማታችን : መክንያት : እንደዚያ : ያለውን : መቅሠፍትና : መከራ : ያገኘነ : በጅ : የሚለውን : ረዲት : ትሰደን : ዘንድ : እንለምንሃለን :: ማረነ : አቤቱ :: በሰማያዊትም : በረከትህ : የምድርን : ፍሬ : አብዛ :: እኛም : የቸርነትህን : ስጥወታ : ተቀብለን : ላንተ : ምስጋና : ለነዲያንም : ረዲት : ለኛም : ደስታ : እንረባው : ዘንድ : ልባችነን : አቅና : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

## በጾርና : በሁከት : ጊዜ ::

ሁሉን : ቻይ : አምላክ : ሆይ : የነገሥታት : ሁሉ : ንጉሥ : የዓለምም : ሁሉ : ገዢ :: ኃይልህን : ለመቃወም : ፍጥረት : ሁሉ : አይችልም :: ኃጥአንን : በቅን : መግሠጽ : በውነትም : ንስሐ : ለሚገቡት : መማር : ላንተ : ነውና :: ከጸላቶቻችን : እጅ : እንድትጠብቀን : እንድትረዳንም : በትሕትና : እንለምንሃለን :: ትዕቢታቸውን : አዋርድ :: ክፋታቸውንም : ጸጥ : አሰኝ : ተንኰላቸውንም : ገልብጥ : እኛ : በመጠበቅህ : ጸንተን : ሁልግዜ : ፍርሃት : ሁሉ : እንዳይደርስብን : አንተን : እናመሰግን : ዘንድ : አንተ : ብቻ : ድል : የምታሰነሣ : ባንድ : ልጅህ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን : ምግባር :: አሜን ::

## ባገር : በሽታ : ጊዜ ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ :: ሕዝብህ : በምድረ : በዳ : በሙሴና : በሐሮን : ላይ : በተነሡ : ጊዜ : አንተ : ተቈጥተህ : በሽታውን : ሰደድህባቸው :: በዳዊትም : በንጉሥ : ዘመን : በቸነፈር : ሰባት : እልፍ : ሰዎችን : ገደልህ : ምህረትህንም : አስበሃልና : የቀሩትን : አዳንህ :: ለኛም : ለኃጢአተኞች : አሁን : እጅግ : በሽታና : ሞት : ላገኘነ : እ ዘንልን :: የዚያን : ጊዜም : ቤዛውን : ተቀብለህ : አጥፊዩን : መልአክ : መቅሠፍቱን : እንደስተወህ : እንደሁም : አሁን : ይህች : በሽታና : ክፉ : ሕማም : ከኛ : ታርቃት : ዘንድ : ውደድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::



## በመቅሰስ : ጊዜ : ስለ : ሚቀሰሱ : ሰዎች ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሰማያዊ : አባታችን : ሆይ :: አንተ : በተወደደ : ልጅህ : በከበረ : ደሙ : ለራስህ : ከቶሊካዊት : ቤተ : ክርስቲያንን : ተበጅተሃልና :: በምህረትህ : ተመልከታት :: በዚህ : ወራትም : የባሮችህን : ለመንጋህ : ኤጲስቆጶሳትና : ጠባቆች : ያሉትን : ልባቸውን : እንደህ : መርተህ : አቅናቸው : እጃቸውን : ከቶ : በማንም : ላይ : በድንገት : እንዳይጭኑ : በምነትና : በጥበብ : ደህና : ሰዎችን : እንዲመርጹ : እንጅ : በተቀደሰች : በቤተ : ክርስቲያንህ : መልእክት : ያገለግሉህ : ዘንድ :: ለተቀደሰችም : ሹመት : ሁሉ : ለሚቀሰሱ : ጸጋህንና : ሰማያዊት : በረከትህን : ስጣቸው : እርሳቸው : ፀሕይወታቸውና : በትምህርታቸው : ክብርህን : ይገልጹ : ዘንድ : የሰውንም : ሁሉ : መድኃኒት : ያስታውቁ : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

## ወይስ : ይህች : ልመና ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ : የበጎ : ስጥወታ : ሁሉ : ሰጭ :: አንተ : ባምላካዊት : ምክርህ : ለቤተ : ክርስቲያንህ : ልዩ : ልዩን : መልእክት : አደርገሃልና :: በርስዋ : ለሹመትና : ለማገልገል : ሁሉ : ለሚጸሩ : ጸጋህን : እንድትሰጣቸው : በትሕትና : እንለምንሃለን : እርሳቸውም : በፊትህ : ታምነው : እንዲያገለግሉህ : በትምህርትህ : እውነት : ምላቸው : የሕይወትንም : ንጽሕና : አልበሳቸው : ለታላቅ : ስምህ : ለምስጋና : ለቅድስት : ቤተ : ክርስቲያንህም : ለጥቃሚ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

## ይህችም : ልመና : ከቀደሙት : በኋላ : ትከተል ::

አቤቱ : ወትሮ : መማርና : ይቅር : ማለት : ጠባይህና : ገንዘብህ : ነውና : በትሕትና : ያደረግናትን : ልመናችነን : ተቀበል :: እኛም : እንኳ : በኃጢአታችን : ሰንሰለት : ከታሠርን : የታላቅ : ምህረትህ : ርህራኄ : ትፈታን :: ስለ : የሱስ : ክርስቶስ : ስለ : መኻከለኛችንና : ጰራቅሊጦሳችን : ስለ : ክብሩ :: አሜን ::

የጸርለመንት : ሸንጎ : በተሰበሰበች : ጊዜ : ደህች : ልመና : ትለመንላት ::

በሁሉ : መሓሪ : አምላክ : ሆይ : ለዚች : መንግሥት : እንደ ያው : ይልቁንም : እጅግ : ከምትፈራህ : ከቸርም : ንግሥታችን : በታች : በዚህ : ወሬት : ለተሰበሰበች : ለጸርለመንት : ሸንጎ : በትሕትና : እንለምንሃለን : እንድትወድ : ምክሬቸውን : ሁሉ : ታቀናላቸው : ዘንድ : ለምስጋናህም : መዝረጋት : ለቤተ : ክርስቲያንህም : በጐነት : ለንግሥታችንና : ለግዛትዋም : እረፍት : ክብርም : ደህንነትም : ታበጅላቸው : ዘንድ :[በድካማቸው : ነገር : ሁሉ : እንዲህ : በደህናና : በምነት : መሰረት : እንዲሠራ : እንዲቆምም : ዕርቅና : ደህንነት : እውነትና : ቅንም : ደህና : አምልኮና : ፍርሃትህም : በመኻከላችን : እስኪጸና : ለትውልድ : ሁሉ :: ይህንና : የቀረውን : መሻት : ሁሉ : ለርሳቸው : ለኛም : ለቤተ : ክርስቲያንህም : ሁሉ : በትሕትና : እንለምናለን : ከሁሉ : በተባረከ : ጌታችንና : መድኃኒታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ስምና : በመኻከለኝነቱ :: አሜን ::

ስለ : ሰው : ንብረት : ሁሉ : ልመና : ሊጣኒያ : ባይደገም : ለመንበብ ::

አቤቱ : የሰው : ሁሉ : ፈጣሪና : ጠባቂ : ሆይ :: ለሰው : ሁሉ : አይነትና : ንብረት : በትሕትና : እንለምንሃለን : በመንገድህ : ታስታውቃቸው : ዘንድ : የሚያድነውንም : ደህንነትህ : ባሕዛብ : ሁሉ : መኻከል : ትገልጽ : ዘንድ : እንድትወድ :: ከሌላ : ነገርም : ይልቅ : ለከቶሊካዊት : ቤተ : ክርስቲያን : ለደህንነትዋ : እንለምንሃለን : እርስዋ : በበጎ : መንፈስ : እንደህ : ትመሬና : ትገዛ : ዘንድ : ክርስቲያን : የተባሉ : ሰዎች : ሁሉ : ወደ : እውነት : መንገድ : ተመርተው : እንደገቡ : ሃይማኖትንም : በመንፈስ : አንድነት : በሰላምም : ማሠርያ : በሕይወትም : ጽድቅ : እንዲጠብቁ :: ደግሞም : አባታችን : ሆይ : በነፍሳቸው : ወይስ : በሥጋቸው : ወይስ : በግዛታቸው : ባንዳች : መከራ : የተቀበሉትን : የሚጨነቁት



ንም : ለቸርነትህ : አደራ : እናሰጣቸዋለን : [* ከሌሎች : ይልቅ : ጸሎታችንን : የፈለጉትን : ሰዎች : (የፈለገውን : ሰው :) (የፈለገችን : ሴት)] እንደ : ልዩ : ልዩ : ጉዳያቸው : ታጸናቸው : ዘንድ : ታቀላቸውም : ዘንድ : እንድትወድ : ትዕግሥትን : በመከራቸው : ደህና : ጭራሸንም : ከጭንቀታቸው : ሁሉ : ሰጥተሃቸው :: ይህንንም : ነገር : ስለ : የሱስ : ክርስቶስ : መኽንያት : እንለምናለን :: አሜን ::

* ሰው : የጉባኤን : ለመና : ሲሻ : ጊዜ : ይህ : ይደገማል ::

ምስጋና ::

ለጉባኤና : ለሰው : ሁሉ ::

ሁሉን : የምትችል : እግዚአብሔር : የምህረት : ሁሉ : አባት : ሆይ :: እኛ : ክብር : የሌለን : ባሮችህ : ለኛና : ለሰው : ሁሉ : ስለ : አደረግህው : ስለ : ቸርነትህና : ስለ : ፍቅርህ : ሁሉ : በትሕትና : ከልባችንም : እናመሰግንሃለን : [* ከሌላ : ይልቅም : በዚህ : ወሬት : ስለ : አሳየሃቸው : — አሳየሀው : — አሳየሃት : — ስለ : በጐነትህ : ያመሰግኑህ : — ያመሰግንህ : — ታመሰግንህ : — ዘንድ : ለሚወዱ : ሰዎች : — ለሚወድ : ሰው : — ለምትወድ : ሴት : — እናመሰግንሃለን :] : ስለ : ፍጥረታችን : ስለ : መጠበቃችንም : ወደዚህ : ዓለም : ስለሚደርስም : በረከትህ : ሁሉ : እንባርክሃለን :: ከሁሉ : ይልቅ : ግን : በዓለም : መድኃኒት : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ስለ : ገለጽሀው : አሳብንም : ሁሉን : ስለሚወጣው : ፍቅርህ : ስለ : ጸጋህም : መቀበያ : ስለ : ዘላለምም : ክብር : ተስፋ :: ደግሞም : የሚገባውን : የምህረትህን : ሁሉ : ዕውቀት : እንድትሰጠነ : እንለምንሃለን : ልባችን : ያለ : ግብዝነት :

* በቀደም : የጉባኤን : ልመና : ሽቶ : የነበረ : አሁን : በግልጽ : ያመሰግን : ዘንድ : ቢሻ : ቄስ : ይህነን : ይበል ::

ያመሰግንህ ፡ ዘንድ ፡ እኛም ፡ ባፋችን ፡ ብቻ ፡ ምስጋናህን ፡ አንደንገልጽ ፡ በሕይወታችንም ፡ እንጂ ፡ ነፍሳችንን ፡ ለማገልገልህ ፡ አቅርበን ፡ በፊትህም ፡ ዕድሜያችንን ፡ ሁሉ ፡ በቅድስና ፡ በጽድቅም ፡ ተመላልሰን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ ለርሱም ፡ ካንተና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ዝናም ፡፡

አቤቱ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በምህረትህ ፡ ምክር ፡ መጀመርያውንና ፡ ኋለኛውን ፡ ዝናም ፡ ለሰው ፡ የሚጠቅመውን ፡ ፍሬ ፡ ያስወጣ ፡ ዘንድ ፡ ለምድር ፡ አዘንመሃልና ፡ እኛ ፡ በትሕትና ፡ እናመሰግንሃለን ፡፡ በብርቱ ፡ ጭንቀታችን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ዝናም ፡ በርስትህ ፡ ላይ ፡ አዘንመህልናልና ፡ በደረቀም ፡ ጊዜ ፡ አጥጠህዋልና ፡ ለተዋረድና ፡ ለባሮችህ ፡ ለታላቅ ፡ መጽናታችን ፡ ለቅዱስ ፡ ስምህም ፡ ምስጋና ፡ ስለ ፡ ምህረትህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ጸሓይ ፡፡

እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በቅን ፡ መቅሠፍትህ ፡ በጅግ ፡ ጉርፍና ፡ ውኃ ፡ ካዋረድህነ ፡ በኋላ ፡ በምህረትህ ፡ በደህና ፡ ጊዜ ፡ በሆነ ፡ ጸሓይ ፡ ነፍሳችንን ፡ አቀለሃልና ፡ አጸንተሀንማልና ፡ ስለዚች ፡ ምህረትህ ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናመሰግናለንና ፡ እናከብራለን ፡ ወትሮም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ቸርነትህን ፡ እንገልጻለን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ስለ ፡ ጽጋብ ፡፡

በሁሉ ፡ ላይ ፡ መሓሪ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ በፍርሃትህ ፡ የለመነችውን ፡ ልመና ፡ አንተ ፡ በታላቅ ፡ ቸርነትህ ፡ ሰምተህ ፡ መሻታችንንና ፡ ራባችንን ፡ ለምላትና ፡ ለጽጋብ ፡ ለውጠሃልና ፡ በትሕትና ፡ ስለዚህች ፡ ታላቅ ፡ በጐነትህ ፡ እናመሰግንሃለን ፡ ደግሞም ፡ ምድራችን ፡ ፍሬዋን ፡ ታወጣልን ፡ ዘንድ ፡ ቸርነትህን ፡ እንድታኖርልን ፡ እንለምንሃለን ፡ ለምስጋናህና ፡ ለደስታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡



ስለ ፡ ዕርቅ ፡ ከጸላቶቻችን ፡ እጅም ፡ ስለ ፡ መርደት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ባሮችህን ፡ ከጸላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ ለመጠበቅ ፡ ብርቱ ፡ አምባ ፡ የሆንህላቸው ፡ በዙርያ ፡ ሁሉ ፡ ከከበበነ ፡ ከታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ ሁሉ ፡ አድነህናልና ፡ እናመሰግንሃለን ፡ እናከብርህማለን ፡ ለጸላቶቻችን ፡ ምርኮ ፡ እንደልተሰጠነ ፡ ቸርነትህ ፡ ብቻ ፡ እንደሆን ፡ እናስታውቃለን ፡፡ ይህችንም ፡ ምህረትህ ፡ እንድታኖርልን ፡ እንለምነሃለን ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ማደናችንና ፡ ብርቱ ፡ ረጃችን ፡ እንደለህ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ካገር ፡ ሁከት ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ ተመለሰች ፡ ዕርቅ ፡፡

አንተ ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የሰማዩ ፡ አባታችን በቤት ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ላንድ ፡ ልብ ፡ ማስማማት ፡ ያመጸኛውንና ፡ ለሁከት ፡ የዘነበለውን ፡ ሕዝብ ፡ ቍጣውን ፡ ማስረጋት ፡ ያንተ ፡ ስራ ፡ ነው ፡፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ በመኻከላችን ፡ የተነሣቸውን ፡ ሁከትና ፡ ሸፍጥ ፡ ታረጋት ፡ ዘንድ ፡ ወደሃልና ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እንባርካለን ፡፡ ጸጋህንም ፡ ለሁላችን ፡ በትሕትና ፡ እንለምናለን ፡ እንጊዴህ ፡ ለተቀደሱ ፡ ትእዛዛትህ ፡ ታዝዘን ፡ እንመላለስ ፡ ዘንድ ፡ ባምልኮም ፡ ሁሉ ፡ በውነትም ፡ በጭምትም ፡ በርቅም ፡ ሕይወት ፡ ኑረን ፡ እንደህም ፡ ስለ ፡ ገለጽህብን ፡ ስለዚች ፡ ምህረትህ ፡ የምስጋናውንና ፡ የክብርን ፡ ምሥዋዕታችን ፡ አዘውትረን ፡ እናቀርብልህ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ከቸነፈርና ፡ ከሌላ ፡ ካገር ፡ በሽታ ፡ ስለ ፡ ማደን ፡፡

እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በዚች ፡ ወራት ፡ ባደረግህ ፡ በብርቱና ፡ በሚያስፈራ ፡ መጕበኘትህ ፡ ስለ ፡ መተላለፋችን ፡ አቍሰልህነ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችንም ፡ ፈጅህነ ፡ ደሮ ፡ በፍርድህ ፡ መኻከል ፡ ምህረትህን ፡ አስበህ ፡ ነፍሳችንን ፡ ከሞት ፡ መንጋጋ ፡ ዘንድ ፡ አደንህ ፡፡ ስለዚህም ፡ ላባታዊት ፡ ቸርነት ፡ አንተ ፡ ያደንሃቸውን ፡ ነፍሳችንንና ፡ ሥጋችነ

ን : እናቀርብልሃለን : ሕያው : ምሥዋዕት : ይሆኑልህ : ዘን
ድ :: ምህረትህንም : ለዘወትር : በቤተ : ክርስቲያንህ : መ
ካከል : እናመሰግናለንና : እናበልጣለን : በየሱስ : ክርስ
ቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

ወይስ : ይህ ::

እኛ : በፊትህ : በሁሉ : መሓሪ : አባታችን : ሆይ : በሕግ :
የተቃየምህው : መቅሠፍት : ሁሉ : በወደቀብን : በኃጢአ
ታችን : ብዛትና : በልባችን : ድንዛዜ : መክንያት : ቢገባን :
እንደ : ነበረ : በትሕትና : እናስታውቃለን :: አንተ : ግን : ከ
ምህረትህ : ርኅራኄ : የተነሣ : እኛ : በድካምና : በፍረት :
በተዋረድን : ጊዜ : ያሳዘነነውን : በሽታ : አስቀርተሃልና : የ
ደስታውንና : የጤናውንም : ድምጽ : ለመኖርያችን : መል
ሰሃልና : እኛ : ላምላካዊት : ልዕልናህ : የምስጋናንና : የክ
ብርን : ምሥዋዕት : እናቀርብልሃለን : አንተም : ስለ : ጠ
በቅህነ : የከበረውን : ስምህ : እናመሰግናለንና : እናከብረ
ዋልን : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

---

ጸሎት : የሐዋርያት : መልእክትም : የወንጌልም :
ክፍል : በየእሁድና : በየበዓል : ሁሉ : ባመት :
ሁሉ : ለማንበብ ::

የክርስቶስ : መምጣት : መጀመርያ : እሁድ ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ : አሁን : በዚህ : በ
ሚያልፍ : ልጅህ : የሱስ : ክርስቶስ : በጅግ : መዋረድ : ይ
ጐብኘን : ዘንድ : የመጣበት : ዘመን : የጨለማውን : ስ
ራ : ጥለን : የብርሃንን : እቃ : ጦር : እንለብስ : ዘንድ : ጸ
ጋህን : ስጠነ :: በኋለኛው : ቀን : እርሱ : በሕያዋንና : በሙ
ታን : ለመፍረድ : በከበረች : ግርማው : ሲመለስ : ጊዜ : እ
ኛ : ለማያልፍ : ሕይወት : እንነሣ : ዘንድ : በርሱ : ካንተ
ና : ከመንፈስ : ቅዱስ : ጋራ : በሚኖርና : በሚገዛ : ዛሬና :
ለዘላለም :: አሜን ::

¶ ይህችም : ጸሎት : ዕለት : ዕለት : ትደገማለች : እ
ስከ : ልደት : ማታ : ድረስ ::

የመልእክት : ክፍል :: ሮሜ : ፲፫፡ ፰::

ለማንም : ሌላ : ዕዳ : አይሁንባችሁ : እርሱ : በርሳ
ችሁ : ከመዋደድ : በቀር :: ባልንጀራውን : የሚወድ : ሕግ
ን : ፈጽሞታልና :: ይኸም : የተባለው :: አታመንዝር :: አ
ትግደል :: አትስረቅ :: ባሰት : አትመስክር :: አትመኝ ::
ሌላ : ትእዛዝም : እንደለ : ፍጻሜው : በዚኽ : ነገር : ነው ::
ባልንጀራኽን : ውደድ : እንደ : ራስኽ :: ፍቅር : በባልንጀራ :
ላይ : ክፉ : አይሰራም :: ስለዚኽም : የሕግ : ፍጻሜ : ፍ
ቅር : ነው :: ደህ : ነገርም :: ዘመን : አውቀን : ከምኝታችን :
የምንነሣበት : ጊዜ : እንደ : ደረሰ :: ዛሬ : መድኃኒት : ወ

ደኛ ፡ የቀረበ ፡ ነውና ፡ ካመነበት ፡ ጊዜ ፡ ይልቅ ። ሌሊቱም ፡ ሔደ ፡ ቀኑም ፡ ቀርበ ። ስለዚኽ ፡ የጨለማውን ፡ ስራ ፡ ከኛ ፡ ዘንድ ፡ እናውልቅ ። የብርሃንም ፡ ጋሻ ፡ ጦር ፡ እንልበስ ። በቀን ፡ እንመላለስ ፡ እንደ ፡ በቀን ። በዘፈንና ፡ በስካርም ፡ አይደለም ። በዝሙትም ፡ አይደለም ፡ በርኵሰትም ፡ በሐሜትም ፡ በቅንዓትም ። ጌታን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ልበሱት ፡ እንጂ ። ሥጋውንም ፡ ለፍትወት ፡ አትደግፉ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፳፩፡ ፩፡—፲፫።

ወደ ፡ የሩሳሌምም ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ፋጌ ፡ ቤትም ፡ በመጹ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ አጠገብ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሱስ ፡ ሁለት ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ላከ ፡ እንዲህ ፡ ሲላቸው ። በፊታችሁ ፡ ወዳለችው ፡ አገር ፡ ሒዱ ፡ የታሠረችንም ፡ አህያ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ታገኛላችሁ ፡ ግልገልዋንም ፡ ከርስዋ ፡ ጋራ ። ፈትዋቸው ፡ እርሳቸውንም ፡ አምጹልኝ ። ማንምም ፡ አንዳች ፡ ቢላችሁ ፡ ጌታ ፡ ይሻቸዋል ፡ በሉ ። እርሱም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይሰዳቸዋል ። ይኽም ፡ ሁሉ ፡ የሆነ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ በነቢይ ፡ የተባለው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ለፅዮን ፡ ልጅ ፡ በልዋት ። እነሆ ፡ ንጉሥሽ ፡ ወዳንች ፡ ይመጻል ። ገር ፡ ሁኖ ። ባህያ ፡ ላይም ፡ ተቀምጦ ፡ በግልገልም ፡ ባህያዪቱ ፡ ልጅ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሒደው ፡ የሱስ ፡ እንደዘዛቸው ፡ አደረጉ ። አህያዪቱንና ፡ ግልገልዋንም ፡ አመጹ ። ልብሳቸውንም ፡ በላያቸው ፡ አነጸፉ ፡ በላያቸውም ፡ አስቀመጡት ። እጅግ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ልብሳቸውን ፡ በመንገድ ፡ አነጸፉ ። ሌሎችም ፡ ከዛፍ ፡ ጫፍ ፡ ጫፏን ፡ ቍርጠው ፡ ያነጸፉ ፡ ነበረ ። በፊቱም ፡ የሔዱ ፡ ሰዎች ፡ የተከተሉትም ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ሆሳዕና ፡ ለዳዊት ፡ ልጅ ። በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚመጻ ፡ የተባረከ ፡ ነው ። ሆሳዕና ፡ በአርያም ። የሱስም ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ አገሪቱ ፡ ሁልዋ ፡ ታወከች ፡ ስትል ። ይኽ ፡ ማነው ። ሕዝብም ፡ አሉ ። ይኽ ፡ ነቢዩ ፡ የሱስ ፡ ነው ፡ የናዝሬቱ ፡ የገሊላ ፡ አገር ፡ ያለች ። የሱስም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ገባ ፡ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ የ



ሚሸጡን ፡ የሚገዙንም ፡ ሁሉ ፡ አወፃ ። የሰራፎችንም ፡ ማዕድ ፡ የርግብ ፡ ሻጮችንም ፡ ወንበር ፡ ገለበጠ ። አላቸውም ። የተጻፈ ፡ ነው ፡ ቤቴ ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ይባላል ። እላንተ ፡ ግን ፡ የሌቦችን ፡ ዋሻ ፡ አደረጋችሁት ።

## የመምጣት ፡ ሁለተኛ ፡ እሁድ ።

### ጸሎት ።

ቡሩክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ የተቀደሰውን ፡ መጽሐፍ ፡ ሁሉ ፡ ለመማሪችን ፡ አስጽፈሀዋልና ። እኛ ፡ እንዲህ ፡ እንሰማው ፡ ዘንድ ፡ እናነበውም ፡ እናመለክተውም ፡ እንማረውም ፡ ዘንድ ፡ በውሥጣችንም ፡ እንጠብቀው ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠን ፡ እኛ ፡ በመጽሐፍ ፡ ታግሠን ፡ በርሱም ፡ ተጽናንተን ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ያስደረግህልነውን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ ተስፋ ፡ እንድንጨብጣት ፡ ለወትሮም ፡ በርስዋ ፡ ጸንተን ፡ እንድንጠብቃት ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ሮሜ ፡ ፲፭፡ ፬፡—፲፫።

አስቀድሞ ፡ የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ እኛን ፡ ለማስተማር ፡ ተጽፈዋልና ። ተስፋ ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ በትዕግሥት ፡ በመጻሕፍትም ፡ ባለ ፡ ማጽናናት ። እግዚአብሔርም ፡ የትዕግሥትና ፡ የማጽናናት ፡ አምላክ ፡ አንድ ፡ አሳብ ፡ ይስጣችሁ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ እንደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ። ባንድ ፡ ልብ ፡ ባንድ ፡ አፍም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ የጌታችንን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ አባት ። ስለዚኽም ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ተቀባበሉ ። ክርስቶስም ፡ እንደ ፡ ተቀበለን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ። እላለሁም ፡ ክርስቶስ ፡ የግዝረት ፡ አገልጋይ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነት ። ያባቶችን ፡ ተስፋ ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ። አሕዛብም ፡ ስለ ፡ ምሕረት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ። እንደ ፡ ተጻፈ ። ስለዚኽ ፡ እገዛልኻለሁ ፡ በአሕዛብ ፡ ለስምኽም ፡ ዝማሬ ፡ አቀርባለሁ ። ደግሞም ፡ አለ ። ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ እላንተ ፡ አሕዛብ ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋራ ። ደግሞም ፡ አለ ። አሕዛብ ፡ ሁላች

ሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ። ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ ያመስግኑት ። ኢሳይያስም ፡ ደግሞ ፡ አለ ። ስር ፡ ለእሴይ ፡ ይሆናል ፡ የሚነሣም ፡ ለአሕዛብ ፡ አለቃ ፡ የሚሆን ። አሕዛብም ፡ ተስፋ ፡ ያደርጉታል ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የተስፋ ፡ አምላክ ፡ ደስታን ፡ ሁሉ ፡ ሰላምንም ፡ ይሞላባችሁ ፡ በሃይማኖት ። በተስፋ ፡ ትበዙ ፡ ዘንድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ኃይል ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፳፩፡ ፳፭፡—፴፫፡፡

ምልክትም ፡ ይሆናል ፡ በፀሐይ ፡ በጨረቃም ፡ በከዋክብትም ። በምድር ፡ ላይም ፡ የአሕዛብ ፡ ጭንቀት ፡ በፍርሃት ። ባሕርና ፡ ሞገዱም ፡ ይበጣበጣሉ ፡ የሰዎችም ፡ ነፍስ ፡ ትደክማለች ፡ ከፍርሃት ፡ የተነሣ ፡ በዓለም ፡ ላይም ፡ የሚመጣውን ፡ ከመጠበቅ ፡ የተነሣ ። የሰማዮች ፡ ኃይል ፡ ትናወጻለችና ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ በደመና ፡ ሲመጣ ፡ ያያሉ ፡ ከታላቅ ፡ ኃይል ፡ ከምስጋናም ፡ ጋራ ። ይህች ፡ ትሆንም ፡ ዘንድ ፡ በጀመረች ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ እዩ ፡ ራሳችሁንም ፡ አንሡ ። ደኅንነታችሁ ፡ ቀርብዋልና ። ምሳሌም ፡ አላቸው ። እዩ ፡ ወደ ፡ በለስ ፡ ወደ ፡ ዛፍም ፡ ሁሉ ። በጨበጨበች ፡ ጊዜ ፡ በጋ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ ታያላችሁ ፡ በሰውነታችሁም ፡ ታውቃላችሁ ። እንደሁም ፡ እላንተ ፡ ይህችን ፡ ሁና ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እንደ ፡ ቀረበች ፡ እወቁ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡ ይኸች ፡ ትውልድ ፡ እንደ ታልፍ ፡ ሁሉ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ። ሰማይና ፡ ምድር ፡ ያልፉሉ ። ነገሬ ፡ ግን ፡ አያልፍም ።

---

የመምጸት ፡ ሶስተኛ ፡ እሁድ ።

ጸሎት ።

አቤቱ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አንተ ፡ በመጀመርያ ፡ ሳትመጣ ፡ መለክተኛህን ፡ በፊትህ ፡ መንገድህን ፡ ያበጅልህ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ላክሀው ። ለባሮችህም ፡ ለምሥጢራትህም ፡ መጋቦች ፡ ጸጋህን ፡ ስጣቸው ፡ እርሳቸው ፡ ደግመው ፡ የምቢተኞችን ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ጻድቃን ፡ ጥበብ ፡ መልሰው ፡ መንገድ



ህን ፡ ያበጁልህ ፡ ዘንድ ። አንተ ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ዓለምን ፡ ለመፍረድ ፡ ስትመጣ ፡ እኛ ፡ ተወደን ፡ እንድንገኝ ፡ በፊትህ ፡ አንተ ፡ የምትኖር ፡ የምትገዛም ፡ ከአብና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፬፡ ፩፡—፭፡፡

ስለዚኽም ፡ ሰዎች ፡ እኛን ፡ የክርስቶስ ፡ አገልጋዮች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምሥጢርም ፡ መጋቦች ፡ ሁነን ፡ ይቍጠሩን ። ከዚኽም ፡ ጋራ ፡ ከመጋቦች ፡ ከርሳቸው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ሁኖ ፡ ይገኝ ፡ ዘንድ ፡ ይፈለጋል ። ይኸም ፡ ነገር ፡ ለኔ ፡ ምናምን ፡ ነው ፡ በላንት ፡ ዘንድ ፡ ወይም ፡ በሰው ፡ ቀን ፡ ይፈረድብኝ ፡ ዘንድ ። እኔ ፡ ስንኳ ፡ በራሴ ፡ አልፈርድም ። በራሴ ፡ ላይ ፡ አንዳችን ፡ አላውቅምና ። በዚህ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አልጸደቅሁም ። ደሮ ፡ የሚፈርድብኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ። ስለዚኽም ፡ በምንም ፡ አትፍረዱ ፡ ከጊዜው ፡ አስቀድማችሁ ፡ ጌታ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ። በጨለማ ፡ የተሠወረውንም ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ የሚያወጣ ፡ የልብንም ፡ ምክር ፡ የሚገልጥ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ለሁሉ ፡ ኢያንዳንዱ ፡ ምስጋና ፡ ይሆናል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፲፩፡ ፪፡—፲፡፡

ዮሐንስም ፡ በግዞት ፡ ሳለ ፡ የክርስቶስን ፡ ስራ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁለት ፡ ላከበት ፡ አለውም ። የሚመጣው ፡ አንተን ፡ ነኽ ፡ ወይስ ፡ ሌላውን ፡ ልንጠብቅ ። የሱስም ፡ መለሰላቸው ፡ እንደህም ፡ አላቸው ። ሒዱ ፡ የምትሰሙትንም ። የምታዩትንም ፡ ለዮሐንስ ፡ ንገሩት ። ዕውሮች ፡ ያያሉ ፡ አንካሶችም ፡ ይሔዳሉ ። ለምጻሞችም ፡ ይነጻሉ ፡ ደንቆሮቹም ፡ ይሰማሉ ። የሞቱም ፡ ይነሣሉ ፡ ለድኆችም ፡ በወንጌል ፡ ይሰበካል ። በኔም ፡ የማይጠራጠር ፡ ምስጉን ፡ ነው ። እለዚያም ፡ ከሒዱ ፡ በኋላ ፡ የሱስ ፡ ለተሰበሰቡት ፡ ስለ ፡ ዮሐንስ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ ጀመረ ። ምን ፡ ታዩ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ወጣችሁ ። ሸምበቆን ፡ ነፋስ ፡ የሚወዘውዘውን ። ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ወጣችሁ ፡ ልታዩ ። ቀጭ

ን ፡ ልብስ ፡ የለበሰውን ፡ ሰውን ፡፡ እነሆ ፡ ቀጭን ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ በነገሥታት ፡ ቤት ፡ አሉ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ወጣችሁ ፡ ልታዩ ፡፡ ነቢይን ፡፡ አወን ፡ እላችኋለሁ ፡ ከነቢይም ፡ የሚበልጠውን ፡፡ እርሱ ፡ ነውና ፡ ስለርሱ ፡ የተጻፈለት ፡፡ እነሆ ፡ መልእክተኛዬን ፡ በፊትኽ ፡ እሰደለሁ ፡ መንገድኽን ፡ በፊትህ ፡ የሚያበጅ ፡፡

---

## የመምጻት ፡ አራተኛ ፡ እሁድ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ኃይልህን ፡ አንሣ ፡ በመኻከላችንም ፡ መጥተህ ፡ በችሎትህ ፡ እርደን ፡፡ እኛም ፡ በፊታችን ፡ የተሰራውን ፡ ሩጫ ፡ እንደንሮጥ ፡ በኃጢአታችንና ፡ በዓመፃችን ፡ የተከለከልነውን ፡ ቸር ፡ ምህረትህና ፡ ጸጋህ ፡ ቶሎ ፡ ይፈታን ፡ በልጅህ ፡ በጌታችን ፡ ካሳ ፡፡ ለርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፊልጵስዩስ ፡ ፬፥ ፬፥—፯፡፡

በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ሁለግዜ ፡፡ ደግሞም ፡ እላለሁ ፡፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡፡ የውሃታችሁ ፡ ለሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ትታወቅ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ቅርብ ፡ ነው ፡፡ በምንም ፡ አታስቡ ፡፡ በሁሉ ፡ በጸሎትና ፡ በልመና ፡ ከምስጋና ፡ ጋራ ፡ መሻታችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ትታወቅ ፡፡ ከአእምሮም ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰላም ፡ ልባችሁንና ፡ አሳባችሁን ፡ ይጠብቅ ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፩፥ ፲፱፥—፳፰፡፡

ይኽ ፡ ነው ፡ የዮሐንስ ፡ ምስክር ፡ አይሁድ ፡ ከየሩሳሌም ፡ ካህናትን ፡ ሌዋውያንንም ፡ በላኩበት ፡ ጊዜ ፡ ይጠይቁት ፡ ዘንድ ፡፡ አንተ ፡ ማነኽ ፡ ሲሉ ፡፡ በግልጥም ፡ ተናገረ ፡ አልካደምም ፡፡ አስታወቃቸውም ፡፡ እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ አይደለሁም ፡ ብሎ ፡፡ ጠየቁትም ፡፡ እንኪያ ፡ ማነኽ ፡፡ ኤልያስን ፡



ነኽ ፡ ሲሉ ፡፡ አለም ፡፡ አይደለሁም ፡፡ አንተ ፡ ነቢይን ፡ ነኽ ፡፡ መለሰም ፡፡ አይደለም ፡፡ አሉትም ፡ እንኪያስ ፡ ማነኽ ፡ አንተ ፡፡ ለላኩን ፡ ምላሽ ፡ እንመልስ ፡ ዘንድ ፡፡ ምን ፡ ትላለኽ ፡ ስለ ፡ ራስኽ ፡፡ አለም ፡፡ እኔ ፡ አዋጅ ፡ ነጋሪ ፡ ነኝ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚጮኽ ፡፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ አቅኑ ፡ ነቢዩ ፡ ኢሳይያስ ፡ እንደለ ፡፡ የተላኩትም ፡ ከፈሪሳውያን ፡ ነበሩ ፡፡ ጠየቁትም ፡ አሉትም ፡፡ እንኪያ ፡ ለምን ፡ ታጠምቃለኽ ፡ ክርስቶሰ ፡ ካልሆንኽ ፡ ኤልያስም ፡ ነቢይም ፡፡ ዮሐንስም ፡ መለሰላቸው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ እኔ ፡ በውኃ ፡ አጠምቃለሁ ፡፡ በመኻከላችሁ ፡ ግን ፡ ቁምዋል ፡ የማታውቁት ፡፡ ይኽ ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ በኋላዬ ፡ የሚመጣው ፡፡ በፊቴም ፡ የሆነ ፡ እኔ ፡ የጫማውን ፡ ሲር ፡ እፈታ ፡ ዘንድ ፡ የማይገባኝ ፡፡ ይኽም ፡ ሁሉ ፡ ሆነ ፡ በአብሬ ፡ ቤት ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡፡

---

## የክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ አንድ ፡ ልጅህን ፡ ጠባያችነን ፡ ይለብስ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዘመንም ፡ ከንጽሕት ፡ ድንግል ፡ ይወለድ ፡ ዘንድ ፡ የሰጠህነ ፡፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ እኛም ፡ አዲስ ፡ ተወልደን ፡ የጸጋውንም ፡ ልጅነት ፡ ተቀብለን ፡ ልጆችህ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ እንታደስ ፡ ዘንድ ፡ በርሱ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እርሱ ፡ ካንተና ፡ ከዚያ ፡ መንፈስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ሁኖ ፡ የሚኖርና ፡ የሚገዛ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

¶ ይህችም ፡ ጸሎት ፡ እስከ ፡ ግዝረት ፡ ማታ ፡ ትጸለያለች ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ዕብራውያን ፡ ፩፥ ፩፥—፲፪፥

እግዚአብሔር ፡ አስቀድሞ ፡ በብዙ ፡ ምሳሌ ፡ በብዙ ፡ ነገርም ፡ ላባቶቻችን ፡ በነቢያት ፡ አፍ ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ እርሱ ፡ በዚኸ ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ሁሉን ፡ ወራሽ ፡ ባደረገ

ው ፡ በልጁ ፡ ነገረን ፡፡ ዓለሙንም ፡ በርሱ ፡ የፈጠረ ፡፡ እርሱ
ም ፡ የክብሩ ፡ ብርሃን ፡ የአካሉም ፡ ምሳሌ ፡፡ ሁሉንም ፡ የ
ያዘ ፡ በችሎቱ ፡ ቃል ፡፡ እርሱም ፡ የኃጢአታችንን ፡ ማንጻት ፡
በራሱ ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ በታላቅነት ፡ ቀኝ ፡ በከፍታ ፡ ተቀመ
ጠ ፡፡ ይኸም ፡ ከመላእክት ፡ ይበልጣል ፡ እርሱ ፡ የወረሰው ፡
ስም ፡ ከርሳቸው ፡ በበለጠ ፡ መጠን ፡፡ ማንን ፡ ነው ፡ ከመ
ላእክት ፡ ያለው ፡ ከቶ ፡፡ አንተ ፡ ልጄ ፡ ነህ ፡፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወ
ለድሁኸ ፡፡ ደግሞስ ፡ ማንን ፡ አለ ፡፡ እኔ ፡ አባት ፡ እሆነዋ
ለሁ ፡ እርሱም ፡ ልጄ ፡ ይሆናል ፡፡ ደግሞም ፡ በኵር ፡ ወደ ፡
ዓለም ፡ ባገባ ፡ ጊዜ ፡ አለ ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ መላእክ
ት ፡ ሁሉ ፡ ለርሱ ፡ ይሰግዱሉ ፡፡ ስለ ፡ መላእክትም ፡ አለ ፡፡
መላእክቱን ፡ ንፈሳትን ፡ ያደረገ ፡ አገልጋዮቹንም ፡ የእሳ
ትን ፡ ነበልባሎች ፡፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ ግን ፡ አለ ፡፡ ዙፋንኸ ፡ አ
ምላክ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡፡ የመንግሥትኸም ፡ በትር ፡ የቅ
ንነት ፡ በትር ፡ ነው ፡፡ ጽድቅን ፡ ወደድኸ ፡ ዓመፃንም ፡ ጠላ
ኸ ፡፡ ስለዚኸም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክኸ ፡ የደስታ ፡ ቅ
ቤ ፡ ቀባኸ ፡ ከባልንጀሮችኸ ፡ ይልቅ ፡፡ ደግሞም ፡ አለ ፡፡ አን
ተ ፡ አቤቱ ፡ በጥንት ፡ ምድርን ፡ መሠረትኸ ፡ ሰማዮችም ፡
የጅኸ ፡ ስራ ፡ ናቸው ፡፡ እርሳቸው ፡ ይጠፋሉ ፡ አንተ ፡ ግን ፡
ትኖራለኸ ፡፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጃሉ ፡ እንደ ፡ መ
ጐናጸፊያም ፡ ትጠቀላቸዋለኸ ፡ ይለወጡማል ፡፡ አንተ ፡
ግን ፡ አንተ ፡ ነኸ ፡ ዘመንኸም ፡ አያልቅም ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡ ዮሐንስ ፡ ፩፤ ፩፤—፲፬፤

በመጀመርያ ፡ ቃል ፡ ነበረ ፡፡ ቃልም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘ
ንድ ፡ ነበረ ፡፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ነበረ ፡፡ እርሱም ፡ በ
መጀመርያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነበረ ፡፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡
ሆነ ፡፡ ያለርሱም ፡ ከሆነው ፡ ሁሉ ፡ ምንም ፡ አልሆነም ፡፡ በ
ርሱ ፡ ሕይወት ፡ ነበረች ፡፡ ሕይወትም ፡ የሰው ፡ ብርሃን ፡ ነበ
ረች ፡፡ ብርሃንም ፡ በጨለማ ፡ ያበራል ፡፡ ጨለማም ፡ አታገ
ኘውም ፡፡ ሰው ፡ ነበረ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተላከ ፡ ስሙም ፡
ዮሐንስ ፡፡ እርሱ ፡ ለምስክር ፡ መጣ ፡ ለብርሃን ፡ ሊመሰ
ክር ፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡ ያምን ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱ ፡ ብርሃን ፡ አ



ልነበረም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ለብርሃን ፡ ሊመሰክር ፡ ተላከ ፡፡ ለ
ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚያበራ ፡ እውነተኛ ፡ ብርሃን ፡ ወደ ፡ ዓለ
ም ፡ መጥቶ ፡ ነበረ ፡፡ በዓለም ፡ ነበረ ፡፡ ዓለሙም ፡ በርሱ ፡
ሆነ ፡፡ ዓለምም ፡ አላወቀውም ፡፡ ወደ ፡ ወገኖቹም ፡ መ
ጣ ፡፡ ወገኖቹም ፡ አልተቀበሉትም ፡፡ ለተቀበሉት ፡ ሁሉ ፡ ግ
ን ፡ ሥልጣን ፡ ሰጣቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይሆኑ ፡
ዘንድ ፡ በስሙ ፡ የሚያምኑ ፡፡ ከደም ፡ ያይደሉ ፡ ከሥጋ ፡
ፈቃድም ፡ ከሰው ፡ ፈቃድም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተወለ
ዱ ፡ እንጂ ፡፡ ቃልም ፡ ሥጋ ፡ ሆነ ፡ በኛም ፡ አደረ ፡፡ ክብሩን
ም ፡ አየነ ፡ እንደ ፡ አብ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ልጁ ፡ ክብር ፡፡ ጸ
ጋና ፡ እውነት ፡ የመላበት ፡፡

የቅዱስ ፡ እስጢፋኖስ ፡ በዓል ፡፡

ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ እኛ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በውነትህ ፡
ምስክር ፡ መክንያት ፡ መከራውን ፡ ብንታገሥ ፡ ዓይኖቻችን ፡
ወትሮ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አቅንተን ፡ በሚመጣ ፡ ዘመን ፡ የሚ
ገለጸውን ፡ ክብር ፡ በሃይማኖት ፡ እናይ ፡ ዘንድ ፡ በመንፈ
ስ ፡ ቅዱስም ፡ መልተን ፡ እንደ ፡ መጀመርያ ፡ ሰማዕትህ ፡
እንደ ፡ ቅዱስ ፡ እስጢፋኖስ ፡ አሳዳጆቻችንን ፡ ለመውደድ
ና ፡ ለመባረክ ፡ እንማር ፡ ዘንድ ፡ እርሱም ፡ ለገዳዮቹ ፡ ለ
ምኖሃልና ፡ ቡሩክ ፡ የሱስ ፡ ሆይ ፡ ስላንተ ፡ የሚታገሡትን ፡
ሁሉ ፡ ትደግፍ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ የምትቆ
ም ፡ አንደኛ ፡ መኻከለኛችንና ፡ ጰራቅሊጦሳችን ፡ ሁነህ ፡፡
አሜን ፡፡

* ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ የልደት ፡ ጸሎት ፡ ይከተል ፡
እርሱም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይደገም ፡ እስከ ፡ ግዝ
ረት ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፯፤ ፶፭፤—፷፤

መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ መልቶበት ፡ ነበረ ፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡
ተመለከተ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ክብር ፡ አየ ፡፡ የሱስም ፡

በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ቁሞ ፡፡ አለም ፡፡ እነሆ ፡ ሰማዮችን ፡ ተከፍተው ፡ አያለሁ ፡ የሰው ፡ ልጅንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ቁሞ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ጮሁ ፡ ጆሮዋቸውንም ፡ ደፈኑ ፡፡ ያንድ ፡ ልብም ፡ ሁነው ፡ ተነሡበት ፡ ካገርም ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ አወጡት ፡ ወገሩትም ፡፡ ምስክሮችም ፡ ወደንድ ፡ ጐበዝ ፡ እግር ፡ ስሙን ፡ ሳውል ፡ ወደሚሉት ፡ ልብሳቸውን ፡ አኖሩ ፡፡ እስጢፋኖስንም ፡ ወገሩ ፡ እርሱ ፡ ሲጸልይ ፡ ሲልም ፡፡ አቤቱ ፡ የሱስ ፡ ሆይ ፡ መንፈሴን ፡ ተቀበል ፡፡ በጕልበቱም ፡ ተንበረከከ ፡ በታላቅ ፡ ቃልም ፡ ጮኸ ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡ አቤቱ ፡ ይህችን ፡ ኃጢአት ፡ አትቍጠርባቸው ፡፡ ይህነንም ፡ ብሎ ፡ አንቀላፋ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳፫፤ ፴፬፤—፴፱፤

ስለዚኽ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ ነቢያትን ፡ እልክባችኋለሁ ፡ ጠቢባንንም ፡ ጻፎችንም ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አያሌን ፡ ትገድላላችሁ ፡ ትሰቅሉማላችሁ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አያሌን ፡ በመስጊዶቻችሁ ፡ ትገርፋላችሁ ፡ ካገር ፡ ወደገርም ፡ ታሳድዋቸዋላችሁ ፡፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የፈሰሰው ፡ የጻድቅ ፡ ደም ፡ ሁሉ ፡ ከጻድቁ ፡ ከአቤል ፡ ደም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ በራክያ ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡ ዘካርያስ ፡ ደም ፡ ድርስ ፡ በቤተ ፡ መቅደስና ፡ በመሠዊያው ፡ መኻከል ፡ የገደላችሁት ፡ ይመጣባችሁ ፡ ዘንድ ፡፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ ይኽ ፡ ሁሉ ፡ በዚች ፡ ትውልድ ፡ ላይ ፡ የመጣል ፡፡ የሩሳሌም ፡ የሩሳሌም ፡፡ ነቢያትን ፡ የምትገድይ ፡ ወደንችም ፡ የተላኩትን ፡ የምትወግሪ ፡፡ ስንተግዜ ፡ ልጆችሽን ፡ እሰበስብ ፡ ዘንድ ፡ ወደድሁ ፡ ዶሮ ፡ ጫጩቶችዋን ፡ በክንፏዋ ፡ ታች ፡ እንድትሰበስብ ፡፡ እንቢንም ፡ አላችሁ ፡፡ እነሆ ፡ ቤታችሁ ፡ የተፈታ ፡ ሁኖ ፡ ይቀርላችኋል ፡፡ እላችኋለሁና ፡ እንደታዩኝ ፡ እስክትሉ ፡ ድረስ ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚመጣ ፡ የተባረከ ፡ ነው ፡፡



የቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ የወንጌላዊ ፡ በዓል ፡፡

ጸሎት ፡፡

መሐሪ ፡ ጌታችን ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ የብርሃንህን ፡ ጸደል ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ እንድትሰድ ፡ እርስዋ ፡ በተባረከ ፡ ሐዋርያህና ፡ ወንጌላዊህ ፡ በቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ ትምህርት ፡ በርታ ፡ በውነትህ ፡ ብርሃን ፡ እንደህ ፡ ትመላለስ ፡ ዘንድ ፡ በመጨርሻ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ብርሃን ፡ እንድትደርስ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ የዮሐንስ ፡ ፩፤ መልእክት ፡ ፩፤ ፩፤—፲፤

ከመጀመርያ ፡ ጀምሮ ፡ የነበረ ፡፡ የሰማነውም ፡፡ ባይናችንም ፡ ያየነው ፡፡ የተመለከትነውም ፡ እጆችነም ፡ የደሰሰችው ፡ ስለ ፡ ሕይወት ፡ ነገር ፡፡ ሕይወትም ፡ ተገለጸች ፡፡ አየነም ፡ እንመሰክርማለን ፡፡ በዘላለሙም ፡ ሕይወት ፡ እናስታወቃችኋለን ፡፡ በአብ ፡ ዘንድ ፡ በነበረች ፡ ለኛም ፡ በተገለጸች ፡፡ ያየነውንም ፡ የሰማነውም ፡ እርሱን ፡ እናስታውቅባችኋለን ፡፡ ለላንት ፡ ደግሞ ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ ትሆንላችሁ ፡ ዘንድ ፡፡ የኛ ፡ አንድነት ፡ ግን ፡ ከአብ ፡ ጋራ ፡ ናት ፡፡ ከልጁም ፡ ከየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጋራ ፡፡ ይኽችንም ፡ ነገር ፡ እንጽፋላችኋለን ፡ ደስታችሁ ፡ ትፈጽም ፡ ዘንድ ፡፡ ከርሱም ፡ የሰማናት ፡ የነገርናችኋትም ፡ መልእክት ፡ ይኽች ፡ ናት ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከቶም ፡ ጨለማ ፡ እንደ ፡ ሌለበት ፡፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ አለነ ፡ ብለን ፡ በጨለማ ፡ ብንመላለስ ፡ አሰተኞች ፡ ሆነ ፡ እውነትንም ፡ አናደርግም ፡፡ በብርሃን ፡ ግን ፡ ብንመላለስ ፡ እርሱ ፡ በብርሃን ፡ እንደለ ፡ ለኛ ፡ አንድነት ፡ አለነ ፡ እርሱ ፡ በርሳችን ፡፡ የልጁም ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ደም ፡ ከኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ያነጻናል ፡፡ ኃጢአት ፡ የሉብነም ፡ ብንል ፡ እኛ ፡ ራሳችነን ፡ እናስታለን ፡ እውነትም ፡ የለችነም ፡፡ በኃጢአታችን ፡ ብንናዘዝ ፡ እርሱ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡ ጻድቅም ፡ ነው ፡ ኃጢአታችነን ፡ ይቅር ፡ ይልን ፡ ዘንድ ፡ ከግፏም ፡ ሁሉ ፡ ያነጻን ፡ ዘንድ ፡፡ ኃጢአት ፡ አልሰራነም ፡ ብንለ ፡ ላሰተኛ ፡ እናደርገዋለን ፡ ቃሉም ፡ በኛ ፡ የልነም ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፳፩፤ ፲፱፤ — ፳፭፤

ይህንንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ። ተከተለኝ ፡ አለው ። ጴጥሮስም ፡ ተመለሰ ፡ የሱስም ፡ የወደደውን ፡ በራትም ፡ ጊዜ ፡ ባጠገቡ ፡ የተቀመጠውን ፡ ጌታ ፡ ሆይም ፡ ማነው ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጥኽ ፡ ያለውን ። ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ሲከተለው ፡ አየ ፡ ጴጥሮስም ፡ ይህነን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ የሱስን ፡ አለው ። አቤቱ ፡ ደኽስ ፡ እንዴት ፡ ነው ። የሱስም ፡ አለው ። እርሱስ ፡ እስክመጣ ፡ ድረስ ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ብወድ ፡ ምን ፡ ገደደኽ ። አንተ ፡ ተከተለኝ ። አሁንም ፡ ይኽ ፡ ነገር ፡ ያ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ እንዳይሞት ፡ በወንድሞች ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። የሱስን ፡ እንዳይሞት ፡ አላለውም ። ብወድስ ፡ እስክመጣ ፡ ድረሰ ፡ ቢቀመጥ ፡ ምን ፡ ገደደኽ ፡ እንጂ ። ይኽ ፡ ደቀ ፡ መዝሙርም ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ በዚኽ ፡ ነገር ፡ የመሰከረ ፡ የጻፈውም ። ምስክሩም ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለን ። እጅግ ፡ ሌላ ፡ ነገርም ፡ አለ ፡ የሱስ ፡ ያደረገው ። እርሱም ፡ በያንዳንዱ ፡ ቢጻፍ ፡ ዓለም ፡ ስንኳ ፡ የተጻፈውን ፡ መጽሐፍ ፡ ባልቻለው ፡ በመሰለኝ ። አሜን ።

የንጹሓን ፡ ሕፃናት ፡ በዓል ።

ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ከልጆችና ፡ ከሕፃናት ፡ አፍ ፡ ኀይልን ፡ ያዘጋጅኽ ፡ ሕፃናትንም ፡ በሞታቸው ፡ ያመሰግኑህ ፡ ዘንድ ፡ ያደረግሃቸው ። ኀጢአትን ፡ ሁሉ ፡ በውሥጣችን ፡ ግደል ። እንዲሁም ፡ በጸጋህ ፡ አብርታን ፡ እኛ ፡ በሕይወታችን ፡ ንጽሕና ፡ በሃይማኖታችንም ፡ ጽናት ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

በመልእክት ፡ ፈንታ ። ራእይ ፡ ፲፬፤ ፩ — ፭፤

አየሁም ፡ እነሆም ፡ በግ ፡ በጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡፡



ከርሱም ፡ ጋራ ፡ መቶ ፡ ካርባ ፡ አራት ፡ ሺህ ። ያባቱም ፡ ስም ፡ በግምባራቸው ፡ ተጽፎዋል ። ከሰማይም ፡ ድምፅን ፡ ሰማሁ ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ውኆች ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ ታላቅ ፡ ነጕድጓድም ፡ ድምፅ ። መሰንቆ ፡ የሚመቱትንም ፡ ድምጽ ፡ ሰማሁ ፡ በመሰንቋቸው ፡ ሲደረድሩ ። እንደ ፡ ዲስ ፡ ምስጋናም ፡ ያለውን ፡ በዙፋኑ ፡ ፊት ፡ ባራቱ ፡ እንስሶችና ፡ በቀሳውስቱም ፡ ፊት ፡ አዘመሩ ። ማንም ፡ ያችን ፡ ዝማሬ ፡ ይማር ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውም ፡ ከምድር ፡ ዘንድ ፡ ከተዋጁ ፡ ከመቶ ፡ አርባ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ በቀር ። እሌኽ ፡ ናቸው ፡ ከሴቶች ፡ ጋራ ፡ ያልረከሱ ። ድንግሎች ፡ ናቸውና ። በጉንም ፡ ወደሚሔድበት ፡ ሁሉ ፡ የሚከተሉት ፡ እሌኽ ፡ ናቸው ። እሌኽ ፡ ከሰዎች ፡ ተዋጁ ፡ ቀደማያት ፡ ሁነው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለበጉም ። ባፋቸውም ፡ ሐሰት ፡ አልተገኘም ። በእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ናቸውና ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፪፤ ፲፫፤ — ፲፰፤

እርሳቸውም ፡ ከሔዱ ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ለዮሴፍ ፡ በሕልም ፡ ታየው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ተነሣ ፡ ሕፃኑንም ፡ ከናቱ ፡ ጋራ ፡ ይዘኅ ፡ ወደ ፡ ምሥር ፡ ሽሽ ። ከዚያም ፡ እስክነግርኽ ፡ ድረስ ፡ ተቀመጥ ። ሄሮድስ ፡ ሕፃኑን ፡ ሊገድለው ፡ ይሿዋልና ። እርሱም ፡ ተነሥቶ ፡ ሕፃኑንና ፡ እናቱን ፡ በሌት ፡ ወሰደ ፡ ወደ ፡ ምሥርም ፡ ሔደ ። ከዚያም ፡ ሄሮድስ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ተቀመጠ ። ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በነቢይ ፡ የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ከምሥር ፡ ልጄን ፡ ጸራሁት ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ሄሮድስ ፡ የጥበብ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ተሣለቁበት ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። ሰደደም ፡ በቤተ ፡ ልሔምም ፡ በወሰንዋም ፡ ሁሉ ፡ ያሉትን ፡ ሕፃናት ፡ ሁሉ ፡ አስገደለ ። ሁለት ፡ አመት ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ከዚያም ፡ የሚያንሰውን ። ከጥበብ ፡ ሰዎች ፡ በጣም ፡ መርምሮ ፡ በጠየቀው ፡ ዘመን ፡ በኵል ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ተፈጸመ ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ የተባለው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ድምፅ ፡ በራማ ፡ ተሰማ ፡

ልቅሶ ፡ ዋይታም ፡ እጅግ ፡ ማልቀስም ፡፡ ራሔል ፡ ለልጆችዋ ፡ ታለቅሳለች ፡ ለመጽናናትም ፡ እምቢ ፡ አለች ፡ የሉምና ፡፡

## ክልደት ፡ በኋላ ፡ የሚከተል ፡ እሁድ ፡፡

### ጸሎት ፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ አንድ ፡ ልጅህን ፡ ጠባያችንን ፡ ይለብስ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዘመንም ፡ ከንጽሕት ፡ ድንግል ፡ ይወለድ ፡ ዘንድ ፡ የሰጠህን ፡፡ ጸጋህን ፡ ስጠን ፡ እኛም ፡ አዲስ ፡ ተወልደን ፡ የጸጋውንም ፡ ልጅነት ፡ ተቀብለን ፡ ልጆችህ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ እንታደስ ፡ ዘንድ ፡ በርሱ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እርሱ ፡ ካንተና ፡ ከዚያ ፡ መንፈስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ሁኖ ፡ የሚኖርና ፡ የሚገዛ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ገላትያን ፡ ፬፤ ፩፤—፯፤፤

እኔም ፡ እላለሁ ፡ ወራሽ ፡ ሕፃን ፡ በሆነበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በርሱና ፡ በባርያ ፡ ማኽል ፡ ልዩነት ፡ የለውም ፡ እርሱ ፡ የሁሉ ፡ ጌታ ፡ ሲሆን ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ካለቆችና ፡ ከመጋቦች ፡ በታች ፡ ነው ፡፡ አባቱ ፡ እስካደረገለት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡፡ እንደሁም ፡ እኛ ፡ ሕፃናት ፡ ሳለን ፡ ለዚኽ ፡ ዓለም ፡ ለመሠረት ፡ ነገሬ ፡ ባሮች ፡ ነበርን ፡፡ የዘመን ፡ ፍጻሜ ፡ ግን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጁን ፡ ላከ ፡፡ ከሴት ፡ የተወለደውን ፡ ከኦሪት ፡ በታችም ፡ የሆነውን ፡፡ ከኦሪት ፡ በታች ፡ ያሉትን ፡ ይበዠ ፡ ዘንድ ፡፡ የልጅነትንም ፡ መዝገብ ፡ እንወስድ ፡ ዘንድ ፡፡ ልጆችም ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የልጁን ፡ መንፈስ ፡ በልባችሁ ፡ ላከ ፡ አባታችን ፡ አብ ፡ ሲል ፡ የሚጮህ ፡፡ እንግዴህም ፡ ባርያ ፡ አይደለኽም ፡ ልጅ ፡ እንጅ ፡፡ ልጅም ፡ ከሆንኽ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ወራሽ ፡ ነህ ፡ በክርስቶስ ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፩፤ ፲፰፤—፳፭፤

የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ልደትም ፡ እንደህ ፡ ነበረ ፡፡ እናቱ ፡ ማርያም ፡ ለዮሴፍ ፡ በታጨች ፡ ጊዜ ፡፡ ሳይገናኙም ፡ ከመ



ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፀንሳ ፡ ተገኘች ፡፡ ዮሴፍም ፡ ጬኛዋ ፡ ጻድቅ ፡ ነበረ ፡ በሕዝቡም ፡ ፊት ፡ ሊጸየፋት ፡ አልወደደም ፡ ሸሽጎ ፡ ይለቃት ፡ ዘንድ ፡ አለ ፡ እንጅ ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ይህነን ፡ ሲያስብ ፡ እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በሕልም ፡ ታየው ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡ ዮሴፍ ፡ ሆይ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ጬኛኽን ፡ ማርያምን ፡ ከመውሰድ ፡ አትፍራ ፡፡ በርስዋ ፡ የተፀነሰ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡፡ ልጅንም ፡ ትወልዳለች ፡ ስሙንም ፡ የሱስ ፡ ትለዋለኽ ፡፡ እርሱ ፡ ሕዝቡን ፡ ከኀጢአታቸው ፡ ያድናቸዋልና ፡፡ ይኽም ፡ ሁሉ ፡ ሆነ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በነቢይ ፡ የተባለው ፡ ሊፈጸም ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡ እነሆ ፡ ድንግል ፡ ትፀንሳለች ፡ ልጅንም ፡ ትወልዳለች ፡ ስሙንም ፡ አማኑኤል ፡ ይሉታል ፡፡ ትርጓሜው ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ የሆነ ፡፡ ዮሴፍም ፡ ከንቅልፉ ፡ ተነሥቶ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ እንደዘዘው ፡ አደረገ ፡፡ ጬኛውንም ፡ ማርያምን ፡ ወሰደ ፡፡ አላወቃትምም ፡ የበኽር ፡ ልጅዋን ፡ እስክ ፡ ትወልድ ፡ ድረስ ፡፡ ስሙንም ፡ የሱስ ፡ አለው ፡፡

## የክርስቶስ ፡ ግዝረት ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ የተባረከውን ፡ ልጅህ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ አስገዘረሀዋልና ፡ ከሕግም ፡ በታች ፡ አድርገሀዋልና ፡ የመንፈስን ፡ አይነተኛውን ፡ ግዝረት ፡ ስጠን ፡ ልባችንና ፡ ብልታችን ፡ ሁሉ ፡ ከዓለምና ፡ ከሥጋ ፡ ፍትወት ፡ ሁሉ ፡ ሙቶ ፡ እኛ ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ለተባረከች ፡ ፈቃድህ ፡ እንታዘዝ ፡ ዘንድ ፡ በርሱ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ሮሜ ፡ ፬፤ ፰፤—፲፬፤፤

ምስጉን ፡ ነው ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃጢአቱን ፡ የማይቈጥርበት ፡ ሰው ፡፡ ይህች ፡ ምስጋና ፡ ግን ፡ በግዝረትን ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ ናት ፡ ወይስ ፡ በቍላፍነት ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡፡ ሃይማኖት ፡ ለአብርሃም ፡ ጽድቅ ፡ ሁና ፡ ተቈጠረችለት ፡ ብለናልና ፡፡

እንደትም : ተቈጠረችለት :: በግዝረትን : ሳለ : ነው :
ወይስ : በቊላፍነት :: በግዝረት : አይደለም :: በቊላፍ
ነት : እንጅ :: የግዝረትንም : ምልክት : በቊላፍነት : ሳለ :
ለሆነችው : ለሃይማኖቱ : ጽድቅ : ማሕተም : ልትሆነው :
ተቀበላት :: እርሱ : በቊላፍነት : ተገኝተው : ላመኑ :
ሁሉ : አባት : ይሆንላቸው : ዘንድ :: ጽድቅ : ለርሳቸው :
ደግሞ : ትቈጠርላቸው : ዘንድ :: አባትም : ለግዝረት ::
ከግዝረት : ብቻ : ላሉ : አይደለም :: ያባታችንን : የአብርሃ
ምን : በቊላፍነት : የነበረችውን : የሃይማኖቱን : ፍለጋ :
ደግሞ : ለሚከተሉ : እንጅ :: ለአብርሃምና : ለዘሩ : የሆ
ነች : ተስፋ : ዓለምን : ይወርስ : ዘንድ : በኦሪት : የመ
ጣች : አይደለችምና :: በሃይማኖት : ጽድቅ : እንጅ :: የኦ
ሪት : ሰዎችስ : ወራሾች : ከሆኑ :: ሃይማኖት : ከንቱ :
በሆነች : ተስፋም : ባልጠቀመች ::

የወንጌል : ክፍል :: ሉቃስ : ፪ ፲፫ — ፳፩ ::

መላእክትም : ከርሳቸው : ዘንድ : ወደ : ሰማይ : በሔዱ :
ጊዜ : ጠባቆች : እርሱ : በርሳቸው : ወደ : ቤተ : ልሔም :
ደህነን : እግዚአብሔር : ያስታወቀነውን : የሆነውን : ነገር :
እናይ : ዘንድ : እንሒድ : አሉ :: ፈጥነውም : መጡ : ማር
ያምንም : አገኙ : ዮሴፍንም :: ሕፃኑንም : በበረት : ተኝ
ቶ :: ባዩም : ጊዜ : ስለዚህ : ሕፃን : የተባላቸውን : ነገር :
አወሩ :: የሰሙትም : ሁሉ : ጠባቆች : በነገርዋቸው :
ነገር : ተደነቁ :: ማርያም : ግን : ይህነን : ነገር : ሁሉ : ትጠ
ብቀው : በልብዋም : ትመረምረው : ነበረች :: ጠባቆች
ም : ተመለሱ : በሰሙት : ባዩትም : ሁሉ : እንደ : ተባ
ለላቸው : እግዚአብሔርን : ኢያከበሩ : ኢያመሰገኑም ::
ስምንተኛው : ቀንም : ሕፃኑ : ሊገዘር : በተፈጸመ : ጊዜ :
ስሙ : የሱስ : ተባለ :: አስቀድሞ : በሆድ : ሳይረገዝ :
ከመልአኩ : የተባለበት ::

* ይች : ጸሎትም : መልእክትም : ወንጌልም : ለዕለት :
ዕለት : ነው : እስከ : ኤጲፋንያስ : ድረስ ::



የኤጲፋንያስ : በዓል :

ክርስቶስ : ለአረማውያን : የተገለጸባት ::

ጸሎት ::

አቤቱ : በኮከብ : መርተህ : ላረማውያን : አንድ : ልጅህ
ን : የገለጽህላቸው :: ለኛም : አሁን : በሃይማኖት : ላወቅነ
ህ : በምህረትህ : ስጠን : ከዚህች : ሕይወት : በኋላ : የከበ
ረችን : መለኮትህ : እንጸግብ : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ :
በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ኤፌሶን : ፫ ፩ — ፲፪ ::

ስለዚኸም : እኔ : ጳውሎስ : ብክርስቶስ : የሱስ : ለላን
ት : ላሕዛብ : የታሠርሁ :: ስለላንት : የተሰጠችኝን : የእግ
ዚአብሔርን : ጸጋ : መጋቢነት : ሰምታችሁ : እንደ : ሆና
ችሁ :: በራእይ : ምሥጢሩን : አስታውቁልኛልና : (በጥቂት :
እንደ : ጻፍሁላችሁ :: እንዲቻላችሁ : ስታነቡት : ጊዜ :
ማስተዋሌን : በክርስቶስ : ምሥጢር : ታውቁ : ዘንድ) ::
ባለፈ : ዘመን : ለሰው : ልጆች : ያልታወቀቸውን :: ዛሬ :
ለቅዱሳን : ሐዋርያቱ : ለነቢያቱም : በመንፈስ : እንደ :
ተገለጠች :: አሕዛብ : አንድ : እንደ : ሆኑ : በርስቱ : አን
ድም : እንደ : ሆኑ : በሥጋው :: በክርስቶስ : ተስፋም :
አንድ : እንደ : ሆኑ :: በወንጌሉ : እኔ : አገልጋይ : የሆንሁ
ለት : እንደ : እግዚአብሔር : ጸጋ : ስጥወታ :: እንደ : ችሎ
ቱ : ስራ : እንደ : ተሰጠችኝ :: ለኔም : ከቅዱሳን : ሁሉ :
ለተጠቃሁ :: ለኔ : ይህች : ጸጋ : ተሰጠችኝ : ለአሕዛብ : የ
ምስራች : እነግር : ዘንድ : በማትመረመር : በክርስቶስ :
ጸጋ : ባለጠግነት :: ለሰውም : ሁሉ : የምሥጢሩን : ሥር
ዓት : አበራ : ዘንድ : ተሸሽጎ : የነበረውን : ከጥንት : ጀ
ምሮ :: በእግዚአብሔር : ዘንድ : ሁሉን : በፈጠረ : በየሱስ :
ክርስቶስ :: ዛሬ : ላለቆችና : ለሥልጣናትም : በሰማያት :
የእግዚአብሔር : ልዩ : ልዩ : ጥበብ : በቤተ : ክርስቲያን :
ትታወቅ : ዘንድ :: እንደ : ቀደመው : እንደ : ዘላለም : ፈ

ቃዲ ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ በጌታችን ፡ እንደ ፡ አደረጋት ::
በርሱ ፡ ድፍረትን ፡ ያገኘነ ፡ ያለ ፡ መጠራጠርም ፡ ወደርሱ ፡
መግባትን ፡ በሃይማኖቱ ::

የወንጌል ፡ ክፍል :: ማቴዎስ ፡ ፪፡ ፩፡—፲፪፡፡

የሱስም ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ በተወለደ ፡ ጊዜ ፡ በይሁዳ ፡ አ
ገር ፡ በንጉሡ ፡ በሄሮድስ ፡ ዘመን :: እነሆ ፡ የጥበብ ፡ ሰዎች ፡
ከምሥራቅ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ መጡ :: ኢያሉ ፡ ወዴት ፡
ነው ፡ የተወለደ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ :: ኮከቡን ፡ በምሥራ
ቅ ፡ አይተናልና ፡ እንሰግድለትም ፡ ዘንድ ፡ መጥተናልና ::
ሄሮድስ ፡ ንጉሥም ፡ ሰምቶ ፡ ደነገፀ ፡ የሩሳሌምም ፡ ሁ
ሉ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ :: የካህናትንም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ የሕዝ
ብንም ፡ ጻፎች ፡ ሰበሰበ ፡ ጠየቃቸውም ፡ ወዴት ፡ ይወለ
ደል ፡ ክርስቶስ ፡ ብሎ :: እርሳቸውም ፡ አሉት ፡ በቤተ ፡ ል
ሔም ፡ በይሁዳ ፡ አገር :: እንዲህ ፡ በነቢይ ፡ ተጽፏልና ::
አንቺ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ የይሁዳ ፡ ምድር ፡ በይሁዳ ፡ አለቆ
ች ፡ አታንሺም :: ሕዝቤን ፡ እሥራኤልን ፡ የሚጠብቅ ፡
ገዢ ፡ካንቺ ፡ ይወፀልና :: ሄሮድስ ፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የጥ
በብን ፡ ሰዎች ፡ በስውር ፡ ጸራቸው ፡ ከርሳቸውም ፡ ተረዳ ፡
የታያቸውን ፡ የኮከቡን ፡ ዘመን :: ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔምም ፡
ሰደደቻው ፡ አላቸውም :: ሒዱ ፡ ስለ ፡ ተወለደም ፡ ሕፃን ፡
አጅግ ፡ መርምሩ :: ባገኛችሁትም ፡ ጊዜ ፡ ንገሩኝ ፡ እኔም ፡
መጥቼ ፡ እሰግድለት ፡ ዘንድ :: እርሳቸውም ፡ ከንጉሥ ፡
ከሰሙ ፡ በኋላ ፡ ሔዱ :: እነሆም ፡ በምሥራቅ ፡ ያዩት ፡ ኮ
ከብ ፡ መራቸው ፡ ሕፃኑ ፡ ባለበቱ ፡ ላይ ፡ ደርሶ ፡ እስኪቆ
ም ፡ ድረስ :: ኮከቡንም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ደሳላቸው ፡ አጅግ ፡
ታላቅ ፡ ደስታ :: ወደ ፡ ቤትም ፡ መጹ ፡ ሕፃኑንመ ፡ ከናቱ ፡
ከማርያም ፡ ጋራ ፡ አገኙት :: ወድቀውም ፡ ሰገዱለት ::
መዝገባቸውንም ፡ ከፈቱ ፡ ወርቅንም ፡ ዕጣንንም ፡ ከርቤ
ንም ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ አድርገው ፡ ሰጡት :: በሕልምም ፡
ታያቸው ፡ ወደ ፡ ሄሮድስ ፡ እንዳይመለሱ :: በሌላ ፡ መንገ
ድም ፡ ወደገራቸው ፡ ሔዱ ::



መጀመርያ ፡ እሁድ ፡ ከኤጲፋንያስ ፡ በኋላ ::

ጸሎት ::

አቤቱ ፡ እንለምንሃለን ፡ የሚጸሩብህን ፡ የሕዝብህን ፡
ልመና ፡ በምህረትህ ፡ እንድትቀበለው ፡ ያደርጉት ፡ ዘንድ፡
የሚገባቸውን ፡ ነገር ፡ ያውቁት ፡ ዘንድ ፡ ያስታውሉትም ፡
ዘንድ ፡ ታምነውም ፡ ይፈጽሙት ፡ ዘንድ ፡ ጸጋውንና ፡ ኃይ
ልን ፡ እንዲያገኙ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት ፡ ክፍል :: ሮሜ ፡ ፲፪፡ ፩፡ — ፭፡፡

እኔ ፡ ግን ፡ እለምናችኋለሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ምሕረት :: ሥጋችሁን ፡ ታቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ ሕያው
ት ፡ መሥዋዕት ፡ አድርጋችሁ ፡ የተቀደሰችም ፡ እግዚአብሔ
ርንም ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ :: በምትገባችሁ ፡ ማገልገል :: ይ
ህንንም ፡ ዓለም ፡ አትምሰሉ :: ነገር ፡ ግን ፡ መልካችሁን ፡
ለውጡ ፡ በልባችሁ ፡ መታደስ :: የእግዚአብሔርን ፡ በጎ ፡
ፈጽምትንም ፡ የተቀበለችውንም ፡ ፈቃድ ፡ ምን ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ትፈትኑ ፡ ዘንድ :: በተሰጠችኝም ፡ ጸጋ ፡ በመካከላ
ችሁ ፡ ላለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እላለሁ :: ነፍሳችሁን ፡ እንደ ፡ ማ
ይገባችሁ ፡ ታላቅ ፡ እንዳታድርጉ ፡ ነፍሳችሁ ፡ እንደሚገባች
ሁ ፡ ይምሰላችሁ ፡ እንጅ ፡ ኢያንዳንዳችሁ ፡ እግዚአብሔ
ር ፡ እንደ ፡ ከፈለው ፡ እንደ ፡ ሃይማኖቱ ፡ መጠን :: ለኛም ፡
አጅግ ፡ ብልት ፡ እንዳለን ፡ ባንድ ፡ ገላ :: ብልት ፡ ሁሉ ፡ ግ
ን ፡ ስራውም ፡ አንድ ፡ እንዳልሆነ :: እንዲሁም ፡ እኛ ፡ ብዙ ፡
ሁነን ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ነን ፡ በክርስቶስ :: እርሱ ፡ በርሳችን ፡ ግ
ን ፡ ኢያንዳንዳችን ፡ የባልንጀራው ፡ ብልት ፡ ነው ::

የወንጌል ፡ ክፍል :: ሉቃስ ፡ ፪፡ ፵፩፡—፶፪፡፡

አባት ፡ እናቱም ፡ ባመት ፡ ባመት ፡ ለፋሲካ ፡ በዓል ፡ ወ
ደ ፡ የሩሳሌም ፡ ይሔዱ ፡ ነበሩ :: ዕድሜውም ፡ አሥራ ፡ ሁ
ለት ፡ አመት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ወጡ ፡ እ
ንደ ፡ በዓሉ ፡ ወግ :: ወራቱም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ሲመለ
ሱ ፡ ብላቴናው ፡ የሱስ ፡ በየሩሳሌም ፡ ቀረ :: ዮሴፍም ፡ እ
ናቱም ፡ አላወቁትም :: ከባልንጀሮችም ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ይመ

ስላቸው : ነበር :: ያንድ : ቀንም : መንገድ : ሔዱ : በዘመደ
ቻቸውና : በሚያውቋቸውም : ዘንድ : ፈለጉት :: ባላገኙት
ም : ጊዜ : ወደ : የሩሳሌም : ሊሹት : ተመለሱ :: ከሦስ
ት : ቀንም : በኋላ : በመቅደስ : ተቀምጦ : አገኙት : በመም
ህራን : ማኸል : ሲሰማቸው : ሲጠይቃቸውም :: የሚሰሙ
ትም : ሁሉ : በማስተዋሉና : በምላሹ : አደነቁ :: ባዩትም :
ጊዜ : አደነቁ :: እናቱም : አለችው :: ልጄ : ሆይ : ለምን : እ
ንዲህ : አደረግኸብን :: እነሆ : አባትኽና : እኔ : ተጨንቀን :
ፈለግነኽ :: አላቸውም :: የፈለጋችሁኝ : ምነው :: ላባቴ : ባ
ለው : እሆን : ዘንድ : እንዲገባኝ : አታውቁምን :: እርሳ
ቸው : ግን : ያላቸውን : ነገር : አላስተዋሉም :: ከርሳቸው
ም : ጋራ : ወረደ : ወደ : ናዝሬትም : መጸ : ለርሳቸውም :
ይታዘዝ : ነበረ :: እናቱም : ይህነን : ነገር : ሁሉ : በልብዋ :
ጠበቀች :: የሱስም : አደገ : በጥበብና : በቁመት : በጸጋ
ም : በእግዚአብሔር : ዘንድ : በሰውም : ዘንድ ::

---

ሁለተኛ : እሁድ : ከኤጲፋንያስ : በኋላ ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : ለዘላለምም : የምትኖር : አም
ላክ : ሆይ :: አንተ : በሰማይና : በምድር : ያለውን : ነገር :
ሁሉ : ገዝተሃልና : የሕዝብህን : ልመና : በምሕረት : ስማ :
የዘመናችንም : ቀን : ሁሉ : ሰላምህን : ስጠኝ : በየሱስ :
ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ሮሜ : ፲፪፡ ፮፡—፲፮።

እንደ : ተሰጠችነም : ጸጋ : ልዩ : ልዩ : ስጥወታ : ኑራልናለ
ችና :: ትንቢት : ያለችው : እንደ : ሃይማኖት : ምሳሌ : ት
ንቢት : ይናገር :: አገልጋይም : ቢሆን : በማገልገሉ : ይንቃ ::
አስተማሪም : ቢሆን : በማስተማሩ :: የሚያጸናናም : ቢሆ
ን : በማጽናናት :: ሰጪም : ቢሆን : በየውሃት : ይስጥ ::
አለቃም : ቢሆን : ሳይታከት : ይግዛ :: መጽዋችም : ቢሆን :
በደስታ : ይመጽውት :: ፍቅር : ያለ : ግብዝና : ትሁን :: ክፉ



ን : ጸልታችሁ : ለበጎ : ተጣበቁ :: ከወንድሞች : ጋራ : ከለ
ልባችሁ : ተዋደዱ : እርሱ : በርሳችሁ :: እርሱ : በርሳችሁ
ም : በማክበር : ተቀደደሙ :: በስራችሁም : አታከቱ :: በ
መንፈስም : የምትቃጠሉ : ሁኑ : ለእግዚአብሔርም : የ
ምትገዙ :: በተስፋም : ደስ : የሚላችሁ : ሁኑ :: በመከራ
ም : የምትታገሡ :: በጸሎትም : የምታዘወትሩ :: ለቅዱሳ
ን : በሚሹት : ነገር : የምትከፈፈሉ : ሁኑ :: እንግዶችን :
ለመቀበል : የምትቸኵሉ : ሁኑ :: የሚያሳድዋችሁን : መ
ርቁ :: መርቁ : አትርገሙም :: ደስ : ካላቸው : ጋራ : ደስ :
ይበላችሁ :: ከሚያለቅሱም : ጋራ : አልቅሱ :: አንድ : ልብ :
ይሁንላችሁ : እርሱ : በርሳችሁ :: ከፍ : ወደለ : ነገርም : ል
ባችሁን : አታደርጉ : ዝቅ : ካለ : ጋራ : ተሰማሙ : እንጅ ::

የወንጌል : ክፍል :: ዮሐንስ : ፪፡ ፩፡—፲፩።

በሦስተኛውም : ቀን : ሰርግ : ነበረ : በቃና : በገሊላ :: የየ
ሱስም : እናት : ከዚያ : ነበረች :: የሱስም : ደቀ : መዛሙ
ርቱም : ወደ : ሰርግ : ተጸሩ :: የወይን : ጸጅም : ባለቀ : ጊ
ዜ : የየሱስ : እናት : ጸጅ : የላቸውም : አለችው :: የሱስ
ም : አላት :: ካንች : ጋራ : ምናለኝ : አንች : ሴት :: ጊዜ
ዬ : ገና : አልደረሰም :: እናቱም : ላገልጋዮች :: እርሱ :
የሚላችሁትን : ሁሉ : አድርጉ : አለች :: ከዚያም : ስድስ
ት : የደንጊያ : ጋኖች : ተቀምጠው : ነበሩ : እንደ : አይሁድ :
እንደ : ማንጻታቸው : ልማድ :: ከርሳቸውም : ኢያንዳን
ዱ : ሁለት : ማድጋ : ወይም : ሦስት : ያነሣ : ነበር :: የሱስ
ም :: ጋኖችን : ውኃ : ምልዋቸው : አላቸው :: እስከ : ላይ :
ድረስም : መልዋቸው :: አላቸውም :: አሁንም : ቅዱ : ለ
መርፈቂያም : አለቃ : ውሰዱት :: አደረሱትም :: የምር
ፋቁም : አለቃ : ያነን : ተለውጦ : ለጸጅ : የሆነውን : ው
ኃ : በቀመሰ : ጊዜ : (ከወዴትም : እንደለ : አላወቀም : አገ
ልጋዮች : ግን : ውኃ : የመሉት : ያውቁት : ነበር) :: የም
ርፋቁ : አለቃ : ሙሽራውን : ጸራ :: አለውም :: ሰው :
ሁሉ : አስቀድሞ : መልካሙን : ጸጅ : ያመጻል :: በሰከሩ
ም : ጊዜ : የዚያን : ጊዜ : የተዋረደውን :: አንተ : ግን : መ

ልካሙን ፡ ጸጅ ፡ እስካሁን ፡ ጠበቅኽ ። ይኸች ፡ ናት ፡ የተአምራት ፡ መጀመርያ ፡ የሱስ ፡ በቃና ፡ ገሊላ ፡ ያደረጋት ። ክብሩንም ፡ ገለጠ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ አመኑበት ።

---

## ሶስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከኤጲፋንያስ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ድካሜችንን ፡ በምህረት ፡ እይ ፡ በፍርሃታችንና ፡ በመከራችን ፡ በጉዳያችንም ፡ ሁሉ ፡ ቀኙ ፡ እጅህን ፡ ዘርግተህ ፡ እርዳንና ፡ ጠብቅን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ሮሜ ፡ ፲፪፡ ፲፯ — ፳፩።

በራሳችሁ ፡ ዘንድ ፡ ብልሃተኞች ፡ አትሁኑ ። ለማንም ፡ ክፉን ፡ በክፉ ፡ አትመልሱ ። መልካም ፡ ለማድረግ ፡ አስቡ ፡ እንጅ ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ። ቢቻላችሁስ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ዕርቅ ፡ ይሁንላችሁ ። ነፍሳችሁን ፡ አትበቀሉ ፡ ወዳጆቼ ፡ ሆይ ። ለቍጣ ፡ስፍራ ፡ ስጡ ፡ እንጅ ። ተጽፏልና ። በቀል ፡ ለኔ ፡ ነው ። እኔም ፡ ፍዳውን ፡ እከፍላለሁ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እንጊዴህ ፡ ጸላትኽ ፡ ቢራብ ፡ አብላው ፡ ቢጠማም ፡ አጠጣው ። ይህነን ፡ ብታደርግ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ የሳት ፡ ፍም ፡ ትሰበስባለኽና ። ክፉ ፡ አያሸንፍኽ ። ክፉውን ፡ በበጎ ፡ አሸንፍ ፡ እንጅ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፰፡ ፩ — ፲፫።

ከተራራም ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ ተከተሉት ፡ ብዙ ፡ አሕዛብ ። እነሆም ፡ ለምጻም ፡ መጥቶ ፡ ሰገደለት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። አቤቱ ፡ ብትወድስ ፡ እኔን ፡ ማንጻት ፡ ይቻልኻል ። የሱስም ፡ እጁን ፡ዘረጋ ፡ ዳሰሰውም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ወድጃለሁ ፡ ንጻ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከለምጹ ፡ ነጻ ። የሱስም ፡ አለው ። ተጠንቀቅ ፡ ለማንም ፡ አትናገር ። ነገር ፡ ግን ፡ ሒድ ፡ ራስኽን ፡ ለካህን ፡ አስይ ፡ ሙሴም ፡ ያዘዘውን ፡ ቍርባን ፡ አቅርብ ፡ ምስክር ፡ ይሆንላቸው ፡ ዘንድ ። የሱስም ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የመቶ ፡ አለቃ ፡ ወደርሱ ፡ መጣ ፡ ለምኖት ። ብሎም ፡ አቤቱ ፡ ብላቴናዬ ፡ መፃጉ ፡ ሁኖ ፡ እጅግም ፡ አሞት ፡ በቤት ፡ ተንትቷል ። የሱስም ፡ አለው ፡ እኔ ፡ መጥቼ ፡ እፈውሰዋለሁ ። የመቶ ፡ አለቃም ፡ መልሶ ፡ አለው ። አቤቱ ፡ ከሰገነቴ ፡ በታች ፡ እንድትገባ ፡ አይገባኝም ። ነገር ፡ ግን ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ በል ፡ ብላቴናዬም ፡ ይድናል ። እኔም ፡ ደግሞ ፡ የምገዛ ፡ ሰው ፡ ነኝና ፡ ከኔም ፡ በታች ፡ ጭፍራ ፡ አለኝ ። ይህነንም ፡ ሒድ ፡ እለዋለሁ ፡ ይሔድማል ፡ ሌላውንም ፡ ና ፡ እለዋለሁ ፡ ይመጣልም ። ባርያዬንም ፡ ይህነን ፡ አድርግ ፡ ብለው ፡ ያደርገዋል ። የሱስም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ተደነቀ ፡ ለሚከተሉትም ፡ አለ ። በውነት ፡ እነግራችኋለሁ ፡ በእሥራኤል ፡ እንኳ ፡ ይህነን ፡ የሚያህል ፡ ሃይማኖት ፡ አላገኘሁም ። እላችሁማለሁ ፡ ብዙ ፡ ከምሥራቅ ፡ ከምዕራብም ፡ ይመጣሉ ፡ ከአብርሃምም ፡ ከይስሐቅም ፡ ከያዕቆብም ፡ ጋራ ፡ ይረፋቃሉ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ። የመንግሥት ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ጭራሽ ፡ ጨለማ ፡ ይጣላሉ ። ልቅሶ ፡ ወደለበት ፡ ጥርስንም ፡ ማፋጨት ። የሱስም ፡ ለመቶ ፡ አለቃ ፡ አለው ፡ ሒድ ፡ እንደ ፡ ሃይማኖትኽም ፡ ይሁንልኽ ። ብላቴናውም ፡ ደነ ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ።



---

## አራተኛ ፡ እሁድ ፡ ከኤጲፋንያስ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

እግዚአብሔር ፡ ሆይ ። እኛ ፡ በብዙና ፡ በታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ እንደ ፡ ተከበብነ ፡ ስለ ፡ ባሕርያችንም ፡ ድካም ፡ ወትሮ ፡ ቀንተን ፡ ለመቆም ፡ እንደንችል ፡ አንተ ፡ አውቀሃልና ። በፍርሃት ፡ ሁሉ ፡ የሚደግፈነውን ፡ ከፈተናም ፡ ሁሉ ፡ የሚያድንነውን ፡ ኃይልና ፡ መጠበቅ ፡ ስጠነ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ሮሜ ፡ ፲፫፤ ፩፤—፯፡፡

ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለተሾሙ ፡ ሥልጣናት ፡ ይገዛ ። ሥልጣን ፡
አትገኝምና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እንጅ ። ያሉም ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተሾሙ ፡ ናቸው ። እንግዲህ ፡
በሥልጣን ፡ ላይ ፡ የሚነሣ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥርዓት ፡
ይቃወማል ። የሚቃወሙም ፡ ይፈረድባቸዋል ። ሹማም
ት ፡ በበጎ ፡ ስራ ፡ ላይ ፡ ለፍርሃት ፡ አይደሉምና ፡ በክፉ ፡
እንጅ ። መኰንኑንስ ፡ እንዳትፈራ ፡ ብትወድ ፡ መልካም ፡
አድርግ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድም ፡ ምስጋና ፡ ይሆንልኻል ። የእግ
ዚአብሔር ፡ ሎሌ ፡ ላንተ ፡ ነውና ፡ ለበጎ ። ክፉ ፡ ግን ፡ ብታ
ደርግ ፡ ፍራ ። በከንቱ ፡ ሰይፍ ፡ አይታጠቅምና ። የእግዚአ
ብሔር ፡ ሎሌ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡ ክፉ ፡ የሚያደርገ
ውን ፡ በቍጣ ፡ የሚበቀል ። ስለዚኽም ፡ በግድ ፡ መገዛት ፡
ይፈለጋል ። ስለ ፡ ቍጣው ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ስለ ፡ ልብ
ም ፡ እንጅ ። ስለዚኽ ፡ ደግሞ ፡ ግብርን ፡ ትሰጣላችሁ ። የእ
ግዚአብሔር ፡ አገልጋዮች ፡ ናቸውና ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁል
ጊዜ ፡ የሚጠብቁ ። አሁንም ፡ ለሁላቸው ፡ የሚገባቸውን ፡
ስጡ ። ግብር ፡ ለሚገባው ፡ ግብሩን ። ቀርጽም ፡ ለሚገ
ባው ፡ ቀርጹን ። ፍርሃት ፡ ለሚገባው ፡ ፍርሃቱን ። ክብር ፡
ለሚገባው ፡ ክብሩን ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፰፤ ፳፫—፴፬፡፡

ወደ ፡ ታንኳም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙሮቹ ፡ ተከተ
ሉት ። እነሆም ፡ ታላቅ ፡ መናወጥ ፡ በባሕር ፡ ሆነ ፡ መው
ጀ ፡ ታንኳውን ፡ እስኪደፍነው ፡ ድረስ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ተኝ
ቶ ፡ ነበረ ። ደቀመዛሙሮቹም ፡ ወደርሱ ፡ ቀረቡ ፡ አስነሡ
ትም ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። አቤቱ ፡ አድነን ፡ እንጠፋለንና ። አላ
ቸውም ፡ ምነው ፡ ትፈራላችሁ ፡ እላንተ ፡ ሃይመኖታችሁ ፡
የጐደለች ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተነሣ ፡ ንፋሶችንና ፡ ባሕሩንም ፡ ገ
ሠፀ ። ታላቅ ፡ ጸጥታም ፡ ሆነ ። ሰዎች ፡ ግን ፡ አደነቁ ፡ እን
ደዚህ ፡ ሲሉ ፡ ይህ ፡ ማነው ። ንፋሶችና ፡ ባሕር ፡ እንኳ ፡ ይታ
ዘዙለታልና ። ወደ ፡ ማዶም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ጌርጌሴን



ያን ፡ አገር ፡ ተቀበሉት ፡ ሁለት ፡ አጋንንት ፡ ያደረባቸው ፡ ሰዎች ፡ ከመቃብሮች ፡ ወጥተው ። እጅግም ፡ ክፉ ፡ ነበሩ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በዚያች ፡ መንገድ ፡ ማለፍ ፡ እስኪሳነው ፡ ድረስ ። እነሆም ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ካንተ ፡ ጋራ ፡ ምን ፡ አለን ፡ የሱስ ፡ ሆይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ። ወደ ዚኽ ፡ መጣኽን ፡ መከራ ፡ ልታመጣብን ፡ ጊዜው ፡ ሳይ ደርስ ። ከዚያም ፡ ከርሳቸው ፡ ርቃ ፡ የርያ ፡ ታላቅ ፡ መንጋ ፡ ትሰማራ ፡ ነበረች ። አጋንንትም ፡ ለመኑት ፡ እንዲህ ፡ ሲ ሉ ። ታወፃነስ ፡ እንደ ፡ ሆንኽ ፡ ወደ ፡ እርያ ፡ መንጋ ፡ እን ገባ ፡ ዘንድ ፡ እዘዘን ። አላቸውም ፡ ሒዱ ። እርሳቸውም ፡ ወጥተው ፡ ወደ ፡ እርያ ፡ መንጋ ፡ ሔዱ ። እነሆም ፡ የርያ ፡ መንጋ ፡ ሁሉ ፡ ከገደል ፡ አፋፍ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ወደቁ ፡ በው ኃም ፡ ሞቱ ። እረኞች ፡ ግን ፡ ሸሹ ፡ ወደ ፡ አገርም ፡ ሔዱ ፡ በነገሩም ፡ ሁሉ ፡ አወሩ ፡ አጋንንትም ፡ በነበሩባቸው ፡ ሰዎች ። እነሆም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የሱስን ፡ ለመቀበል ፡ ወ ጣች ። ባዩትም ፡ ጊዜ ፡ ካገራቸው ፡ እንዲያልፍ ፡ ለ መኑት ።

---

## አምስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከኤጲፋንያስ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

አቤቱ ፡ ማኅበርህንና ፡ ቤትህን ፡ ለዘወተር ፡ ባይነተኛ ፡ አምላኮህ ፡ እንድጠበቃት ፡ እንለምንሃለን ፡ በሰማያ ዊት ፡ ምህረትህ ፡ ተስፋ ፡ ብቻ ፡ የተደገፉ ፡ በኃይለኛ ፡ ችሎ ትህ ፡ ለዘላለም ፡ ይጠበቁ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ቆሎሰይስ ፡ ፫፤ ፲፪፤—፲፯፡፡

አሁንም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ መረጣችሁ ፡ እላንተ ፡ ቅ ዱሳን ፡ የምትሆኑ ፡ የተወደዳችሁም ። መሐረትን ፡ ልበሱ ። ርኅራኄንም ። ቸርነትንም ። ትሕትናውንም ። ገርነትንም ። ትዕግሥትንም ። እርሱ ፡ በርሳችሁም ፡ ተቻቻሉ ። እርሱ ፡

በርሳችሁም : ይቅር : ተባባሉ : ለማንም : መክሰሻ : ቢኖር : በባልንጀራው : ላይ :: ክርስቶስ : ይቅር : እንዳላችሁ : እላንተም : እንደዚሁ : ይቅር : በሉ :: በዚኽም : ነገር : ሁሉ : ላይ : ፍቅርን : ልበሱ :: እርሱ : የፍጻሜ : ማሠርያ : ነውና :: የእግዚአብሔር : ሰላምም : በልባችሁ : ይግዛ :: ወደርሱ : የተጸራችሁ : ናችሁና : ባንድ : ሥጋ :: የምታመሰግኑም : ሁኑ :: የእግዚአብሔር : ቃልም : በምላት : ይደርባችሁ :: እርሱ : በርሳችሁም : በጥበብ : ሁሉ : አስተምሩ : ለየባልንጀራችሁ : ልብም : ተናገሩ :: በመዝሙር : በምስጋናም : በመንፈሳዊት : ዝማሬም : በጸጋ : አዝምሩ : ለእግዚአብሔር : በልባችሁ :: በቃልም : በስራም : የምታደርጉት : ሁሉ : በየሱስ : ክርስቶስ ፡ በጌታችን : ስም : አድርጉት :: እግዚአብሔርንም : አብንም : በርሱ : አመስግኑ ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፲፫፤ ፳፬፤—፴።

መንግሥተ : ሰማያት : በርሻው : ላይ : መልካም : ዘር : የዘራውን : ሰውን : ትመስላለች :: ሰዎችም : በተኙ : ጊዜ : ጸላቱ : መጣ : እንክርዳድንም : በስንዴው : መኻከል : ዘርቶ : ሔደ :: ስንዴውም : በበቀለ : ጊዜ : ባፈራም : ጊዜ : የዚያን : ጊዜም : እንክርዳዱ : ታየ : ደግሞ :: የባለቤቱም : ባሮች : መጡ : አሉትም :: ጌታ : ሆይ : መልካም : ዘር : በርሻኽ : ላይ : አልዘራኽምን :: እንክርዳዱስ : ከወዴት : መጣ :: እርሱ : ግን : አላቸው :: ጸላተኛ : ሰው : ይህነን : አደረገ :: ባሮቹም : ሒደን : ብንለቅመው : ትወዳለኽን : አሉት :: እርሱ : ግን : አለ :: አይሆንም :: እንክርዳዱን : ስትለቅሙ : ስንዴውን : ከርሱ : ጋራ : እንዳትነቅሉ :: ተዋቸው : ባንድ : ይደጉ : እስከ : መከር : ድረስ :: በመከር : ዘመንም : አጫጆችን : እላለሁ :: እንክርዳዱን : ቀድማችሁ : ሰብስቡ : ኢየሸክምም : ለመቃጠል : እሠሩት :: ስንዴውን : ግን : በጎተራዬ : ክተቱ ::



ስድስተኛ : እሁድ : ከኤጲፋንያስ : በኋላ ::

ጸሎት ::

አምላክ : ሆይ : ልጅህ : የሰይጣንን : ስራ : ያፈርስ : ዘንድ : እኛንም : የእግዚአብሔርን : ልጆች : የዘላለምንም : ሕይወት : ወራሾች : ያደርገን : ዘንድ : ተገልጽዋልና :: ስጠኝ : እንለምንሃለን : ይህች : ተስፋ : ስላለችኝ : እኛ : ነፍሳችነን : እንድታነጻን : እርሱ : እንደ : ነጻ :: እርሱ : በኃይልና : በታላቅ : ምስጋና : ሲመለስ : ጊዜ : እኛም : በዘላለምና : በመሰገኒችም : መንግሥቱ : እርሱን : እንመሰል : ዘንድ : ከንተ : ጋራ : አብ : ሆይ : ካንተም : ጋራ : መንፈስ : ቅዱስ : ሆይ : ኑሮ : ወደሚገዛባት : አንድ : አምላክ : ለዘላለም :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ፩፤ ዮሐንስ : ፫፤ ፩፤—፰።

እዩ : እንዴት : ያለውን : ፍቅር : ሰጠን : አብ : የእግዚአብሔር : ልጆች : እንባል : ዘንድ :: ስለዚኽ : ዓለም : አያውቅንም : እርሱን : አላወቀምና :: ወዳጆቼ : ሆይ : እኛ : አሁን : የእግዚአብሔር : ልጆች : ነን :: ገናም : ምን : እንሆናለን : አልተገለጠም :: ነገር : ግን : እርሱ : በተገለጠ : ጊዜ : እንደርሱ : እንድንሆን : አወቅነ :: እናየዋለንና : እርሱ : እንደለ :: ይኽችም : ተስፋ : ያለቸው : ሁሉ : ራሱን : ያነጻል : እርሱም : ንጹሕ : እንደ : ሆነ :: ኃጢአትን : የሚያደርግ : ሁሉ : ሕግንም : መተላለፍ : ያደርጋል :: ኃጢአትም : እርሱ : ሕግን : መተላለፍ : ነው :: እላንተም : ያ : ኃጢአታችነን : ሊያስወግድ : እንደ : ተገለጠ : ታውቃላችሁ :: ኃጢአትም : በርሱ : የለም :: በርሱ : የሚኖር : ሁሉ : ኃጢአት : አይሰራም :: ኃጢአት : የሚሰራ : ሁሉ : አላየውም : አላወቀውምም :: ልጆቼ : ሆይ : ማንም : አያስታችሁ :: ጽድቅ : የሚያደርግ : ጻድቅ : ነው : ያም : ጻድቅ : እንደ : ሆነ :: ኃጢአትም : የሚያደርግ : እርሱ : ከሰይጣን : ነው :: ሰይጣን : ከጥንት : ኃጢአትን : አድርጓልና :: ስለዚኽ : ተገለጠ : የእግዚአብሔር : ልጅ : የሰይጣንን : ስራ : ሊሽር ::

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳፬፡ ፳፫፡—፴፩፡፡

የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ማንም ፡ እነሆ ፡ ክርስቶስ ፡ ከዚኽ ፡ ነው ፡ ወይም ፡ ከዚያ ፡ ቢላችሁ ፡ አትመኑ ፡፡ አሰተኞች ፡ ክርስቶስ ፡ አሰተኞች ፡ ነቢያትም ፡ ይነሣሉና ፡፡ ታላላቆች ፡ ምልክት ፡ ታምራትም ፡ ያደርጋሉ ፡ የተመረጹትን ፡ ስንኳ ፡ ሊያስቱ ፡ ቢቻላቸው ፡፡ እነሆ ፡ አስቀድሜ ፡ ነገርኋችሁ ፡፡ ቢልዋችሁም ፡ እነሆ ፡ በውድማ ፡ ነው ፡፡ አትውጡ ፡፡ እነሆ ፡ በቤት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቢሉ ፡፡ አትመኑ ፡፡ መብረቅ ፡ ከምሥራቅ ፡ እንደ ወጣ ፡ እስከ ፡ መዕራብም ፡ እንደ ታይ ፡ እንዲሁም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ መታየት ፡ ይሆናልና ፡፡ ጥምብም ፡ ወደለበት ፡ ከዚያ ፡ ንስር ፡ ይሰበሰባል ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከዚያ ፡ ዘመን ፡ መከራ ፡ በኋላ ፡ ጸሓዩቱ ፡ ጨለማ ፡ ትሆናለች ፡ ጨረቃውም ፡ ብርሃንዋን ፡ አትሰጥም ፡፡ ከዋክብቱም ፡ ከሰማይ ፡ ይወድቃሉ ፡፡ የሰማይም ፡ ኃይል ፡ ትናወጻለች ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምልክት ፡ በሰማይ ፡ ይታያል ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ያለቅሳሉ ፡ የምድር ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡፡ የሰው ፡ ልጅም ፡ በሰማይ ፡ ደመና ፡ ላይ ፡ ሲመጻ ፡ ያዩታል ፡ ከብዙ ፡ ኃይልና ፡ ምስጋና ፡ ጋራ ፡፡ መላእክቱንም ፡ ይልካል ፡ ከታላቁ ፡ ከመለከት ፡ ድምፅ ፡ ጋራ ፡፡ ለርሱ ፡ የተመረጹትንም ፡ ካራቱ ፡ ንፋሳት ፡ ያከማቻሉ ፡ ከሰማይ ፡ ዳር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ደርዋ ፡ ድረስ ፡፡

ሶስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከጾም ፡ አርባ ፡ በፊት ፡፡

ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ የሕዝብህን ፡ ልመና ፡ በሞገስ ፡ እንድትሰማ ፡ እንለምንሃለን ፡፡ እኛ ፡ በኃጢአታችን ፡ መክንያት ፡ መቀሠፍት ፡ በቅን ፡ የሚገባነ ፡ በቸርነትህና ፡ በምህረትህ ፡ ስለ ፡ ስምህም ፡ ምስጋና ፡ እንድን ፡ ዘንድ ፡፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ የሚገዛም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፱፡ ፳፬፡—፳፯፡፡

አታውቁምን ፡ የመቀደደምን ፡ ሩጫ ፡ የሚሮጡ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሮጡ ፡፡ የማሸነፏን ፡ ዋጋ ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ብቻ ፡ ያገኛል ፡፡ እላንትም ፡ እንደዪህ ፡ ሩጡ ፡ እንድታገኙት ፡፡ የሚጋደልም ፡ ሁሉ ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ አቅሞውን ፡ ይጠብቃል ፡፡ እሌህም ፡ የሚጠፋውን ፡ አክሊል ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡፡ እኛ ፡ ግን ፡ የማይጠፋውን ፡፡ እንጊዲህ ፡ እኔ ፡ እንደዪህ ፡ እሮጣለሁ ፡ ላልታወቀ ፡ ነገር ፡ እንደሚሮጥ ፡ እንዳልሆን ፡፡ እንዲሁም ፡ እታግላለሁ ፡ ንፋስን ፡ እንደሚመታ ፡ እንዳልሆን ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሥጋዬን ፡ እጥብቄ ፡ እይዘዋለሁ ፡ አስገዛውማለሁ ፡፡ ሌሎችን ፡ አስተምሬ ፡ እኔ ፡ ለራሴ ፡ የተጣልሁ ፡ እንዳልሆን ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳፡ ፩—፲፮፡፡

መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ባለቤትን ፡ ሰው ፡ ትመስላለች ፡ ማልደ ፡ የወጣውን ፡ ሰራተኞችን ፡ ለወይን ፡ አታክልቱ ፡ ሊሰማማ ፡፡ ሰራተኞችንም ፡ በዲናር ፡ ለቀን ፡ ተሰማማ ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ አታክልቱም ፡ ሰደዳቸው ፡፡ በሶስተኛ ፡ ሰዓትም ፡ ወጣ ፡ ሌሎችንም ፡ ተግባር ፡ ፈተው ፡ በገቢያ ፡ ቁመው ፡ አየ ፡፡ እሊያንም ፡ እላንትም ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ አታክልት ፡ ሒዱ ፡፡ እኔም ፡ የሚገባችሁን ፡ እሰጣችኋለሁ ፡ አላቸው ፡፡ እርሳቸውም ፡ ሔዱ ፡፡ ደግሞም ፡ ወጣ ፡ በስድስተኛና ፡ በዘጠነኛ ፡ ሰዓት ፡ እንዲሁም ፡ አደረገ ፡፡ ባሥራ ፡ አንደኛ ፡ ሰዓትም ፡ ወጣ ፡ ሌሎችንም ፡ ቁመው ፡ አገኘ ፡ ተግባር ፡ ፈተው ፡፡ አላቸውም ፡ ምን ፡ ሁናችሁ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ተግባር ፡ ፈታችሁ ፡ ከዚኽ ፡ ቁማችኋል ፡፡ እርሳቸውም ፡ ማንም ፡ የተሰማማነውን ፡ አጥተን ፡ አሉት ፡፡ እርሱም ፡ አላቸው ፡፡ እላንትም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ አታክልት ፡ ሒዱ ፡ የሚገባችሁንም ፡ ትወስዳላችሁ ፡፡ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ የወይን ፡ አታክልት ፡ ባለቤት ፡ መጋቢውን ፡ አለ ፡፡ ሰራተኞችን ፡ጥራ ፡ ደመወዛቸውንም ፡ ስጣቸው ፡ ከኋለኞች ፡ ጀምረኽ ፡ እስከ ፡ ፊተኞች ፡ ድረስ ፡፡ ባሥራ ፡ አንደኛዪቱ ፡ ሰዓትም ፡ የተሰማማቸው ፡ በመጹ ፡ ጊዜ ፡ ኢየራሳቸው ፡ ዲናርን ፡ ወሰዱ ፡፡

የፊተኞችም ፡ በመጹ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ የሚወስዱ ፡ መሰላቸው ፡፡ እርሳቸውም ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ኢየሬሳቸው ፡ ዲናርን ፡ ወሰዱ ፡፡ ከወሰዱም ፡ በኋላ ፡ በባለቤቱ ፡ አንጐረጐሩ ፡ እንደዩህ ፡ ሲሉ ፡፡ እለዚኽ ፡ የኋለኞቹ ፡ አንዲት ፡ ሰዓት ፡ ሰሩ ፡ ከኛ ፡ ጋራም ፡ አስተካከልኻቸው ፡ እኛ ፡ የቀኑን ፡ ክብድና ፡ ትኵሳት ፡ የተሸከምነ ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ መለሰ ፡ ከርሳቸውም ፡ አንዱን ፡ አለ ፡፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ አልበደልሁኽም ፡፡ ባንድ ፡ ዲናር ፡ አልተሰማማኸኝምን ፡፡ ገንዘብኽን ፡ ይዘኽ ፡ ሒድ ፡፡ እኔ ፡ ለዚህም ፡ ለኋለኛው ፡ እንደንተ ፡ እሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ወድጀለሁና ፡፡ ወይስ ፡ በከብቴ ፡ የወደድሁትን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አይገባኝምን ፡፡ ወይስ ፡ ዓይንኽን ፡ ምቀኛ ፡ ናት ፡ እኔ ፡ ቸር ፡ ነኝና ፡፡ እንዲህ ፡ የኋለኞች ፡ የፊተኞች ፡ ይሆናሉ ፡ የፊተኞችም ፡ የኋለኞች ፡፡ የተጸሩ ፡ ብዙ ፡ ናቸውና ፡ የተመረጹ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡፡

ሁለተኛ ፡ እሁድ ፡ ከጾም ፡ አርባ ፡ በፊት ፡፡

ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ባንደች ፡ እኛ ፡ በምናደርገው ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ እንደንታመን ፡ አይተሃልና ፡፡ በኃይልህ ፡ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ እንጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ውደድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፪፡ ቆሮንቶስ ፡ ፲፩፡ ፲፱፡—፴፩፡፡

እላንተ ፡ ብልሆተኞች ፡ ስትሆኑ ፡ ሰነፎችን ፡ ትታገሡ ፡ ዘንድ ፡ ትወዷላችሁና ፡፡ ማንም ፡ ቢገዛችሁ ፡፡ ማንም ፡ ቢበላችሁ ፡፡ ማንም ፡ ከብታችሁን ፡ ቢወስድባችሁ ፡፡ ማንም ፡ ቢኰራባችሁ ፡፡ ማንም ፡ ፊታችሁን ፡ ቢጸፋችሁ ፡ ትታገሣላችሁና ፡፡ እኔም ፡ ይህነን ፡ እንደ ፡ ኀፍረት ፡ እላለሁ ፡ እኛ ፡ እንደ ፡ ደከምነ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ማንም ፡ በሚደፍርበቱ ፡ (በስንፍና ፡ እናገራለሁ) ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እደፍርበታለሁ ፡፡ ዕብራውያንን ፡ ናቸው ፡፡ እኔም ፡ እንዲሁ ፡ ነኝ ፡፡ የእሥራኤል ፡ ወገንን ፡ ናቸው ፡፡ እኔም ፡ ደግሞ ፡፡ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ናቸውን ፡፡ እኔም ፡ ደግሞ ፡፡ የክርስቶስ ፡ አገልጋዮች ፡ ናቸውን ፡፡ (በስንፍና ፡ እናገራላሁ ፡፡) እኔ ፡ እበልጣለሁ ፡፡ በድካም ፡ ብዝቼ ፡፡ በመመታትም ፡ መልቼ ፡ በመታሠርም ፡ አትርፌ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ሞትም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡፡ ከአይሁድ ፡ አምስት ፡ ጊዜ ፡ ተገረፍሁ ፡ አርባ ፡ ግርፋት ፡ አንድ ፡ ጐድሎ ፡፡ በበትር ፡ ተመታሁ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተወገርሁ ፡፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ የነበርሁባት ፡ መርከብ ፡ ተሰበረች ፡፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ በባሕር ፡ ጥልቅ ፡ ተቀመጥሁ ፡፡ በመንገድ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡፡ በውኃ ፡ ፍርሃትም ፡፡ በወንበዶች ፡ ፍርሃትም ፡፡ በዘመዶቼ ፡ ፍርሃትም ፡፡ በአሕዛብ ፡ ፍርሃትም ፡፡ ባገርም ፡ በፍርሃት ፡፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ በፍርሃት ፡፡ በባሕርም ፡ በፍርሃት ፡፡ ባሰተኞች ፡ ወንድሞችም ፡ በፍርሃት ፡፡ በድካምና ፡ በችጋር ፡፡ በትጋት ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡፡ በራብ ፡ በጥማትም ፡፡ በጾምም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡፡ በብርድና ፡ በራቁትነት ፡፡ ሜደዊ ፡ ነገርም ፡ ሳይቈጠር ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ የምትኖርብኝ ፡ ያብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ሁሉ ፡ ትካዜ ፡ ናት ፡፡ ማነው ፡ የሚደክም ፡ እኔም ፡ ላልደክምን ፡፡ ማነው ፡ የሚሰናከል ፡ እኔም ፡ ላልቃጠልን ፡፡ ትምክሕትስ ፡ ደገባ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በድካሜ ፡ እመካለሁ ፡፡ ለዘላለም ፡ የተባረከ ፡ እግዚአብሔር ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ የጌታችን ፡ አባት ፡ አሰት ፡ እንደልናገር ፡ ያውቃል ፡፡



የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ሉቃስ ፡ ፰፡ ፬፡—፲፭፡፡

ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ ወደርሱ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ካገርም ፡ ሁሉ ፡ ወደርሱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡፡ በምሳሌ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡፡ ዘሪ ፡ ዘሩን ፡ ለመዝራት ፡ ወጣ ፡፡ እርሱም ፡ ሲዘራ ፡ ከርሱ ፡ በመንገድ ፡ አጠገብ ፡ የወደቀ ፡ አለ ፡፡ ተረገጠም ፡ የሰማይ ፡ ዎፍም ፡ በላው ፡፡ ሌላውም ፡ በደንጊያ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡፡ በበቀለም ፡ ጊዜ ፡ ደረቀ ፡፡ እርጥበት ፡ የለውምና ፡፡ ሌላውም ፡ በሾኽ ፡ ማኽል ፡ ወደቀ ፡፡ እሾኽም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ በቀለና ፡ አነቀው ፡፡ ሌላውም ፡ በመልካም ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡፡

በበቀለም ፡ ጊዜ ፡ መቶ ፡ ዕፅፍ ፡ አፈራ ። ይህንንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ጸራ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ሰሚ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ይስማ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ጠየቁት ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ይህ ፡ ምሳሌ ፡ ማለቱ ፡ ምንድር ፡ ነው ። እርሱም ፡ አለ ። ለላንት ፡ ተሰጠ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የመንግሥቱን ፡ ምሥጢር ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ። ለቀሬት ፡ ግን ፡ በምሳሌ ። ሲያዩ ፡ እንዳያዩ ፡ ሲሰሙም ፡ እንዳያስተውሉ ። ምሳሌው ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ነው ። ዘሩ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ነው ። በመንገድ ፡ አጠገብም ፡ ያሉ ፡ እርሳቸው ፡ የሚሰሙ ፡ ናቸው ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ዲያብሎስ ፡ ይመጣል ፡ ቃልንም ፡ ከልባቸው ፡ ዘንድ ፡ ይወስዳል ፡ አምነው ፡ እንዳይድኑ ። በደንጊያ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ የተዘሩ ፡ እርሳቸውም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ቃልን ፡ በደስታ ፡ ይቀበሉታል ። እሌሁም ፡ ሥር ፡ የላቸውም ። ለጊዜውም ፡ ያምናሉ ፡ በፈተና ፡ ጊዜም ፡ ይክዳሉ ። በሾኽም ፡ የወደቀ ፡ እሌኽም ፡ የሚሰሙ ፡ ናቸው ። በትካዜም ፡ በባለጠግነትም ፡ በዚች ፡ ሕይወትም ፡ ደስታ ፡ ተመላልሰው ፡ ይታነቃሉ ። ፍሬንም ፡ አያበስሉም ። በመልካም ፡ ምድር ፡ ግን ፡ የወደቀ ፡ እርሳቸው ፡ ናቸው ፡ ቃልን ፡ ሰምተው ፡ በየዋህና ፡ በበጎ ፡ ልብ ፡ የሚጠብቁት ፡ ፍሬንም ፡ በትዕግሥት ፡ የሚያፈሩ ።

---

## ጾም ፡ አርባውን ፡ የሚቀድም ፡ እሁድ ።

### ጸሎት ።

አቤቱ ፡ ስራችን ፡ ሁሉ ፡ ፍቅር ፡ ባይኖር ፡ አንዳች ፡ እንዳይጠቅመን ፡ አስተምረህናልና ። መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ስደድልን ፡ ከሁሉም ፡ የተሻለውን ፡ የፍቅርን ፡ ስጦታ ፡ በልባችን ፡ አፍስስ ፡ እርሱ ፡ የሰላምና ፡ የበጐነት ፡ ሁሉ ፡ ማሠርያ ፡ ነውና ፡ ያለርሱም ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ምውት ፡ ሁኖ ፡ በፊትህ ፡ ይቈጠራል ። ይህንን ፡ ስጠኝ ፡ ባንድ ፡ ልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መክንያት ። አሜን ።



### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፤ ቆሮንቶስ ፡ ፲፫፤ ፩፤—፲፫።

በሰዎችና ፡ በመላእክት ፡ ቋንቋ ፡ ብናገር ፡ ፍቅርም ፡ ባትኖርልኝ ። እንደሚጮህ ፡ ናስ ፡ ሆንሁ ። ወይም ፡ እንደሚሰማ ፡ ጸንጸል ። ትንቢትም ፡ ብትኖርልኝ ፡ ምሥጢርንም ፡ ሁሉ ፡ ባውቅ ፡ ዕውቀትንም ፡ ሁሉ ። ሃይማኖትም ፡ ሁሉ ፡ ብትኖርልኝ ፡ ተራራ ፡ እስካፈልስ ፡ ድረስ ። ፍቅርም ፡ ከሌለችኝ ። አንዳችም ፡ አይደለሁም ። ለድኆችም ፡ ገንዘቤን ፡ ሁሉ ፡ ባበላ ። ሥጋዬንም ፡ በሳት ፡ ለመቃጠል ፡ ብሰጥ ። ፍቅርም ፡ ከሌለችኝ ። ያ ፡ ምንም ፡ አይረባኝም ። ፍቅር ፡ ለቍጣ ፡ ትዘገያለች ፡ ቸርም ፡ ናት ። ፍቅር ፡ አትቀናም ። ፍቅር ፡ አትኰራም ። አትነፋም ። ፈትዋን ፡ አታጠቍርም ። ገንዘብዋን ፡ አትሻም ። ቶሎ ፡ አትቈጣም ። ለክፉ ፡ አታስብም ። በግፍም ፡ ደስ ፡ አይላትም ። በውነት ፡ ደስ ፡ ይላታል ፡ እንጂ ። ሁሉን ፡ ትችላለች ። ሁሉንም ፡ ታምናለች ። ሁሉንም ፡ ተስፋ ፡ ታደርጋለች ። ሁሉን ፡ ትታገሣለች ። ፍቅር ፡ ከቶ ፡ አትወድቅም ። ትንቢት ፡ ታልፈለችና ። ቋንቋም ፡ ትቀራለች ። ዕውቀትም ፡ ትጠፋለች ። ከውቀት ፡ ከፍለን ፡ እናውቃለንና ። ከትንቢቱም ፡ ከፍለን ፡ እንናገራለን ። ፍጹም ፡ ግን ፡ የሚሆን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ በክፍል ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ። ሕፃን ፡ በነበርሁ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሕፃን ፡ እናገር ፡ ነበርሁ ። እንደ ፡ ሕፃንም ፡ አውቅ ፡ ነበርሁ ። እንደ ፡ ሕፃንም ፡ አስብ ፡ ነበርሁ ። ጕልማሳ ፡ ግን ፡ በሆንሁ ፡ ጊዜ ፡ የሕፃኑን ፡ ነገር ፡ ሻርሁ ። ዛሬስ ፡ የተሰወረ ፡ ነገር ፡ በማስተዋት ፡ እንደሚታይ ፡ እኛ ፡ እናያለንና ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እናያለን ። ዛሬስ ፡ ከውቀቱ ፡ ከፍዬ ፡ አውቃለሁ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ አውቃለሁ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ታወቅሁ ። አሁንም ፡ ትኖራለች ፡ ሃይማኖት ። ተስፋም ። ፍቅርም ። እሌኽ ፡ ሦስቱ ። ከሌኽ ፡ ግን ፡ የምትበልጥ ፡ ፍቅር ፡ ናት ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፰፤ ፴፩፤—፵፫።

አሥራ ፡ ሁለቱንም ፡ ወሰደ ፡ አላቸውም ። እነሆ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ እንወጣለን ። በነቢያትም ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡

የተጸፈ : ሁሉ : ይፈጸማል :: አሳልፈው : ለአሕዛብ : ይሰ
ጡታልና :: ያፌዙበትማል :: ይሰድቡማል :: ይተፉበትማል ::
ይገርፉትማል : ይገሉትማል :: በሶስተኛውም : ቀን : ይነሣ
ል :: እርሳቸው : ግን : ከዚኽ : ነገር : ምንም : አላወቁም ::
ይኽ : ነገርም : ከርሳቸው : ተሠውሮ : ነበር : የተባለውን
ም : አያውቁም : ነበሩ :: ወደ : ኢያሪኮም : በቀረበ : ጊዜ ::
እነሆ : አንድ : ዕውር : ተቀምጦ : ነበረ : በመንገድ : አጠ
ገብ : ሲለምን :: ሕዝብም : ሲያልፍ : ሰማ :: ይኽም : ም
ንድር : ነው : ብሎ : ጠየቀ :: ነገሩትም : የሱስ : የናዝሬቱ :
እንደ : ያልፍ :: እርሱም : ጮኸ : እንዲህ : ሲል :: የሱስ : የዳ
ዊት : ልጅ : ማረኝ :: በፊትም : የነበሩ : ተቃዩሙት : ዝም :
ሊበል : ብለው :: እርሱ : ግን : ጮኸቱን : አበዛ :: የዳዊት :
ልጅ : ሆይ : ማረኝ : ሲል :: የሱስም : ቆመ : ወደርሱም :
ያመጡት : ዘንድ : አዘዘ :: ወደርሱም : በቀረበ : ጊዜ : ጠየ
ቀው : እንዲህ : ሲል :: ምን : ትሻለኽ : አደርግልኽ : ዘንድ ::
እርሱም : አለ :: አቤቱ : አይ : ዘንድ :: የሱስም : አለው ::
እይ :: ሃይማኖትኽ : አዳነችኽ :: የዚያን : ጊዜውም : አየ ::
እግዚአብሔርንም : ኢያመሰገነ : ተከተለው :: ሕዝቡም :
ሁሉ : አይተው : እግዚአብሔርን : አመሰገኑ ::

የጾም : አርባ : መጀመርያ : ቀን ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ :: አንተ : ከፈ
ጠርሀው : ፍጥረት : ሁሉ : አንዳችን : የማትጸላ : ንስሐ
ም : ለሚገቡ : ሁሉ : ኃጢአታቸውን : ይቅር : የምትላቸው :
አዲስና : የተደቀሰውን : ልብ : በውሥጣችን : ፍጠርልን :
እኛ : እንደሚገባን : በኃጢአታችን : መክንያት : አልቅ
ሰን : ጕስቍልናችንንም : ተናዝዘን : ካንተ : ከምህረት :
ሁሉ : አምላክ : ዘንድ : ፍጽምትን : ይቅርታና : ስርየት :
እንቀበል : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን :

* ይህች : ጸሎት : ከየዕለት : ጸሎት : ጋራ : በጾም :
አርባ : ዕለት : ዕለት : ትደገም ::



በመልእክት : ፈንታ :: ዮኤል : ፪ ፲፪ — ፲፯ ::

አሁንም : ወደኔ : ተመለሱ : ይላል : እግዚአብሔር : በፍ
ጹም : ልባችሁ : በጾምና : በልቅሶ : ባዘንም :: ልባችሁ
ንም : ቅደዱ : ልብሳችሁንም : አይደለም :: ወደ : እግዚ
አብሔርም : ወደምላካችሁ : ተመለሱ :: እርሱ : ሩሩ :
ነውና : ይቅር : ባይም :: ለቍጣም : የዘገየ : ምሕረቱም :
የበዛች : በክፉም : ያዝናል :: ይመለስ : እንደ : ሆን : ያዝ
ንም : እንደሆን : ማን : ያውቃል : የመሥዋዕትና : የመር
ጨትንም : በረከት : ለእግዚአብሔር : ላምላካችሁ : በኋ
ላው : ያተርፋል :: በመለከት : ንፉ : በጽዮን :: ጾምን : ቀ
ድሱ : ጉባዔንም : ጽሩ :: ሕዝቡንም : ሰብስቡ : ማኅበሩ
ንም : ቀድሱ :: ሽማግሎችንም : ሰብስቡ : ሕፃናቱንም :
አከማቹ : ጡትም : የሚጠቡትን :: ሙሽሪው : ከቤቱ :
ይውጣ : ሙሽሪዪቱም : ከመኖርያዋ :: ካህናትም : የእግ
ዚአብሔር : አገልጋዮች : በደጀና : በመሠውያው : መኻ
ከል : ያልቅሱ :: ይበሉም : አዘን : አቤቱ : ለሕዝብኽ : ርስ
ትኽንም : ለመለገድ : አሳልፈኽ : አትስጥ : አሕዛብ :
ይገዝዋቸው : ዘንድ :: ስለ : ምን : ይላሉ : በአሕዛብ : አ
ምላካቸው : ወዴት : ነው ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፮ ፲፮ — ፳፬ ::

በጾማችሁም : ጊዜ : አትጸውልጉ : እንደ : ግብዞች :: እርሳ
ቸው : ይጸወልጋሉና : ፊታቸውንም : ይለውጣሉና : ለሰዎ
ች : እንደ : ጾሙ : ሊታዩ :: እውነት : እነግራችኋለሁ : ዋ
ጋቸውን : እንደ : ተቀበሉ :: አንተ : ግን : በጾምኽ : ጊዜ :
ራስኽን : ቀባ : ፊትኽንም : ታፀብ :: ለሰው : እንደትታ
ይ : ጾመኛ : መስለኽ : ነገር : ግን : ላባትኽ : በስውር :
ለሚያይ :: በስውርም : የሚያይ : አባትኽ : በግልጽ : ይከ
ፍልኻል :: መዝገብን : አትሰብስቡላችሁ : በምድር : ላ
ይ :: ትል : ወደሚበላው : ነቀዝም : ወደሚያነቅዘው : ሌ
ቦችም : ነድለው : ወደሚሰርቁት :: ነገር : ግን : መዝገብን :
ሰብስቡላችሁ : በሰማይ :: ትል : ወደማይበላው : ነቀዝ

ም ፡ ወደማያነቅዘው ፡ ሌቦችም ፡ ነድለው ፡ ወደማይሰርቁ ት ፡፡ መዝገባችሁ ፡ ወደለበት ፡ ልባችሁም ፡ ከዚያ ፡ ይሆና ልና ፡፡

---

## የጾም ፡ አርባ ፡ መጀመርያ ፡ እሁድ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ አንተ ፡ በኛ ፡ ፈንታ ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊ ት ፡ ጾመሃልና ፡፡ ፍጥረትህን ፡ በመርባት ፡ አንደዬህ ፡ አቅናን ፡ ሥጋችን ፡ ለመንፈስ ፡ እንዲገዛ ፡ እኛም ፡ ባይነተኛ ፡ ጽድ ቅና ፡ በቅድስና ፡ ለበጎ ፡ ፈቃድህ ፡ እንድንታዘዝ ፡ አንተን ፡ እናከብር ፡ እናመሰግንህም ፡ ዘንድ ፡ ከአብና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ የምትኖር ፡ የምትገዛም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፪፡ ቆሮንቶስ ፡ ፮፡ ፩፡—፲፡፡

እኛም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ሰርተናልና ፡ እንለምናችኋለን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ በከንቱ ፡ እንዳትቀበሉ ፡፡ ይላልና ፡፡ በደህና ፡ ጊዜ ፡ ሰማሁኽ ፡፡ በመድኃኒትም ፡ ቀን ፡ ረደሁኽ ፡፡ እነሆ ፡ ዛሬ ፡ ነው ፡ ያ ፡ ደህና ፡ ጊዜ ፡፡ እነሆ ፡ ዛሬ ፡ ነው ፡ የመ ድኃኒቱ ፡ ቀን ፡፡ በማንም ፡ ማሰናከልን ፡ አናደርግ ፡ ባገ ዷች ፡ ከቶ ፡፡ መልእክታችን ፡ እንዳትነወር ፡፡ በነገሩ ፡ ሁሉ ፡ ራሳችንን ፡ እንገለጽ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሎላ ልት ፡፡ በብዙ ፡ ትዕግሥት ፡፡ በኃዘንም ፡፡ በመከራም ፡፡ በ መጨነቅም ፡፡ በመመታትም ፡፡ በግዞትም ፡፡ በሁከትም ፡፡ በድካምም ፡፡ በትጋትም ፡፡ በጾምም ፡፡ በንጽሕናም ፡፡ በውቀትም ፡፡ በርኅራኄም ፡፡ በቸርነትም ፡፡ በመንፈስ ፡ ቅዱ ስም ፡፡ ያለ ፡ ግብዝናም ፡ ባለ ፡ መውደድ ፡፡ በውነት ፡ ነገ ርም ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ኃይልም ፡፡ የጽድቅን ፡ እቃ ፡ ጦር ፡ ለብሰን ፡ በቀኝና ፡ በግራ ፡፡ በክብርም ፡ በአፈረትም ፡፡ በጎ ችም ፡ ተብለን ፡ ክፎችም ፡ ተብለን ፡፡ እንደ ፡ አሳቾች ፡ እኛ ፡ እውነተኞች ፡ ስንሆን ፡፡ እንደማንታወቅ ፡ እኛ ፡ በ ጣም ፡ ስንታወቅ ፡፡ እንደ ፡ ምዋቾችም ፡ እነሆም ፡ ሕያዋ ን ፡ ነን ፡፡ እንደምንሣቀይም ፡ ያልሞትነ ፡፡ እንደምናዝን ፡



ሁለግዜም ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡፡ እንደ ፡ ድኆችም ፡ ብዙ ፡ ሰዎ ችን ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ ስናደርግ ፡፡ እንደችም ፡ እንደ ፡ ሌለነ ፡ እኛ ፡ ሁሉን ፡ ስንገዛ ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፬፡ ፩፡—፲፩፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ የሱስ ፡ በመንፈስ ፡ ተደዞ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጣ ፡ ከዲያብሎስ ፡ ሊፈተን ፡፡ አርብዓ ፡ መዐል ትም ፡ አርብዓ ፡ ሌሊትም ፡ ከጾመ ፡ በኋላ ፡ ተራበ ፡፡ ፈታ ኝም ፡ መጣበት ፡ አለውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅስ ፡ እ ንደ ፡ ሆንኽ ፡ በል ፡ እሌኽ ፡ ደንጎች ፡ እንጀራ ፡ እንዲሆኑ ፡፡ እርሱም ፡ መለሰለት ፡ አለም ፡፡ ሰው ፡ በንጀራ ፡ ብቻ ፡ አይኖርም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ በምትወጣው ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ እንጂ ፡ ተብሎ ፡ ተጻፈ ፡፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዲያ ብሎስ ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ አገር ፡ ወሰደው ፡ በቤተ ፡ መቅደ ስም ፡ ቀጸላ ፡ ላይ ፡ አቆመው ፡፡ አለውም ፡ የእግዚአብ ሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆንኽ ፡ ሰውነትኽን ፡ ጣል ፡ ወደ ፡ ታች ፡፡ መልክተኞቹን ፡ ስላንተ ፡ እንዲያዝ ፡ ተጽፎዋልና ፡፡ በጆቸውም ፡ ያነሡኻል ፡ እግርኽ ፡ በደንጊያ ፡ እንዳትሰና ከል ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡ ደግሞ ፡ ተጽፎዋል ፡ አምላክ ኽን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አትፈታተነው ፡ ሲል ፡ ደግሞም ፡ ዲያብሎስ ፡ ይዞት ፡ እጅግ ፡ በረጅመ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ አስ ቀመጠው ፡ የዓለምንም ፡ ሁሉ ፡ መንግሥታት ፡ ክብራቸው ንም ፡ አሳየው ፡፡ አለውም ፡፡ ይህነን ፡ ሁሉ ፡ እሰጥኻለሁ ፡ ለኔ ፡ ሰግደኽ ፡ ብትወድቅ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አለው ፡ የሱ ስ ፡፡ ከኔ ፡ ራቅ ፡ አንተ ፡ ሰይጣን ፡፡ ተጽፎዋልና ፡ ለእግዚአብ ሔር ፡ ለአምላክኽ ፡ስገድ ፡ እርሱንም ፡ ብቻውን ፡ አምል ክ ፡፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ዲያብሎስ ፡ ተወው ፡፡ መላእክ ትም ፡ እነሆ ፡ መጡ ፡ ለርሱም ፡ አገለገሉ ፡፡

---

## የጾም ፡ አርባ ፡ ሁለተኛ ፡ እሁድ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ከነፍሳችን ፡ ራሳችንን ፡ ለመርዳት ፡ ኃይል ፡ እንደጣነ ፡ አይተሃልና ፡፡ አንተ ፡ በሜ

ደችን ፡ በሥጋችን ፡ በውሥጣችንም ፡ በነፍሳችን ፡ ጠብቀን ፡ እኛ ፡ በሥጋ ፡ ላይ ፡ ከሚመጣ ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ በነፍስም ፡ ላይ ፡ ከሚወድቅ ፡ ነፍስንም ፡ ከሚጐዳ ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ተረድተን ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ተሰሎንቄ ፡ ፬፡ ፩፡—፰።

አሁንም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ እንለምናችኋለን ፡ በጌታ ፡ በየሱስም ፡ እንመክራችኋለን ፡ ከኛ ፡ እንደ ፡ ተቀበላችሁ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ ትሔዱ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ደስ ፡ ታሰኙ ፡ ዘንድ ፡ በዚያው ፡ ብዙ ። በጌታ ፡ በየሱስ ፡ የሰጠናችኋቸውን ፡ ትእዛዛት ፡ ታውቃላችሁና ። ይኸ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ነውና ፡ እርሱም ፡ መቀደሳችሁ ። ከዝሙት ፡ ትርቁ ፡ ዘንድ ። ሁሉም ፡ ኢያንዳንዳችሁ ፡ እቃውን ፡ በመቀደስና ፡ በክብር ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ ሊያውቅ ። በዝሙት ፡ ሕማምም ፡ አይደለም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንደማያውቁ ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ። ማንምም ፡ ወንድሙን ፡ እንዳያታለው ፡ ባንዳችም ፡ ግፍ ፡ እንዳያደርግበት ። እግዚአብሔር ፡ በዚኸ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይበቀላልና ። ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ነገርናችሁ ፡ እንደ ፡ መሰከርነም ። እግዚአብሔር ፡ ለርኵሰት ፡ አልጸራነምና ። ለቅድስና ፡ እንጂ ። ስለዚኽም ፡ የማይታዘዝ ፡ ለሰው ፡ የማይታዘዝ ፡ አይደለም ። ለእግዚአብሔር ፡ እንጂ ፡ ቅዱስ ፡ መንፈሱን ፡ ለላንት ፡ ለሰጠው ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፲፭፡ ፳፩፡—፳፰።

የሱስም ፡ ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ጢሮስና ፡ ወደ ፡ ሲዶና ፡ አገር ፡ ሔደ ። እነሆም ፡ የከነዓን ፡ ሴት ፡ ከዚያች ፡ ምድር ፡ ወጣች ፡ ስትጮኽ ፡ እንደዪህም ፡ ስትል ። ማረኝ ፡ አቤቱ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ። ልጄ ፡ በክፉ ፡ ጋኔን ፡ ተይዛለችና ። እርሱ ፡ ግን ፡ አንዳችን ፡ አልመለሰላትም ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ መጡ ፡ ለመኑትም ፡ እንደዪህም ፡ አሉት ። አሰናብታት ፡ በኋላችን ፡ ትጮኻለችና ። እርሱም ፡ መለ



ሰ ፡ አላቸውም ። አልተላክሁም ፡ ወደ ፡ ጠፉ ፡ በጎች ፡ ከእሥራኤል ፡ ቤት ፡ እንጅ ። እርስዋ ፡ ግን ፡ መጣችና ፡ ሰገደችለት ፡ እንደዪህ ፡ ስትል ። አቤቱ ፡ እርዳኝ ። እርሱ ፡ ግን ፡ መለሰ ፡ እንደዪህ ፡ ሲል ። መልካም ፡ አይደለውም ፡ የልጆችን ፡ እንጀራ ፡ ነሥተህ ፡ ለውሾች ፡ መስጠት ። እርስዋም ፡ አለች ። አዎን ፡ አቤቱ ፡ ውሾችም ፡ ደግሞ ፡ ከጌቶቻቸው ፡ ማዕድ ፡ ከወደቀ ፡ ፍርፋሪ ፡ ይበላሉ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ መለሰ ፡ የሱስ ፡ አላትም ። አንች ፡ ሴት ፡ ሃይማኖትሽ ፡ ታላቅ ፡ ናት ። እንደ ፡ ወደድሽ ፡ ይሁንልሽ ። ልጅዋም ፡ ዳነች ፡ ከዚያች ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ።

የጾም ፡ አርባ ፡ ሶስተኛ ፡ እሁድ ።

ጸሎት ።

እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የተዋረድነውን ፡ ባሮችህ ፡ የልባችነን ፡ ፈቃድ ፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ የግርማህንም ፡ ቀኝ ፡ እጅህ ፡ ዘርግተህ ፡ በጸላቶቻችን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ መጸጀችን ፡ ትሆንልን ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፭፡ ፩፡—፲፬።

እንጊዲህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ምሰሉ ፡ እንደ ፡ ተወደዱ ፡ ልጆች ። በፍቅርም ፡ ተመላለሱ ፡ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ወደደነ ፡ ራሱንም ፡ ስለኛ ፡ አሳልፎ ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ ቍርባን ፡ መሥዋዕትም ፡ አድርጎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መዐዛው ፡ ያማረ ፡ ሽቱ ። ዝሙትና ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ስስትም ፡ ከቶ ፡ አይሰማባችሁ ። ለቅዱሳን ፡ እንደሚገባ ። እንዲሁም ፡ ነውረኛ ፡ ነገር ፡ የስንፍና ፡ ነገርም ፡ የማይገባ ፡ ዋዛም ። ስብሐት ፡ እንጅ ። ይህነን ፡ አውቃችኋልና ። አመንዝራ ፡ ቢሆን ፡ ርኩስም ፡ ቢሆን ፡ ባለመግነትንም ፡ የሚወድ ፡ ቢሆን ፡ እርሱም ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልክ ። ለሌህ ፡ ሁሉ ፡ ርስት ፡ የላቸውም ፡ በክርስቶስና ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ። ማንም ፡ አያታላችሁ ፡ በምናምን ፡ ነገር ። ስለዚህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡

ይመጣልና ፡ በማይታዘዙ ፡ ልጆች ፡ ላይ ። ባልንጀሮችም ፡ ኢትሁንዋቸው ። ቀድሞ ፡ ጨለማ ፡ ነበራችሁና ። ዛሬ ፡ ግን ፡ ብርሃን ፡ ናችሁ ፡ በጌታው ። እንደ ፡ ብርሃን ፡ ልጆች ፡ ተመላለሱ ። የመንፈስ ፡ ፍሬ ፡ በበጐነት ፡ ሁሉ ፡ በጽድቅም ፡ በውነትም ፡ ነውና ፡ መርምራችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ስራ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ። ፍሬ ፡ ከሌለው ፡ ግን ፡ ከጨለማ ፡ ስራ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አትሁኑ ። ገሥጽዋቸው ፡ እንጂ ። ከርሳቸው ፡ በስውር ፡ የሚሆነው ፡ በርሱ ፡ መናገር ፡ ደግሞ ፡ ነውር ፡ ነውና ። የምትገሠጽ ፡ ስራ ፡ ግን ፡ ከብርሃን ፡ ትገለጣለች ፡ የተገለጠ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ብርሃን ፡ ነውና ። ስለዚኽም ፡ ይላል ። ንቃ ፡ የተኛኽ ፡ ከሙታንም ፡ ተነሣ ፡ ክርስቶስም ፡ ያበራልኻል ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፩፡ ፲፬—፳፰።

ጋኔንንም ፡ ያወጣ ፡ ነበር ። ያም ፡ ድዳ ፡ ነበር ። ጋኔኑም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ድዳው ፡ ተናገረ ። አሕዛብም ፡ ተደነቁ ። ከርሳቸውም ፡ ሰዎች ፡ አሉ ። በብዔል ፡ ዜቡል ፡ ባጋንንት ፡ አለቃ ፡ አጋንንትን ፡ ያወጣል ። ሌሎችም ፡ ፈትነውት ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከሰማይ ፡ ምልክትን ፡ ይሹ ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ ግን ፡ አሳባቸውን ፡ አወቀ ፡ አላቸውም ። እርሱ ፡ በርሱ ፡ የምትለያይ ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ትጠፋለች ። ቤትም ፡ በቤት ፡ ላይ ፡ ቢለይ ፡ ይወድቃል ። ሰይጣንም ፡ ደግሞ ፡ በራሱ ፡ ቢለይ ፡ እንዴት ፡ ትጸናለች ፡ መንግሥቱ ። ትላላችሁና ፡ እኔ ፡ አጋንንትን ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ እንደወጣ ። እኔስ ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ አጋንንትን ፡ የማወጣ ፡ ከሆንሁ ፡ ልጆቻችሁ ፡ በማን ፡ ያወጣሉ ። ስለዚኽም ፡ ፈራጆቻችሁ ፡ እርሳቸው ፡ ይሆናሉ ። እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጻት ፡ አጋንንትን ፡ አወጣ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እንጊደህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ወደላንት ፡ ደረሰች ። ብርቱው ፡ ጋሻ ፡ ጦሩን ፡ ለብሶ ፡ ቤቱን ፡ ቢጠብቅ ፡ ከብቱ ፡ ደኅና ፡ ነው ። ከርሱ ፡ የበረታ ፡ ግን ፡ ቢመጣበት ፡ ቢያሸንፈውም ፡ ይታመነው ፡ የነበረውን ፡ ጋሻ ፡ ጦሩን ፡ ይወስዳል ፡ ከብቱንም ፡ ይከፍላል ። ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያልሆነ ፡ እርሱ ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ነው ።



ከኔም ፡ ጋራ ፡ የማይሰበስብ ፡ እርሱ ፡ ይበትናል ። መንፈስ ፡ ርኩስ ፡ ከሰው ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ ስፍራ ፡ ይዞራል ፡ ዕረፍትን ፡ ሲሻ ። ባላገኘም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ወጣሁበት ፡ ቤቴ ፡ ልመለስ ፡ ይላል ። ሲመጣም ፡ ጊዜ ፡ ተጠርጎ ፡ አጊጦም ፡ ያገኘዋል ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይሔዳል ፡ ከርሱ ፡ ጋራም ፡ ሰባቱን ፡ ሌሎች ፡ ከርሱ ፡ የሚከፉትን ፡ መናፍስት ፡ ይወስዳል ፡ ይገቡማል ፡ ከዚያም ፡ ይቀመጣሉ ። የዚያ ፡ ሰውም ፡ ኋለኛው ፡ ከፊተኛው ፡ የከፋ ፡ ይሆናል ። እርሱም ፡ ይህን ፡ ሲል ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ከሕዝቡ ፡ ድምጽዋን ፡ ከፍ ፡ አድርጋ ፡ ጮኸች ፡ አለችውም ፡ የተሸከመኽ ፡ ሆድ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡ የጠባኻቸውም ፡ ጡቶች ። እርሱ ፡ ግን ፡ አለ ። የተመሰገኑስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የሚሰሙ ፡ የሚጠብቁትም ።

የጾም ፡ አርባ ፡ አራተኛ ፡ እሁድ ።

ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችን ፡ መቅሠፍት ፡ በውነት ፡ የተገባነ ፡ በጸጋህ ፡ መጸናናትህ ፡ በምህረትህም ፡ እርዳነ ፡ በጌታችንና ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ገላትያን ፡ ፬፡ ፳፩—፴፩።

ንገሩኝ ፡ እላንት ፡ ከኦሪት ፡ በታች ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ የምትወዱ ። ኦሪትን ፡ አትሰሙምን ። ተጽፈዋልና ፡ ለአብርሃም ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ነበሩት ። አንዱ ፡ ከባርያዪቱ ፡ ሁለተኛውም ፡ ከመቤቲቱ ። ነገር ፡ ግን ፡ የባርያዪቱ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሥጋ ፡ ተወለደ ። ከመቤቲቱ ፡ ግን ፡ የተወለደው ፡ በተስፋ ፡ ነው ። እርሳቸውም ፡ ምሳሌ ፡ ናቸው ። እሌኽ ፡ ሁለቱ ፡ ሕገጋት ፡ ናቸውና ። አንዲቱ ፡ ከደብረ ፡ ሲና ፡ ልጆች ፡ ለባርነት ፡ የምትወልድ ፡ እርስዋም ፡ አጋር ፡ ናት ። አጋር ፡ ባረብ ፡ አገር ፡ ያለች ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡ ናትና ። እርስዋም ፡ ዛሬ ፡ ያለችውን ፡ የሩሳሌም ፡ ትመስላለች ።

በባርነትም ፡ አለች ፡ እርስዋ ፡ ከልጆችዋ ፡ ጋራ ። የላይኛ ዪቱ ፡ የሩሳሌም ፡ ግን ፡ እርስዋ ፡ እመቤት ፡ ናት ፡ እርስ ዋም ፡ የኛ ፡ የሁላችን ፡ እናት ፡ የምትሆን ። ተጽፎዋልና ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ደስ ፡ ይበልሽ ፡ አንቺ ፡ መካን ፡ ወልደሽ ፡ የማታውቂ ። እጅግ ፡ ደስ ፡ ይበልሽ ፡ እልልም ፡ በዪ ፡ አን ቺ ፡ አምፀሽ ፡ የማታውቂ ። የመካኒቱ ፡ ልጆች ፡ በዝተዋ ልና ፡ ባል ፡ካላቱ ፡ ይልቅ ። እኛ ፡ ግን ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ የ ተስፋ ፡ ልጆች ፡ ነን ፡ እንደ ፡ ይስሐቅ ። ነገር ፡ ግን ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሥጋ ፡ የተወለደው ፡ እንደ ፡ መንፈስ ፡ የተወለደውን ፡ እንደሳደደው ። እንዲህ ፡ ነው ፡ ዛሬም ። ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ይላል ፡ መጻፉ ። ባርያዪቱን ፡ አውጣ ፡ ልጅዋንም ። የባ ርያ ፡ ልጅ ፡ አይወርስምና ፡ ከመቤት ፡ ልጅ ፡ ጋራ ። አሁን ም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ የባርያ ፡ ልጆች ፡ አይደለነም ። የመቤት ፡ እንጂ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፮፡ ፩፡—፲፬።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ የሱስ ፡ ሔደ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ባሕር ፡ ማዶ ። እርሱም ፡ የጥብርያዶስ ፡ ባሕር ። እጅግ ፡ ሰዎችም ፡ ተከተ ሉት ። በድውያን ፡ የሚያደርጋትን ፡ ተአምራት ፡ ያዩ ፡ ነበ ሩና ። የሱስም ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ፡ ከዚያም ፡ ተቀመጠ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋራ ። ፋሲካም ፡ የአይሁድ ፡ በዓል ፡ ቀርቦ ፡ ነበረ ። የሱስም ፡ ዓይኑን ፡ አንሣ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ወደርሱ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ። ፊልጶስንም ፡ አለው ። ከወዴት ፡ እንጀራ ፡ እንገዛለን ፡ እሊኽ ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ። ይኽነንም ፡ ማለቱ ፡ ይፈትነው ፡ዘንድ ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ የሚያደርገውን ፡ ያውቅ ፡ ነበረና ። ፊልጶስም ፡ መለሰለት ፡ አለውም ። የሁ ለት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ እንጀራ ፡ አይበቃቸውም ፡ ከርሳቸው ፡ ኢያንዳንዱ ፡ ጥቂት ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ። ከደቀ ፡ መዛሙር ቱም ፡ አንዱ ፡ እርሱም ፡ እንድርያስ ፡ የሲሞን ፡ ጴጥሮስ ፡ ወንድም ፡ አለው ። ከዚኽ ፡ ዐሽከር ፡ አለ ፡ አምስት ፡ የገብ ስ ፡ እንጀራ ፡ ያያዘ ፡ ሁለትም ፡ ዓሣ ። ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ይ በቃል ፡ ይኽ ፡ እሊኽን ፡ ለሚያኽሉ ። የሱስም ፡ አለ ። ሰዎ ችን ፡ እንዲቀመጡ ፡ አድርጉ ። በዚያም ፡ ስፍራ ፡ እጅግ ፡



መስክ ፡ ነበረ ። ሰዎችም ፡ ተቀመጡ ፡ ቍጥራቸውም ፡ አ ምስት ፡ ሽህ ፡ ያህላል ። የሱስም ፡ እንጀሮችን ፡ ወሰደ ፡ አ መሰገነም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሰጠ ። ደቀ ፡ መዛሙር ትም ፡ ለተቀመጡት ፡ ሰጡ ። እንዲሁም ፡ ከሁለቱ ፡ ዓሣች ፡ በወደዱት ፡ መጠን ። በጸገቡም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ አለ ። የቀረውን ፡ ቍራሽ ፡ አከማቹ ፡ ከርሱ ፡ አንዳች ፡ እንዳ ይጠፋ ። አከማቹም ፡ አሥራ ፡ ሁለትም ፡ ቅርጫት ፡ ቍራሽ ፡ መሉ ፡ ካምስቱ ፡ ከገብስ ፡ እንጀራ ፡ ለበዮች ፡ የቀረ ። ሰዎ ችም ፡ የሱስ ፡ ያደረገውን ፡ ተአምራት ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ አሉ ። በውነት ፡ ይኽ ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ የሚመጣ ፡ ነቢይ ፡ ነው ።

የጾም ፡ አርባ ፡ አምስተኛ ፡ እሁድ ።

ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ሕዝብህን ፡ በምህረትህ ፡ እንድትይ ፡ እንለምንሃለን ፡ እርሳቸው ፡ በሥ ጋና ፡ በነፍስ ፡ በታላቅ ፡ ቸርነትህ ፡ ተገዝተውና ፡ ተጠብቀ ው ፡ ለዘላለም ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌ ታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ዕብራውያን ፡ ፱፡ ፲፩፡—፲፭።

ክርስቶስ ፡ ግን ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ላለው ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ የካህናት ፡ አለቃ ፡ ሁኖ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ። ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ወደ ፡ ተፈጸመችውም ፡ በጅም ፡ ወዳልተሰራች ፡ እርሱ ም ፡ ማለቱ ፡ ከዚኽ ፡ ፍጥረት ፡ ወዳይደለች ፡ ድንኳን ፡ ገባ ። የፍየልና ፡ የላም ፡ ደም ፡ ይዞም ፡ አልገባም ። ነገር ፡ ግን ፡ በራሱ ፡ ደም ፡ አንደግዜ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገባ ። ስለ ኛም ፡ የዘላለምን ፡ መድኃኒት ፡ አገኘ ። የበሬና ፡ የፍየል ፡ ደምስ ፡ የላምም ፡ አመድ ፡ በረከሱት ፡ ላይ ፡ ቢረጭ ፡ ሥጋ ቸውን ፡ ለማንጻት ፡ የሚቀድሳቸው ፡ ከሆነ ። እንዴት ፡ ይል ቁን ፡ የክርስቶስ ፡ ደም ፡ ለዘላለም ፡ በሚኖር ፡ መንፈስ ፡ ራሱን ፡ ያቀረበ ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕሊናች ሁን ፡ ያነጻል ፡ ከሞተ ፡ ስራ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታገ

ለግሉ ፡ ዘንድ ፡፡ ስለዚኽም ፡ እርሱ ፡ ላደስ ፡ ኪዳን ፡ ማእ
ከላዊ ፡ ሆነ ፡፡ በሞቱ ፡ መድኃኒት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከፊተኛ፡
ኪዳን ፡ በታች ፡ ከሆነ ፡ መተላለፍ ፡፡ ለዘላለም ፡ ርስትም ፡
የተጸረት ፡ ተስፈውን ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፰፡ ፵፮—፶፱፡፡

ማነው ፡ ከላንተ ፡ ስለ ፡ ኀጢአት ፡ የሚወቅሰኝ ፡፡ እውነት
ም ፡ የምናገር ፡ ከሆንሁ ፡ እለንተ ፡ ለምን ፡ አታምኑብኝም ፡፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሆነ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ይሰማል ፡፡ ስለዚኽ ፡ እላንተ ፡ አትሰሙም ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ አይደላችሁምና ፡፡ መለሱ ፡ አይሁድ ፡ አሉትም ፡፡
እኛ ፡ መልካም ፡ እንል ፡ የለነምን ፡ ሳምራዊ ፡ እንደ ፡ ሆን
ኽ ፡ ጋኔንም ፡ እንደለብኽ ፡፡ መለሰ ፡ የሱስ ፡ አለም ፡፡ እ
ኔስ ፡ ጋኔን ፡ የለብኝም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ አባቴን ፡ አከብራለሁ፡
እላንተም ፡ ትንቁኛላችሁ ፡፡ እኔም ፡ ክብሬን ፡ አልሻም ፡፡
የሚሻው ፡ የሚፈርድም ፡ አለ ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡
እላችኋለሁ ፡፡ ማንም ፡ የኔን ፡ ቃል ፡ ቢጠብቅ ፡ ሞትን ፡
አያይም ፡ ለዘላለም ፡፡ አይሁድም ፡ አሉት ፡፡ አሁን ፡ ጋኔን ፡
እንደለብኽ ፡ አወቅነ ፡፡ አብርሃም ፡ ስንኳ ፡ ሞተ ፡ ነቢያ
ትም ፡፡ አንተም ፡ ትላለኽ ፡፡ ማንም ፡ ቃሌን ፡ ቢጠብቅ ፡
ሞትን ፡ አይቀምሰውም ፡ ለዘላለም ፡፡ በውኑ ፡ አንተ ፡ ካ
ባታችን ፡ ካብርሃም ፡ ከሞተው ፡ ትበልጣለኽ ፡፡ ነቢያትም ፡
ሞቱ ፡፡ አንተ ፡ ራስኽን ፡ ማነን ፡ ታደርጋለኽ ፡፡ መለሰ ፡ የ
ሱስ ፡ አለም ፡፡ እኔስ ፡ ራሴን ፡ ባከብር ፡ ክብሬ ፡ አንዳች ፡
አይሆንም ፡፡ አባቴ ፡ ነው ፡ የሚያከብረኝ ፡፡ እላንተ ፡ አም
ላካችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የምትሉት ፡፡ አታውቁትም ፡ ስንኳ ፡፡
እኔ ፡ ግን ፡ አውቀዋለሁ ፡፡ አላውቀውምም ፡ ብል ፡ እንደ
ላንተ ፡ አሰተኛ ፡ ብሆን ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ አውቀዋለሁ ፡ ቃሉንም ፡
እጠብቃለሁ ፡፡ አብርሃም ፡ አባታችሁ ፡ ቀኔን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡
ተመኘ ፡፡ አየም ፡ ደስም ፡ አለው ፡፡ አይሁድም ፡ አሉት ፡፡
ገና ፡ አምሳ ፡ አመት ፡ አልሆነኽም ፡፡ አንተምን ፡ አብርሃ
ምን ፡ አየኽ ፡፡ አላቸውም ፡ የሱስ ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡
እላችኋለሁ ፡፡ አብርሃም ፡ ሳይሆን ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡፡ ያዚያን ፡



ጊዜም ፡ ደንጊያን ፡ አነሡ ፡ ሊወግሩት ፡፡ የሱስ ፡ ግን ፡
ተሠወረ ፡ ከመቅደስም ፡ ወጣ ፡፡ በመኻከላቸውም ፡ አ
ለፈ ፡ እንደሁም ፡ ሔደ ፡፡

---

ፈሲካውን ፡ የሚቀድም ፡ እሁድ ፡፡

ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ከታ
ላቅ ፡ ፍቅርህ ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ የተነሣ ፡ ልጅህን ፡ የሱ
ስ ፡ ክርስቶስ ፡ መድኃኒታችንን ፡ ሥጋችንን ፡ ለመልበስ ፡ በ
መስቀልም ፡ ተሰቅሎ ፡ ለመሞት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የርሱን ፡
የታላቅ ፡ ትሕትናውን ፡ ምሳሌ ፡ ይከተል ፡ ዘንድ ፡ ሰደህዋ
ልና ፡ እኛም ፡ የትዕግሥቱን ፡ ምሳሌ ፡ እንከተል ፡ ዘንድ ፡
የትንሣኤውንም ፡ ተካፋዮች ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡
ስጠነ ፡ በርሱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፊልጵስዩስ ፡ ፪፡ ፭—፲፩፡፡

በላንትም ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ የነበረ ፡ ልብ ፡ ይሁንባች
ሁ ፡፡ እርሱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መልክ ፡ ሲኖር ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ ጋራ ፡ ይተካከል ፡ ዘንድ ፡ መቅማትን ፡ አልቈጠረም ፡፡
ራሱን ፡ ለምናምን ፡ አደረገ ፡ የባርያውንም ፡ መልክ ፡ ይዞ ፡
በሰዎች ፡ ምሳሌ ፡ ሆነ ፡ በመልኩም ፡ ሰው ፡ ሁኖ ፡ ተገኘ ፡፡
ራሱንም ፡ አዋረደ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስም ፡ የታዘዘ ፡ ሆነ ፡
እስከ ፡ መስቀል ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡፡ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔ
ር ፡ እጅግ ፡ አላቀው ፡ ከስምም ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጠውን ፡ ስ
ም ፡ ሰጠው ፡፡ በየሱስ ፡ ስም ፡ ጕልበት ፡ ሁሉ ፡ ይጕነብስ ፡
ዘንድ ፡ በሰማይ ፡ በምድርም ፡ ከምድር ፡ በታችም ፡ ያለ ፡
ሁሉ ፡፡ መላስም ፡ ሁሉ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሆ
ነ ፡ ያስታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ክብር ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳፮፡ ፩፡—፶፱፡፡

በጸባም ፡ ጊዜ ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ የሕዝብም ፡ ሽማግ
ሎች ፡ ሁሉ ፡ በየሱስ ፡ ላይ ፡ ተመካከሩ ፡ ይገድሉት ፡ ዘን

ድ ። አሠረትም ፡ ይዘውትም ፡ ሔዱ ። ለጴንጤኑም ፡ ለ
ጲላጦስ ፡ ለመስለኔ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጡት ። የዚያን ፡ ጊዜ
ም ፡ ያስያዘው ፡ ይሁዳ ፡ እንደ ፡ ተኰነነ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አዘነ ።
ሠላሳ ፡ ብርንም ፡ ለካህናት ፡ አለቆችና ፡ ለሽማግሎች ፡ መ
ለሰ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ንጹሕ ፡ ደምን ፡ አሳልፌ ፡ ሰጠሁና ፡ ኃ
ጢአትን ፡ አደረግሁ ። እርሳቸው ፡ ግን ፡ ምን ፡ ገደደን ፡ ይህ ።
አንተ ፡ እወቅ ፡ አሉት ። እርሱም ፡ ያነን ፡ ብር ፡ በመቅደስ ፡
ጥሎ ፡ ሔደ ፡ ታንቆም ፡ ሞተ ። የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ብ
ርን ፡ ይዘው ፡ አሉ ። ወደ ፡ ቍርባን ፡ ሣጥን ፡ እንጥለው ፡
ዘንድ ፡ አይገባም ። የደም ፡ ዋጋ ፡ ነውና ። ተማከሩም ፡ የ
ሸህላ ፡ ሰሪውንም ፡ እርሻ ፡ ገዙበት ፡ ለንግዶች ፡ መቃብር ።
ስለዚኽም ፡ ያች ፡ እርሻ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የደም ፡ አ
ርሻ ፡ ትባላለች ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ በኤርምያስ ፡ በነቢይ ፡
የተባለው ፡ ተፈጸመ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ሠላሳውን ፡ ብር ፡
ወሰዱ ፡ የተገመገመውን ፡ ዋጋ ፡ ከእሥራኤል ፡ ልጆች ፡ ጋራ ፡
የተሰማሙበትን ። ለሸህላ ፡ ሰሪ ፡ እርሻም ፡ ሰጡት ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንደ፡ዘዘኝ ። የሱስም ፡ በሹም ፡ ፊት ፡ ቆመ ። ሹ
ምም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ጠየቀው ። አንተን ፡ ነህ ፡ ያይሁ
ድ ፡ ንጉሥ ። የሱስም ፡ አለው ። አንተ ፡ ትለዋለህ ። የካ
ህናት ፡ አለቆችና ፡ ሽማግሎችም ፡ ሲያሳጡት ፡ አንዳችን ፡
አልመለሰም ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አለው ፡ ጲላጦስ ። በስ
ንት ፡ ነገር ፡ የሚመስክሩብህ ፡ አትሰማምን ። ባንዲት ፡ ቃ
ልም ፡ እንኳ ፡ አልመለሰለትም ፡ ሹሙ ፡ እጅግ ፡ እስኪያ
ደንቅ ፡ ድረስ ። በየበዓልም ፡ ለሹም ፡ ልማድ ፡ ነበረ ፡ አ
ንዱን ፡ የታሠረውን ፡ ሕዝብም ፡ የወደደውን ፡ ይፈታላቸ
ው ፡ ዘንድ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አንድ ፡ የታሠረ ፡ ነበረላቸ
ው ፡ የታወቀም ፡ ስሙን ፡ በረባስ ፡ የሚሉት ። እርሳቸው
ም ፡ ተከማችተው ፡ ሳሉ ፡ ጲላጦስ ፡ አላቸው ። ማንን ፡ ት
ወዳላችሁ ፡ እፈታላችሁ ፡ ዘንድ ። በረባስን ፡ ወይስ ፡ የሱ
ስን ፡ ክርስቶስ ፡ የሚሉትን ። በቅንዓት ፡ አሳልፈው ፡ አን
ደ ፡ ሰጡት ፡ ያውቅ ፡ ነበረና ። እርሱም ፡ በወንበር ፡ ተቀም
ጦ ፡ ሳለ ፡ ምሽቱ ፡ ላከችበት ፡ እንዲህ ፡ ስትል ። ከዚህ ፡ ጻ



ድቅ ፡ ጋራ ፡ አንዳች ፡ አይሁንልህ ። ዛሬ ፡ በሕልም ፡ እጅግ ፡
መከራ ፡ ተቀበያለሁና ፡ ስለርሱ ። የካህናት ፡ አለቆች ፡ ግ
ን ፡ ሽማግሎችም ፡ ሕዝቡን ፡ በረባስን ፡ ለማደን ፡ የሱስን
ም ፡ ለመግደል ፡ ይለምኑ ፡ ዘንድ ፡ እኪ ፡ አሰኙዋቸው ። ሹ
ምም ፡ መልሶ ፡ አላቸው ። ከሁለቱ ፡ ማንን ፡ እፈታላች
ሁ ፡ ዘንድ ፡ ትሻላችሁ ። እርሳቸውም ፡ አሉ ። በረባስን ።
ጲላጦስም ፡ አላቸው ። ክርስቶስ ፡ ግን ፡ በሚባል ፡ በየሱስ ፡
ምን ፡ ልስራበት ። ሁላቸውም ፡ ይሰቀል ፡ አሉት ። ሹም
ም ፡ አለ ። ምን ፡ ክፉ ፡ አደረገ ። እርሳቸው ፡ ግን ፡ ጩኸታ
ቸውን ፡ አብዝተው ፡ ‘ይሰቀል ፡’ አሉ ። ጲላጦስም ፡ አንዳ
ች ፡ እንዳይረባው ፡ ሁከት ፡ ግን ፡ እንደ ፡ በዛ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ው
ኃውን ፡ ይዞ ፡ በሕዝብ ፡ ፊት ፡ እጁን ፡ ታጠበ ፡ እንዲህ ፡ ሲ
ል ። እኔ ፡ ከዚህ ፡ ጻድቅ ፡ ደም ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ እላንት ፡ እ
ዩ ። ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ መለሱ ፡ አሉም ። ደሙ ፡ በላያችን
ና ፡ በልጆቻችን ፡ ላይ ፡ ይሁን ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ በረባስን ፡
ፈታላቸው ፡ የሱስን ፡ ግን ፡ ገርፎ ፡ ይሰቀል ፡ ዘንድ ፡ አሳል
ፎ ፡ ሰጠ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሹም ፡ ወታደር ፡ የሱስን ፡
ወደ ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ወሰዱት ፡ ጭፍራውንም ፡ ሁሉን ፡ አከ
ማቹበት ። ልብሱንም ፡ ገፈፉት ፡ ቀይ ፡ ልብስንም ፡ አለበሱ
ት ። የሾኽ ፡ አክሊልም ፡ ጐንጕኑ ፡ በራሱ ፡ ላይም ፡ ጫኑት ፡
ዘንግንም ፡ በቀኝ ፡ እጁ ፡ ሰጡት ። በፊቱም ፡ በጕልበታቸ
ው ፡ ተምበረከኩ ፡ ተሣለቁበትም ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ደህና ፡
ነህን ፡ ያይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ። ተፉበትም ፡ ዘንጉንም ፡ ይ
ዘው ፡ ራሱን ፡ መቱበት ። ካፌዙበትም ፡ ወዲያ ፡ ያለበሱ
ትን ፡ ልብስ ፡ ገፈፉት ፡ ልብሱንም ፡ አለበሱት ። ይሰቀሉት
ም ፡ ዘንድ ፡ ወሰዱት ። ሲወጡም ፡ የቄሬናን ፡ ሰው ፡ ሲሞ
ን ፡ የሚሉትን ፡ አገኙ ። እርሱንም ፡ መስቀሉን ፡ ይሸከም ፡
ዘንድ ፡ ግድ ፡ አሉት ። ጎልጎታም ፡ ማለቱ ፡ የራስ ፡ አጽንት ፡
ስፍራ ፡ ወደሚሉት ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ ባሞት ፡ የተቀላቀለ ፡
መጣጣ ፡ ለመጠጥ ፡ ሰጡት ፡ እርሱ ፡ ግን ፡ በቀመሰው ፡ ጊ
ዜ ፡ ሊጠጣው ፡ እምቢ ፡ አለ ። በሰቀሉትም ፡ ጊዜ ፡ ልብሱ
ን ፡ ተከፋፈሉ ፡ ዕፃም ፡ ተጣጣሉበት ፡ በነቢይ ፡ የተባለ ፡ ይ

ፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ሲል ፡፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ልብሶቹን ፡ ተካ
ፈሉ ፡ በቀሚሲም ፡ ላይ ፡ ዕፃውን ፡ ተጣጣሉ ፡፡ ከዚያም ፡
ተቀምጠው ፡ ጠበቁት ፡፡ ከራሱ ፡ በላይም ፡ መክንያቱን ፡
ተጽፈ ፡ አኖሩ ፡ እንደህ ፡ ስትል ፡፡ ይህ ፡ የሱስ ፡ ነው ፡ ያይሁ
ድ ፡ ንጉሥ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁለት ፡ ሌቦች ፡ ከርሱ ፡ ጋ
ራ ፡ ተሰቀሉ ፡ አንዱ ፡ በቀኙ ፡ አንዱም ፡ በግራው ፡፡ ያለፉ
በትም ፡ ሰደቡት ፡ ራሳቸውን ፡ ኢያነቃነቁ ፡፡ ኢያሉም ፡፡ ቤ
ተ ፡ መቅደስን ፡ የምታፈርስ ፡ ሆይ ፡ በሶስት ፡ ቀንም ፡ የም
ትሰራው ፡ ራስህን ፡ አድን ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅስ ፡ እ
ንደ ፡ ሆንኽ ፡ ከመስቀል ፡ ውረድ ፡፡ እንደሁም ፡ የካህናት ፡
አለቆች ፡ ከጻፎችና ፡ ከሽማግሎች ፡ ጋራ ፡ አፌዙበት ፡ እሉ
ትም ፡፡ ሌሎችን ፡ አደነ ፡ ራሱን ፡ ግን ፡ ማደን ፡ አይችልም ፡፡
እርሱ ፡ የእሥራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የሆነ ፡ እንደሆን ፡ አሁን ፡ ከ
መስቀል ፡ ይውረድ ፡ እኛም ፡ እናምንበታለን ፡፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ታምኖ ፡ ነበረ ፡ እርሱም ፡ ቢወደው ፡ አሁን ፡ ያድነ
ው ፡፡ እኔ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ብልዋልና ፡፡ እንዲ
ሁም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የተሰቀሉ ፡ ሌቦች ፡ ሰደቡት ፡፡ ከስድ
ስተኛ ፡ ሰዓትም ፡ ጀምሮ ፡ ጨለማ ፡ ሆነ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላ
ይ ፡ እስከ ፡ ዘጠነኛ ፡ ሰዓት ፡፡ በዘጠነኛ ፡ ሰዓትም ፡ በኵል ፡
የሱስ ፡ ጮኸ ፡ በታላቅ ፡ ድምጽ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ኤሎሄ ፡
ኤሎሄ ፡ ለማ ፡ ሰበኽተኒ ፡፡ ማለቱ ፡፡ አምላኬ ፡ አምላኬ ፡
ለምን ፡ ተውኸኝ ፡፡ አያሌም ፡ ከዚያ ፡ ከቆሙት ፡ ሲሰሙ ፡፡
ይኽስ ፡ ኤልያስን ፡ ይጸራል ፡ አሉ ፡፡ ድንገትም ፡ አንድ ፡ ከ
ርሳቸው ፡ ሩጦ ፡ ሰፍነግንም ፡ ይዞ ፡ መጣጣ ፡ መላባት ፡ በዘ
ንግ ፡ ላይም ፡ ጫነው ፡ አጠጣውም ፡፡ የቀሩት ፡ ግን ፡ አሉ ፡፡
ተው ፡ እንይ ፡ ኤልያስ ፡ መጥቶ ፡ ያድነው ፡ እንደሆን ፡፡ የሱ
ስ ፡ ግን ፡ ደግሞ ፡ በታላቅ ፡ ድምጽ ፡ ጮኾ ፡ መንፈሱን ፡ አ
ሰነበተ ፡፡ እነሆም ፡ የቤተ ፡ መቅደስ ፡ መጋረጃ ፡ በሁለት ፡ ተ
ቀደደ ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡፡ ምድርም ፡ ተናወጠች ፡ አም
ቦችም ፡ ተሰነጠቁ ፡፡ መቃብሮችም ፡ ተከፈቱ ፡ ከቅዱሳን
ም ፡ በድኖች ፡ ከተኙ ፡ ብዙ ፡ ተነሡ ፡ እርሱም ፡ ከትንሣ
በኋላ ፡ ከመቃብሮቻቸው ፡ ወጡ ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ አገርም ፡



ገቡ ፡ ለብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ታዩ ፡፡ የመቶ ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ከር
ሱ ፡ ጋራም ፡ ኑረው ፡ የሱስን ፡ የጠበቁ ፡ መናወጥን ፡ የሆነ
ውንም ፡ ሁሉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፡ እንዲህም ፡ አሉ ፡፡
በውነት ፡ ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፡፡

ፈሲካውን ፡ የሚቀድም ፡ ሰኞ ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ ኢሳይያስ ፡ ፷፫፤ ፩፡—፲፱፡፡

ማነው ፡ ይህ ፡ ከኤዶምያስ ፡ የሚመጣ ፡ ልብሱም ፡ ቀለ
ም ፡ የገባ ፡ ከቦጽራ ፡፡ ይኽ ፡ በልብሱ ፡ ያማረ ፡ በኍልበቱ ፡
ብዛት ፡ የሚሔድ ፡፡ እኔ ፡ በጽድቅ ፡ የምናገር ፡ እኔ ፡ ለማደ
ን ፡ የምበርታ ፡፡ ልብስኽ ፡ ስለምን ፡ ቀላ ፡ ቀሚስኽም ፡ በ
መጥመቂያ ፡ ወይንን ፡ እንደሚረግጥ ፡፡ መጥመቂያውን ፡ ብ
ቻዬን ፡ ረገጥሁ ፡ ከአሕዛብም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አል
ነበረም ፡፡ በቍጣዬም ፡ ረገጥኋቸው ፡ በመዓቴም ፡ ቀጠቀጥ
ኋቸው ፡፡ ደማቸውም ፡ ልብሴን ፡ ረጨ ፡ ልብሴንም ፡ ሁሉ ፡
አረከስሁ ፡፡ የበቀል ፡ ቀን ፡ በልቤ ፡ ነበረና ፡ የተበጀኋቸው
ም ፡ ዘመን ፡ መጣች ፡፡ ዙርያዬንም ፡ አየሁ ፡ የሚረዳም ፡
አልተገኘም ፡ አደነቅሁም ፡ የሚደግፈኝ ፡ አልነበረምና ፡፡ ክ
ንዴም ፡ አዳነችኝ ፡ ቍጣዬም ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ የደገፈኝ ፡፡ በ
ቍጣዬም ፡ አሕዛብን ፡ እረግጣለሁ ፡ በመዓቴም ፡ አሰክራ
ቸዋለሁ ፡ ኍልበታቸውንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ እጥላለሁ ፡፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ አሳስባለሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ምስጋና ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደሰጠን ፡ ሁሉ ፡ መጠን ፡ ለእሥ
ራኤልም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ አደረጋት ፡ እንደ ፡ በጐነቱ ፡ ብዛት ፡
እንደ ፡ ርኅራኄው ፡ መጠን ፡ እንደ ፡ ፍቅሩም ፡ ብዛት ፡፡ አለ
ም ፡ በውነት ፡ ሕዝቤ ፡ ናቸው ፡ አስተኞችም ፡ ልጆች ፡ አደይ
ሉም ፡ መድኃኒትም ፡ ሆነላቸው ፡፡ በጻራቸው ፡ ሁሉ ፡ እር
ሱ ፡ ተጻረ ፡ የፊቱም ፡ መልአክ ፡ አዳናቸው ፡፡ በፍቅሩ ፡ በ
ምሕረቱም ፡ እርሱ ፡ ተበዣቸው ፡ ተሸከማቸውም ፡ የዓለ
መንም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ታዘላቸው ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ የቅዱ
ስነቱን ፡ መንፈስ ፡ አስመረሩና ፡ አሳዘኑት ፡ ተመልሶም ፡ ጸ

ላት ፡ ሆናቸው ፡ እርሱም ፡ ተዋጋቸው ። የቀደመውንም ፡ ዘ
መን ፡ ኢሰበ ፡ ሙሴንና ፡ ሕዝቡንም ። ወዴት ፡ ነው ፡ ይኸ ፡ ከ
ባሕር ፡ ያወጣቸው ፡ ከበጎቹ ፡ ጠባቂ ፡ ጋራ ። የቅድስናውን ፡
መንፈስ ፡ በውሥጡ ፡ ያደረገ ፡ ወዴት ፡ ነው ። በሙሴ ፡ ቀኝ ፡
ያስሔደቸው ፡ በክብሩ ፡ ክንድ ፡ በፊታቸውም ፡ ውኃውን ፡
የከፈለ ፡ ለራሱ ፡ የዘላለምን ፡ ስም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ። በቀ
ላይ ፡ ያስሔደቸው ፡ እንደ ፡ ፈረስ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳይ
ሰናከሉ ። በቍላም ፡ እንደሚወርድ ፡ እንስሳ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ መንፈስ ፡ የሚመራው ፡ ነበረ ። እንዲሁ ፡ ሕዝብኽን ፡
መራኽ ፡ ለራስኽ ፡ የምስጋናውን ፡ ስም ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ።
ከሰማይ ፡ ተመልከት ፡ ከቅዱስነትኽም ፡ ከብርሃንኽም ፡
ማደርያ ፡ እይ ። ቅንዓትኽ ፡ ወዴት ፡ አለች ፡ ኃይልኽስ ። የ
ርኅራኄኽ ፡ ብዛት ፡ ምሕረትኽም ፡ ከኔ ፡ ተከለከለች ። አን
ተ ፡ አባታችን ፡ ነኽና ። አብርሃምም ፡ አያውቀንም ፡ ለእሥራ
ኤልም ፡ አልታወቅነም ። አንተ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ አባታ
ችን ፡ ነኽ ፡ የተበጀኽነም ። ስምኽ ፡ ከዘላለም ፡ ይህ ፡ ነው ።
ለምን ፡ ከመንገድኽ ፡ አሳትኸነ ፡ አቤቱ ፡ ልባችነንም ፡ አጸ
ናኽ ፡ እንዳንፈራኽ ። ስለ ፡ ባሮችኽ ፡ ተመለስ ፡ ስለ ፡ ርስት
ኽ ፡ ነገድ ። የተቀደሱ ፡ ሕዝብኽ ፡ ለጥቂት ፡ ዘመን ፡ ገዙት ።
ጸላቶቻችን ፡ መቅደስኽን ፡ ረገጡ ። ከዘላለም ፡ እንዳልገዛ
ኸነ ፡ ሆነ ፡ ስምኽም ፡ በላያችን ፡ እንዳልተጸራ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማርቆስ ፡ ፲፬፡ ፩፡—፲፪፡፡

በዓለ ፡ ፋሲካ ፡ በዓለ ፡ ናእትም ፡ ከሁለት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡
ነበረ ። የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ጻፎችም ፡ በተንኰል ፡ እን
ዴት ፡ ይይዙት ፡ ዘንድ ፡ ይገሉትም ፡ ዘንድ ፡ ይሹ ፡ ነበር ። ይ
ሉም ፡ ነበረ ፡ በበዓል ፡ አይደለም ። በሕዝቡ ፡ ሁከት ፡ እን
ዳይሆን ። እርሱም ፡ በቢታንያ ፡ ሳለ ፡ በለምጻሙ ፡ በሲሞ
ን ፡ ቤት ፡ ለመብል ፡ ተቀምጦ ። ሴት ፡ መጣች ፡ የሽቱ ፡ ቢረ
ሌ ፡ ይዛ ፡ ናርደስ ፡ የሚሉት ፡ የተፈተነ ፡ ዋጋውም ፡ የበዛ ።
ቢረሌውንም ፡ ሰበረችና ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ገለበጠችው ። ከዚ
ያም ፡ ኢያሌ ፡ ነበሩ ፡ በልባቸው ፡ የተቈጡ ፡ እንዲህም ፡



ያሉ ። ለምን ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡ ጥፋት ፡ በዚህ ፡ ሽቱ ። ይኽ ፡ ከሦ
ስት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ በሚበልጥ ፡ ይሸጥ ፡ ዘንድ ፡ ለድኆች
ም ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ይሆን ፡ ነበረና ። አንጐረጐሩባትም ። የ
ሱስ ፡ ግን ፡ አለ ። ተውዋት ። ለምን ፡ ታደክምዋታላችሁ ።
መልካምን ፡ ስራ ፡ አደረገችብኝ ። ድኆችስ ፡ በላንት ፡ ዘን
ድ ፡ ሁለግዜ ፡ አሉ ። ቸርነትንም ፡ ታደርጉላቸው ፡ ዘንድ ፡
ከወደዳችሁስ ፡ ትችላላችሁ ። እኔ ፡ ግን ፡ በላንት ፡ ዘንድ ፡
ሁለግዜ ፡ አይደለሁም ። ያላትን ፡ ፈጽማ ፡ አደረገችው ።
ሥጋዬን ፡ ለመቅበሬ ፡ ትቀባው ፡ ቀደመች ። እውነት ፡ እላ
ችኋለሁ ። ይኽ ፡ ወንጌል ፡ ወደሚሰበክበት ፡ ዘንድ ፡ በዓለ
ሙ ፡ ሁሉ ። ይህች ፡ ደገሞ ፡ ያደረገችው ፡ ይነገራል ፡ ለርስ
ዋ ፡ መታሰብያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ይሁዳም ፡ ያስቆሮቱ ፡ ካ
ሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንድ ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቆች ፡ ሔደ ፡ አሳል
ፎ ፡ ሊሰጣቸው ። እርሳቸውም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ አላ
ቸው ፡ ብርንም ፡ ይሰጡት ፡ ዘንድ ፡ ተስፈ ፡ አስደረጉለት ።
ጊዜም ፡ ደኘ ፡ ነበር ፡ እንዴት ፡ ያሲዘው ፡ ዘንድ ። በናእት ፡
ቀንም ፡ መጀመርያ ፡ ፋሲካን ፡ ባረዱ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙ
ርቱ ፡ አሉት ። ወዴት ፡ ትወደለኽ ፡ ሒደን ፡ እናሰናደልኽ ፡
ዘንድ ፡ ፋሲካን ፡ እንድትበላ ። ከደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሁለቱ
ን ፡ ሰደደ ፡ አላቸውም ። ወደገር ፡ ሒዱ ፡ ሰውም ፡ ያገኛችኋ
ል ፡ ማድጋ ፡ ውኃ ፡ ተሸክሞ ። ተከተሉት ። ወደሚገባበቱ
ም ፡ ባለ ፡ ቤቱን ፡ በሉት ። መምህር ፡ ይላል ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ የ
ዕረፍት ፡ ስፍራ ፡ ፋሲካን ፡ የምበላበት ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡
ጋራ ። እርሱም ፡ ታላቁን ፡ የተነጸፈችን ፡ የተዘጋጀችንም ፡
አደራሽ ፡ ያሳያችኋል ። ከዚያ ፡ አሰናዱልን ። ደቀ ፡ መዛ
ሙርቱም ፡ ወጽተው ፡ ወደገር ፡ መጡ ። እንደላቸውም ፡ አ
ገኙ ፡ ፋሲካንም ፡ አዘጋጁ ። በመሸም ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ መ
ጣ ፡ ካሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ጋራ ። እርሳቸውም ፡ ተቀምጠው ፡ ሲ
በሉ ፡ የሱስ ፡ አለ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ። ከላንት ፡ አን
ዱ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ የሚበላው ፡ አሳልፎ ፡ እንዲሰጠኝ ። እርሳ
ቸውም ፡ ያዝኑ ፡ ጀመሩ ፡ ይሉትም ፡ ኢያንዳንዱ ። ምናል
ባት ፡ እኔ ፡ እሆን ። ሌላውም ፡ አለ ፡ እኔን ፡ እሆን ። እር

ሶ·ም ፡ መለሰ ፡ አላቸውም ፡፡ አንዱ ፡ ካሥራ ፡ ሁለቱ ፡ እጁ
ን ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ በወጭት ፡ የሚጠልቅ ፡፡ የሰው ፡ ልጅስ ፡ ስ
ለርሱ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ይሔደል ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ወዮለት ፡ ለዚ
ያ ፡ ሰው ፡ በጁ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ የሚሰጥ ፡፡ ያሰው ፡ ባይወለ
ድ ፡ ይሻለው ፡ ነበረ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ሲበሉ ፡ የሱስ ፡ እን
ጀራውን ፡ ወሰደ ፡ ባረከውም ፡ ቈረሰውም ፡ ሰጣቸውም ፡
አለም ፡፡ እንኩ ፡፡ ብሉ ፡፡ ይህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፡፡ ጽዋንም ፡
ወሰደ ፡ አመሰገነም ፡ ሰጣቸውም ፡፡ ሁላቸውም ፡ ከርሱ ፡
ጠጡ ፡፡ አላቸውም ፡፡ ይህ ፡ ደሜ ፡ ነው ፡ ላዲስ ፡ ሥርዓት ፡
ስለ ፡ ብዙ ፡ የሚፈስ ፡፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ ከንግዴህ ፡
ወደህ ፡ ከወይኑ ፡ ፍሬ ፡ አንደልጠጣ ፡ እስከዚያ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
አዲሱን ፡ በምጠጣበት ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥ
ት ፡፡ አመስግነውም ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ወጡ ፡፡ የሱስ
ም ፡ አላቸው ፡፡ ሁላችሁ ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ተሰናከሉብኛላች
ሁ ፡፡ ተጽፏልና ፡፡ ጠባቂውን ፡ እመታለሁ ፡ በጎችም ፡ ይበ
ተናሉ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከተነሣሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ሒጄ ፡
እቀድማችኋላሁ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ አለው ፡፡ ሁሉም ፡ ቢሰና
ከሉ ፡ እኔ ፡ ባልሰናከል ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡፡ እውነት ፡ እ
ልኻለሁ ፡፡ ዛሬ ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ደሮ ፡ ሁለትግዜ ፡ ሳይጮ
ኽ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደኛለኽ ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ጨምሮ ፡ አ
ለ ፡፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ እሞት ፡ ዘንድ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ አልክ
ድኽም ፡፡ ሁሉም ፡ እንደህ ፡ አሉ ፡፡ ጌቴሴማኔም ፡ ወደሚ
ሉት ፡ ስፍራ ፡ መጡ ፡፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፡ አለ ፡፡ ከዚ
ህ ፡ ተቀመጡ ፡ እስክጸልይ ፡ ድረስ ፡፡ ጴጥሮስንም ፡ ያዕቆብ
ንም ፡ ዮሐንስንም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይዞ ፡ ሔደ ፡፡ ይደነግጥም ፡
ያዝንም ፡ ጀመረ ፡፡ አላቸውም ፡፡ ነፍሴ ፡ እጅግ ፡ አዝናለ
ች ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡፡ ከዚህ ፡ ቈዩ ፡ ትጉም ፡፡ ጥቂት
ም ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ፡ በምድርም ፡ ወደቀ ፡፡ ይቻል ፡ እንደሆነ
ም ፡ ሰዓቲቱ ፡ ከርሱ ፡ ታልፍ ፡ ዘንድ ፡ ጸለየ ፡፡ እንደህ ፡ ሲ
ል ፡፡ አባ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ ሁሉ ፡ ይቻልኻልና ፡፡ ይህችን ፡ ጽዋ ፡
ከኔ ፡ ውሰድ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ የምወድ ፡ አይደለም ፡ አን
ተ ፡ የምትወደው ፡ እንጅ ፡፡ መጣም ፡ ተኝተውም ፡ አገኛቸ



ው ፡፡ ጴጥሮስንም ፡ አለ ፡፡ ሲሞን ፡ ሆይ ፡ ትተኛለህን ፡፡ አ
ንዲት ፡ ሰዓት ፡ ስንኳ ፡ ትተጋ ፡ ዘንድ ፡ አልቻልኽምን ፡፡ ት
ጉ ፡ ጸልዩም ፡ ወደ ፡ ፈተና ፡ እንዳትገቡ ፡፡ መንፈስ ፡ እሽተ
ኛ ፡ ነው ፡ ሥጋ ፡ ግን ፡ የደከመ ፡ ነው ፡፡ ደግሞም ፡ ሔደ ፡ የቀ
ደመውንም ፡ ነገር ፡ ጸለየ ፡፡ ደግሞም ፡ ተመልሶ ፡ ተኝተው ፡
አገኛቸው ፡፡ ዓይናቸው ፡ ከብደ ፡ ነበረችና ፡፡ የሚመልሱለ
ትንም ፡ አያውቁም ፡ ነበር ፡፡ ሶስተኛም ፡ መጣ ፡ አላቸው
ም ፡፡ እንግዴህስ ፡ ተኙ ፡ ዕረፉም ፡፡ ይበቃል ፡፡ ሰዓቲቱ ፡ ደረ
ሰች ፡፡ እነሆ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በኃጥኣን ፡ እጅ ፡ ይሰጣል ፡፡ ተ
ነሡ ፡ እንሒድ ፡፡ እነሆ ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጠኝ ፡ ደረሰ ፡፡ የ
ዚያን ፡ ጊዜም ፡ እርሱ ፡ ገና ፡ ይህነን ፡ ሲናገር ፡ ይሁደ ፡ ካ
ሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡ መጣ ፡፡ ከርሱ ፡ ጋራም ፡ እጅግ ፡ ሰዎ
ች ፡ ሰይፍ ፡ ጎመድም ፡ ይዘው ፡ ከካህናት ፡ አለቆች ፡ ከጻ
ፎችም ፡ ከሽማግሎችም ፡፡ የሚያሲዘውም ፡ ምልክት ፡
ሰጥትዋቸው ፡ ነበረ ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡ የምስመው ፡ እርሱ ፡
ነው ፡፡ ያዙት ፡ ደህናም ፡ አድርጋችሁ ፡ ውሰዱት ፡፡ መጽቶ
ም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ወደርሱ ፡ ቀረበ ፡ አለም ፡፡ መምህር ፡
ሆይ ፡ መምህር ፡ ሆይ ፡፡ ሳመውም ፡፡ እርሳቸውም ፡ እጃቸ
ውን ፡ ጣሉበት ፡ ያዙትም ፡፡ ከዚያም ፡ ከቆሙ ፡ አንዱ ፡
ሰይፏን ፡ መዘዘ ፡ የካህናቱንም ፡ አለቃ ፡ ባርያ ፡ መታ ፡፡ ጆ
ሮውንም ፡ ቈረጠው ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አላቸውም ፡፡ በ
ሌባ ፡ ላይ ፡ እንድትወጡን ፡ ወጣችሁ ፡ ሰይፍና ፡ ጎመድ ፡ ይ
ዛችሁ ፡ ልትይዙኝ ፡፡ ሁለግዜ ፡ በላንት ፡ ዘንድ ፡ ነበርሁ ፡ በ
መቅደስ ፡ ሳስተምር ፡ አልያዛችሁኝምም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ መ
ጻሕፍት ፡ ይፈጸሙ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡፡ ሁሉም ፡ ትተውት ፡ ሸ
ሹ ፡፡ አንድ ፡ ጐበዝም ፡ በራቁትነቱ ፡ ላይ ፡ ነጸላ ፡ የለበሰ ፡
ይከተለው ፡ ነበር ፡፡ ጐበዛዝትም ፡ ያዙት ፡፡ እርሱም ፡ ነጸላ
ውን ፡ ትቶ ፡ ራቁቱን ፡ ከርሳቸው ፡ አመለጠ ፡፡ የሱስንም ፡
ይዘው ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቃ ፡ ሔዱ ፡፡ የካህናትም ፡ አለ
ቆች ፡ ሽማግሎችም ፡ ጻፎችም ፡ ሁሉ ፡ ወደርሱ ፡ ተሰበሰ
ቡ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ ከሩቅ ፡ ይከተለው ፡ ነበር ፡ እስከ ፡ ካህና
ቱ ፡ አለቃ ፡ ቤት ፡ ድረስ ፡፡ ከሎላልት ፡ ጋራም ፡ ተቀምጦ ፡

ነበር ፡ በሳትም ፡ ይሞቅ ፡ ነበር ፡፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ግን ፡
ሸንጎም ፡ ሁሉ ፡ ምስክርን ፡ ይሹ ፡ ነበሩ ፡ የሱስን ፡ ሊገሉ
ት ፡፡ አላገኙምም ፡፡ ብዙ ፡ በሐሰት ፡ ይመሰክሩበት ፡ ነበሩ
ና ፡ ምስክርነታቸውም ፡ አልተሰማማም ፡፡ ሰዎችም ፡ ተነ
ሡ ፡ ባሰትም ፡ መሰከሩበት ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ እኛ ፡ ሲል ፡
ሰማነው ፡፡ ኤኔ ፡ ይህነን ፡ እጅ ፡ የሰራውን ፡ መቅደስ ፡ አፈ
ርሳለሁ ፡፡ በሶስተኛ ፡ ቀንም ፡ ሌላውን ፡ በጅ ፡ ያልተሰራው
ን ፡ እሠራለሁ ፡፡ እንዲሁም ፡ ምስክራቸው ፡ አልተሰማማ
ችም ፡፡ የካህናትም ፡ አለቃ ፡ በማኸል ፡ ቆመ ፡ የሱስንም ፡
ጠየቀ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አንዳች ፡ አትመልስምን ፡፡ እሌህ ፡
ባንተ ፡ ምን ፡ ይመሰክሩብኻል ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡
ነበር ፡ አንዳችም ፡ አልመለሰም ፡፡ ደግሞ ፡ ጠየቀው ፡ የካ
ህናት ፡ አለቃ ፡ አለውም ፡፡ አንተን ፡ ክርስቶስ ፡ ነኽ ፡ የተባ
ረከው ፡ ልጅ ፡፡ የሱስም ፡ አለ ፡፡ እኔ ፡ ነኝ ፡፡ የሰውንም ፡ ል
ጅ ፡ በኃይል ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጦ ፡ ከሰማይ ፡ ደመናም ፡ ጋራ ፡
ሲመጣ ፡ ታዩ ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ፡፡ የካህናት ፡ አለቃ ፡ ግን ፡
ልብሱን ፡ ቀደደ ፡ አለም ፡፡ ደግሞ ፡ ምስክሮችን ፡ ምን ፡ ያ
ሻናል ፡፡ ስድቡን ፡ ሰማችሁ ፡፡ ምን ፡ ይምስላችኋል ፡፡ ሁሉ
ም ፡ ሞት ፡ እንዲገባው ፡ ፈረዱበት ፡፡ ሰዎችም ፡ ይተፉበት ፡
ፊቱንም ፡ ሸፈነው ፡ ይጸፉት ፡ ይሉትም ፡ ጀመሩ ፡ ትንቢት ፡
ተናገር ፡፡ ሎላልትም ፡ ይጸፉት ፡ ነበሩ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ በታች
ኛው ፡ ቤት ፡ ሳለ ፡ ከካህናት ፡ አለቃ ፡ ባሮች ፡ አንዲቱ ፡ መ
ጣች ፡፡ ጴጥሮስንም ፡ በሳት ፡ ይሞቅ ፡ ዘንድ ፡ ተቀምጦ ፡ ብ
ታየው ፡ ተመለከተችው ፡ አለችም ፡፡ አንተም ፡ ደግመኽ ፡
ከናዝሬቱ ፡ ከየሱስ ፡ ጋራ ፡ ነበርኽ ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ካደ ፡ እ
ንደይህ ፡ ሲል ፡፡ አላውቅም ፡ አንችም ፡ የምትዪውን ፡ አላስ
ተውልም ፡፡ ወደ ፡ ሚደም ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ወጣ ፡፡ ደሮ
ም ፡ ጮኸ ፡፡ ባርያዪቱም ፡ ደግማ ፡ አየችው ፡ ከዚያም ፡ ለ
ቆሙቱ ፡ ትል ፡ ጀመረች ፡፡ ይኽም ፡ ከርሳቸው ፡ ወገን ፡ ነው ፡፡
እርሱ ፡ ግን ፡ ደግሞ ፡ ካደ ፡፡ ጥቂትም ፡ ቈይተው ፡ የቆሙ
ት ፡ ጴጥሮስን ፡ ደግሞ ፡ አሉት ፡፡ በውነት ፡ አንተ ፡ ከርሳቸ
ው ፡ ወገን ፡ ነኽ ፡፡ አንተም ፡ ደግመኽ ፡ የገሊላ ፡ ሰው ፡ ነኽ



ና ፡፡ አፍህም ፡ አፈቸውን ፡ ይመስላል ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ይረ
ገም ፡ ይምልም ፡ ጀመረ ፡፡ እኔ ፡ ይህነን ፡ ሰው ፡ የምትሉት
ን ፡ አላውቀውም ፡ ሲል ፡፡ ደግሞም ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ደሮ ፡
ጮኸ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ የሱስ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ አሰበ ፡፡ ደሮ ፡
ሁለተግዜ ፡ ሳይጮኽ ፡ ሶስተግዜ ፡ እንድትክደኝ ፡፡ ነገሩንም ፡
ባሰበ ፡ ጊዜ ፡ አለቀሰ ፡፡

ፈሲካውን ፡ የሚቀድም ፡ መክሰኞ ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ ኢሳይያስ ፡ ፶፥ ፯—፲፩፡፡

እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ጆሮ ፡ ከፈተልኝ ፡ እኔም ፡ እን
ቢ ፡ አላልሁም ፡፡ ወደ ፡ ኋላዬም ፡ አልተመለስሁም ፡፡ ሥጋዬ
ን ፡ ለገራፎች ፡ ሰጠሁ ፡ ጕንጫዬንም ፡ ለሚጸፉኝ ፡፡ ፊቴንም ፡
አልመለስሁም ፡ ከሚያሳፍሩኝ ፡ ከሚተፉብኝም ፡፡ እግዚ
አብሔር ፡ አምላክ ፡ ረጅ ፡ ነውና ፡ ስለዚኽ ፡ አላፍርም ፡፡
ስለዚኽ ፡ ፊቴን ፡ እንደ ፡ ብልጭት ፡ ደንጊያ ፡ አደረግሁ ፡ እ
ኔም ፡ እንደላፍር ፡ አውቃለሁ ፡፡ የሚያጸድቀኝ ፡ ቅርብ ፡ ነ
ውና ፡ የሚቃወመኝ ፡ ማነው ፡፡ ባንድ ፡ እንቁም ፡፡ ማነው ፡
አይሆንም ፡ የሚለኝ ፡፡ ወደኔ ፡ ይቅረብ ፡፡ እነሆ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላክ ፡ ረጅ ፡ ነው ፡ ማን ፡ ይፈርድብኛል ፡፡ እነሆ ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጀሉ ፡ ብልም ፡ ይበላቸዋል ፡፡ ማነ
ው ፡ ከላንት ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ የባርያውን ፡ ቃ
ል ፡ የሚሰማ ፡፡ በጨለማ ፡ የሔደ ፡ ብርሃንም ፡ አልነበረለ
ትም ፡፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ተስፋ ፡ ያድርግ ፡ ባምላ
ኩም ፡ ይጠጋ ፡፡ እነሆ ፡ እላንት ፡ ሁላችሁ ፡ እሳት ፡ የምታነ
ዱ ፡ እሳትም ፡ ታጥቃችሁ ፡ በሳታችሁ ፡ ብርሃን ፡ ሒዱ ፡ ባ
ነደዳችሁትም ፡ ነበልባል ፡፡ ይኽ ፡ ከጄ ፡ ይደርስባችኋል ፡ በመ
ከራ ፡ ትተኛላችሁ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማርቆስ ፡ ፲፭፥ ፩—፴፱፡፡

የዚያን ፡ ጊዜውን ፡ ሲጸባ ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ከሽማ
ግሎች ፡ ከጻፎችም ፡ ጋራ ፡ ሸንጎም ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡ ፡፡ የ
ሱስንም ፡ አሠሩት ፡ ወሰዱትም ፡ ለጲላጦስም ፡ አሳልፈው ፡

ሰጡት ፡፡ ጲላጦስም ፡ ጠየቀው ፡፡ አንተን ፡ ነኽ ፡ የአይሁድ ፡
ንጉሥ ፡ ሲል ፡፡ እርሱም ፡ መለሰ ፡ አለውም ፡፡ አንተ ፡ አል
ኽ ፡፡ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ እጅግ ፡ አጣሉት ፡፡ እርሱ ፡ ግ
ን ፡ አንዳች ፡ አልመለሰም ፡፡ ጲላጦስም ፡ ደግሞ ፡ ጠየቀ
ው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አንዳች ፡ አትመልስምን ፡፡ እይ ፡ ስን
ት ፡ ይመሰክሩብኻል ፡፡ የሱስ ፡ ግን ፡ ገናም ፡ አንዳች ፡ አል
መለሰለትም ፡ ጲላጦስ ፡ እስኪደነቅ ፡ ድረስ ፡፡ በየበዓሉ
ም ፡ አንዱን ፡ የታሠረውን ፡ ይፈታላቸው ፡ ነበር ፡ የወደዱ
ትን ፡፡ በርባንም ፡ የሚሉት ፡ ነበር ፡ ከርሱ ፡ አብረው ፡ ከሸፈ
ጡ ፡ ጋራ ፡ ታሥሮ ፡ የነበረ ፡ በሸፍጥ ፡ መግደልን ፡ አድርገው ፡
ነበረና ፡፡ ሕዝቡም ፡ ጮኹ ፡ ይለምኑም ፡ ጀመረ ፡ እንደ ፡
ወትሮ ፡ ያደርግላቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ጲላጦስ ፡ ግን ፡ መለሰላቸ
ው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ የአይሁድን ፡ ንጉሥ ፡ እፈታላችሁ ፡
ዘንድ ፡ ትወዳላችሁን ፡፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ በቅንዓት ፡ አ
ሳልፈው ፡ እንደ ፡ ሰጡት ፡ ያውቅ ፡ ነበረና ፡፡ የካህናት ፡ አለ
ቆችም ፡ ሕዝቡን ፡ አነሡ ፡ ይለምኑት ፡ ዘንድ ፡ በርባንን ፡ ቢ
ፈታላቸው ፡ እንዲሻል ፡፡ ጲላጦስም ፡ መለሰ ፡ ደግሞም ፡
አላቸው ፡፡ ምን ፡ ትሻላችሁ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ሆ
ነ ፡ በምትሉት ፡ አደርግበት ፡ ዘንድ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ደግ
ሞ ፡ ጮሁ ፡ ኢያሉ ፡ ስቀለው ፡፡ ጲላጦስም ፡ አላቸው ፡ ም
ን ፡ ክፋ ፡ አደረገ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ጮኽታቸውን ፡ አበዙ ፡
ስቀለው ፡ ሲሉ ፡፡ ጲላጦስም ፡ ሕዝቡን ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸው ፡
ዘንድ ፡ ወደደ ፡ በርባንንም ፡ ፈታላቸው ፡፡ የሱስንም ፡ ገር
ፎ ፡ ሰጣቸው ፡ ይሰቀል ፡ ዘንድ ፡፡ ጭፍሮችም ፡ ወደ ፡ ፍር
ድ ፡ ስፍራ ፡ ይዘውት ፡ ሔዱ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ውሥጥ ፡ ጭፍሪ
ንም ፡ ሁሉ ፡ አከማቹበት ፡፡ ቀይ ፡ ሐርም ፡ አለበሱት ፡፡ የ
ሾኽም ፡ ዘውድ ፡ ጐንጕኑና ፡ በላዩ ፡ ደፉበት ፡፡ ሰላምም ፡
ይሰጡት ፡ ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ደኅንነት ፡ ይሁንልህ ፡
የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡፡ ራሱንም ፡ በዘንግ ፡ መቱት ፡፡ ተ
ፋበትም ፡ በጕልበታቸውም ፡ ተንበርክከው ፡ ሰገዱለት ፡፡ ከ
ተሣለቁበትም ፡ በኋላ ፡ ቀዩን ፡ ሐር ፡ ገፈፉት ፡ ልብሱንም ፡
አለበሱት ፡፡ ሊሰቅሉትም ፡ አወጡት ፡፡ አንድም ፡ መንገ



ድ ፡ አላፊውን ፡ ሲሞን ፡ የቀሬኑ ፡ የሚባል ፡ ከሜዳ ፡ ሲ
መጣ ፡ እርሱም ፡ የስክንድሮስና ፡ የሩፎስ ፡ አባት ፡፡ መስቀ
ሉን ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡ አሉት ፡፡ ጎልጎታም ፡ ማለቱ ፡ የ
ራስ ፡ አጽንት ፡ ወደሚባል ፡ ስፍራ ፡ ወሰዱት ፡፡ በከርቤም ፡
የተቀላቀለውን ፡ ወይን ፡ ሰጡት ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱ ፡
ግን ፡ አልተቀበለውም ፡፡ በሰቀሉትም ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ተካ
ፈሉ ፡፡ ዕፃም ፡ ተጣጣሉበት ፡ ሁሉ ፡ ኢየራሱ ፡ የደረሰው
ን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡፡ በሰቀሉትም ፡ ጊዜ ፡ ሦስተኛ ፡ ሰዓት ፡
ነበረ ፡፡ የፍርዱም ፡ መክንያት ፡ ተጽፎበት ፡ ነበር ፡ እን
ዲህ ፡ ሲል ፡፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡፡ ሁለት ፡ ወንበደችንም ፡ ሰ
ቀሉ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡፡ አንዱን ፡ በቀኝ ፡ ሁለተኛውንም ፡ በግ
ራው ፡፡ መጻፉም ፡ ተፈጸመ ፡ የሚል ፡፡ ከኃጥኣን ፡ ጋራ ፡
ተቈጠረ ፡፡ የሚያልፉም ፡ ሰደቡት ፡ ራሳቸውንም ፡ ነቀነቁ ፡፡
እንዲህም ፡ አሉ ፡፡ እወይ ፡፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ የምታፈርስ ፡
ሆይ ፡ በሦስት ፡ ቀንም ፡ የምትሠራው ፡፡ ራስኽን ፡ አድን ፡
ከመስቀልም ፡ ውረድ ፡፡ እንዲሁም ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡
ደግሞ ፡ አፌዘው ፡ እርሱ ፡ በርሳቸውም ፡ ከጻፎች ፡ ጋራ ፡ እን
ዲህ ፡ ብለው ፡ ተባበሉ ፡፡ ሌሎችን ፡ አዳነ ፡፡ ራሱን ፡ ሊያድ
ን ፡ አልቻለውም ፡፡ ክርስቶስ ፡ የእሥራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዛሬ ፡
ከመስቀል ፡ ይውረድ ፡ አይተን ፡ እንድናምን ፡፡ ከርሱም ፡
ጋራ ፡ የተሰቀሉት ፡ ተላገዱት ፡፡ ስድስተኛ ፡ ሰዓትም ፡ በሆነ ፡
ጊዜ ፡ ጨለማ ፡ ሆነ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ዘጠነኛ ፡
ሰዓት ፡ ድረስ ፡፡ በዘጠነኛውም ፡ ሰዓት ፡ የሱስ ፡ በታላቅ ፡ ቃ
ል ፡ ጮኸ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ኤሎሄ ፡ ኤሎሄ ፡ ለማ ፡ ሰበኽ
ታኒ ፡፡ ትርጓሜው ፡ የሚሆን ፡፡ አምላኬ ፡ አምላኬ ፡ ለም
ን ፡ ተውኸኝ ፡፡ ሰዎችም ፡ ከቆሙት ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ አሉ ፡
እነሆ ፡ ኤልያስን ፡ ይጸራል ፡፡ አንድም ፡ ፈጠነ ፡ ሰፍነጉንም ፡
መጣጣ ፡ መላበት ፤ በዘንግም ፡ አደረገው ፡ አጠጣውም ፡
እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ተዉት ፡ እንይ ፡ ኤልያስ ፡ መጥቶ ፡ ያወር
ደው ፡ እንደሆን ፡፡ የሱስ ፡ ግን ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ጮኸ ፡ ነፍሱ
ንም ፡ ሰጠ ፡፡ የመቅደሱም ፡ መጋረጃ ፡ ለሁለት ፡ ተቀደደ ፡
ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡፡ የመቶውም ፡ አለቃ ፡ ባንጻሩ ፡ ቁሞ ፡

የነበረው ፡ እንደሆ ፡ ጨኾ ፡ ነፍሱን ፡ አንደ ፡ ሰጠ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አለ ፡፡ በውነት ፡ ደህ ፡ ሰው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፡፡

---

## ፈሲካውን ፡ የሚቀድም ፡ ርቡዕ ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ዕብራውያን ፡ ፱፡ ፲፫፡—፳፰፡፡

ሥርዓትም ፡ ወደለች ፡ የሠራት ፡ ሞት ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ በግድ ፡ ይፈለጋል ፡፡ ሥርዓት ፡ በሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ጸንታለችና ፡፡ ትረባም ፡ ዘንድ ፡ አይቻላትም ፡ በሠራት ፡ ሕይወት ፡ ሁሉ ፡፡ ስለዚኽም ፡ የፊተኛይቱ ፡ ያለ ፡ ደም ፡ አልተገለጠችም ፡፡ ሙሴም ፡ የኦሪትን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ለሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ የበሬና ፡ የፍየል ፡ ደም ፡ ወሰደ ፡ ውኃም ፡ ቀይ ፡ ጸጕርም ፡ የመርጨት ፡ ቅጠልም ፡፡ በመጻፉም ፡ ረጨው ፡ በሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡፡ እንደሆ ፡ ሲል ፡፡ ይኽ ፡ ነው ፡ የኪዳኑ ፡ ደም ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዛችሁት ፡፡ እንደሁም ፡ ድንኳኑን ፡ የማገልገልንም ፡ እቃ ፡ ሁሉ ፡ በደም ፡ ረጫቸው ፡፡ በኦሪት ፡ ሕግም ፡ ሁሉ ፡ በደም ፡ ይነጻልና ፡፡ ደምም ፡ ሳይፈስ ፡ ስርየት ፡ የለም ፡፡ የግድም ፡ የሰማያዊት ፡ ነገር ፡ ምሳሌ ፡ በዚኽ ፡ ትነጻ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡፡ ሰማያዊቱ ፡ ግን ፡ ከዚኽ ፡ በምትበልጠው ፡ መሥዋዕት ፡፡ ክርስቶስ ፡ በጅ ፡ ወደ ፡ ተሰራው ፡ መቅደስ ፡ የውነተኛው ፡ ምሳሌ ፡ ወደ ፡ ሆነው ፡ የገባ ፡ አይደለውምና ፡፡ ወደርስዋ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ገባ ፡ እንጅ ፡፡ ዛሬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስለኛ ፡ ይታይልን ፡ ዘንድ ፡፡ ራሱንም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ የሚያቀርብ ፡ እንደ ይሆን ፡፡ የካህናት ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ እንደ ገባ ፡ ባመት ፡ ባመት ፡ በሌላው ፡ ደም ፡፡ (ያስ ፡ ባይሆን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ሕማማት ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ይገባው ፡ ነበረ ፡ ዓለም ፡ ከተፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡፡) ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ አንደግዜ ፡ ተገለጠ ፡ በራሱ ፡ መሥዋዕት ፡ ኃጢአትን ፡ ይሽር ፡ ዘንድ ፡፡ በሰዎችም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ አንደግዜ ፡ ይሞቱ ፡ ዘንድ ፡፡ ከሞቱ ፡ በኋላም ፡ ፍርድ ፡ እንደለባቸው ፡፡ እንደሁም ፡ ክርስቶስ ፡ ራሱን ፡ አንደግዜ ፡ አቀረበ ፡ የብዙ ፡



ሰዎችን ፡ ኃጢአት ፡ ያስወግድ ፡ ዘንድ ፡፡ ሁለተኛም ፡ ጊዜ ፡ ያለ ፡ ኃጢአት ፡ ይታያል ፡ ደጅ ፡ ለሚጸኑት ፡ ለመድኃኒት ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡ ሉቃስ ፡ ፳፪፡ ፩፡—፳፩፡፡

በዓለ ፡ ፋእትም ፡ ፈሲካ ፡ የሚባል ፡ ቀረበ ፡፡ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ጻፎችም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያጠፉት ፡ ዘንድ ፡ ይሹ ፡ ነበረ ፡፡ ሕዝቡን ፡ ይፈሩ ፡ ነበሩና ፡፡ ሰይጣንም ፡ በይሁዳ ፡ አስቆሮታዊ ፡ በሚባል ፡ ገባ ፡፡ ካሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ቍጥር ፡ በነበረው ፡፡ ሔደም ፡ ከካህናትም ፡ አለቆች ፡ ከወታደር ፡ አለቆችም ፡ ጋራ ፡ ተናገገረ ፡፡ እርሱን ፡ እንዴት ፡ ያሲዛቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ደስም ፡ አላቸው ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ቍረጡ ፡ ብር ፡ ይሰጡት ፡ ዘንድ ፡፡ ተስፋም ፡ ሰጣቸው ፡፡ ጊዜም ፡ ይሻ ፡ ነበረ ፡ ሕዝብ ፡ ሳያውቅ ፡ ያሲዛቸው ፡ ዘንድ ፡፡ በዓለ ፡ ፋእትም ፡ መጣ ፡ ፈሲካ ፡ ይታረድበት ፡ ዘንድ ፡ ይገባ ፡ የነበረው ፡፡ ጴጥሮስንና ፡ ዮሐንስንም ፡ላከ ፡ እንደሆ ፡ ሲላቸው ፡፡ ሒዱችሁ ፡ ፈሲካን ፡ አዘጋጁልን ፡ እንበላ ፡ ዘንድ ፡፡ እርሳቸውም ፡ አሉት ፡፡ ወዴት ፡ ትሻለኽ ፡ እናሰናድ ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱም ፡ አላቸው ፡፡ እነሆ ፡ ወደገር ፡ ስትገቡ ፡ ጊዜ ፡ ማድጋ ፡ ውኃ ፡ የሚሸከም ፡ ሰው ፡ ያገኛችኋል ፡፡ ወደሚገባው ፡ ቤትም ፡ ተከተሉት ፡፡ ለቤቱም ፡ ጌታ ፡ በሉት ፡፡ መምህር ፡ ይልኻል ፡፡ ወዴት ፡ ነው ፡ የዕረፍት ፡ ስፍራ ፡ ፈሲካን ፡ የምበላበት ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ጋራ ፡፡ እርሱም ፡ ታላቅ ፡ የተነጸፈችን ፡ አደራሽ ፡ ያሳያችኋል ፡፡ ከዚያ ፡ አሰናዱ ፡፡ ሔዱም ፡ እንደላቸውም ፡ አገኙ ፡፡ ፈሲካንም ፡ አከናወኑ ፡፡ ጊዜውም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ለመብል ፡ ተቀመጠ ፡፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ሐዋርያት ፡፡ አላቸውም ፡፡ ከሕማሜ ፡ በፊት ፡ ይህንን ፡ ፈሲካ ፡ ከላንተ ፡ ጋራ ፡ እበላ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ተናፈቅሁ ፡፡ እላችኋለሁና ፡ ይህንን ፡ ደግሞ ፡ እንደልበላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡፡ ጽዋንም ፡ ተቀበለ ፡ አመሰገነም ፡ አለም ፡፡ ይህንን ፡ እንኩ ፡ በመኻከላችሁም ፡ ተካፈሉት ፡፡ እላችኋለሁና ፡ ደግሜ ፡ ከወይን ፡ ፍሬ ፡ እንደልጠጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እስክትመጻ ፡ ድረስ ፡፡ እንጀራም ፡ ወሰደ ፡ አመሰገነም ፡ ቍረሰም ፡ ሰጣቸውም ፡

እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ይኸ ፡ ነው ፡ ሥጋዬ ፡ ስለላንት ፡ የሚሰጠው ፡፡
ይህነን ፡ አድርጉት ፡ እኔን ፡ ለመታሰብ ፡፡ ደግሞም ፡ እንዲሁ ፡
ጽዋውን ፡ ከራት ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ይህ ፡ ጽዋ ፡ አዲ
ስ ፡ ሥርዓት ፡ ነው ፡ በደሜ ፡ ስለላንት ፡ በሚፈሰ ፡፡ ነገር ፡ ግ
ን ፡ እነሆ ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጠኝ ፡ እጁ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡ በ
ማዕድ ፡ ላይ ፡፡ የሰው ፡ ልጅም ፡ እንደ ፡ ተቈረጠለት ፡ ይሔ
ዳል ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ወዮለት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ አሳልፎ ፡ ለሚሰ
ጠው ፡፡ እርሶ ፡ በርሳቸውም ፡ ይጠያየቁ ፡ ጀመሩ ፡ እንጃ ፡
ከርሳቸው ፡ ይህነን ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ማነው ፡፡ በ
መካከላቸውም ፡ ደግሞ ፡ ክርክር ፡ ነበረ ፡ ከርሳቸው ፡ ታላ
ቅ ፡ ሁኖ ፡ የሚመስለው ፡፡ እርሶ ፡ ግን ፡ አላቸው ፡፡ የአሕዛ
ብ ፡ ነገሥታት ፡ እርሳቸው ፡ ይገዝዋቸዋል ፡፡ ሥልጣንም ፡ ያ
ለባቸው ፡ ቸርነት ፡ አድራጎች ፡ ይባላሉ ፡፡ እላንት ፡ ግን ፡ እን
ዲህ ፡ አይደለም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከላንት ፡ ታላቁ ፡ እንደ ፡ ታና
ሽ ፡ ይሁን ፡ አለቃውም ፡ እንደ ፡ አገልጋይ ፡፡ ማን ፡ ይበልጣ
ልና ፡፡ ተቀምጦ ፡ የሚበላን ፡ ወይስ ፡ የሚያገለግል ፡፡ ተቀ
ምጦ ፡ የሚበላ ፡ አይደለምን ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ በመካከላችሁ ፡
እንደ ፡ አገልጋይ ፡ ነኝ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እላንት ፡ ናችሁ ፡ ከኔ ፡ ጋ
ራ ፡ በፈተናዬ ፡ የታገሣችሁ ፡፡ እኔም ፡ መንግሥትን ፡ አዘጋ
ጅላችኋለሁ ፡ አባቴ ፡ ለኔ ፡ እንደዘጋጀ ፡፡ ትበሉ ፡ ትጠጡም ፡
ዘንድ ፡ በማዕዴ ፡ በመንግሥቴ ፡፡ በዙፋኖትም ፡ ትቀመጡ ፡
ዘንድ ፡ ባሥራ ፡ ሁለቱም ፡ በእሥራኤል ፡ ነገዶች ፡ ትፈርዱ ፡
ዘንድ ፡፡ ጌታም ፡ አለ ፡፡ ሲሞን ፡ ሲሞን ፡፡ እነሆ ፡ ሰይጣን ፡
እንደ ፡ ስንዴ ፡ ሊነፋችሁ ፡ ፈለጋችሁ ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ ስላንተ ፡
ለመንሁ ፡፡ ሃይማኖትኽ ፡ እንዳታልቅ ፡፡ አንተም ፡ በተመለ
ስኽ ፡ ጊዜ ፡ ወንድሞችኽን ፡ አጽና ፡፡ እርሱም ፡ አለው ፡፡ አ
ቤቱ ፡ እኔ ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ እሥራት ፡
ወደ ፡ ሞትም ፡ እሔድ ፡ ዘንድ ፡፡ እርሶም ፡ አለ ፡ እልኻለ
ሁ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሆይ ፡፡ ዛሬ ፡ ደሮ ፡ እንዳይጮኽ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡
እስክትክደኝ ፡ ድረስ ፡ እንደታውቀኝ ፡፡ አላቸውም ፡፡ በላ
ክኋችሁ ፡ ጊዜ ፡ ያለ ፡ አቍማደ ፡ ያለ ፡ ከረጢትም ፡ ያለ ፡ ጫ
ማም ፡ አንዳች ፡ ጕደለባችሁን ፡፡ እርሳቸውም ፡ አሉ ፡፡ አን



ዳች ፡ ስንኳ ፡፡ አላቸውም ፡፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ አቍማደ ፡ ያለው ፡
ይውሰድ ፡፡ እንዲሁም ፡ ከረጢት ፡፡ ሰይፍ ፡ የሌለውም ፡ ል
ብሱን ፡ ይሸጥና ፡ ሰይፍ ፡ ይግዛ ፡፡ እላችኋለሁና ፡ ይኸ ፡ የተ
ጻፈው ፡ ደግሞ ፡ ይፈጸምብኝ ፡ ዘንድ ፡ አለ ፡፡ ከኃጥኣን ፡ ጋ
ራ ፡ ተቈጠረ ፡ ተብሎ ፡፡ ስለኔ ፡ የተጻፈው ፡ ፍጻሜ ፡ አለው
ና ፡፡ እርሳቸውም ፡ አሉ ፡፡ አቤቱ ፡ እነሆ ፡ ከዚህ ፡ ሁለት ፡ ሰ
ይፎች ፡ አሉ ፡፡ እርሱም ፡ አላቸው ፡ ይበቃል ፡፡ ወጥቶም ፡ እ
ንደ ፡ ልማዱ ፡ ሔደ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡፡ ደቀ ፡ መዛሙር
ቱም ፡ ደግሞ ፡ ተከተሉት ፡፡ ወደ ፡ ቦታውም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡
አላቸው ፡፡ ጸልዩ ፡ ወደ ፡ ፈተና ፡ እንዳትገቡ ፡፡ እርሱም ፡ ከ
ርሳቸው ፡ ራቀ ፡ የደንጊያ ፡ ውርወራ ፡ ያህል ፡፡ በጕልበቱም ፡
ተምበረከከና ፡ ጸለየ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡፡ ብት
ወድስ ፡ ከኔ ፡ አስለፍ ፡ ይህችን ፡ ጽዋ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ፈቃዴ ፡
አይደለም ፡፡ ፈቃድኽ ፡ ትሁን ፡ እንጅ ፡፡ ከሰማይም ፡ መል
አክ ፡ ታየለት ፡ ሊያጸናው ፡፡ በጻረም ፡ ሲጋደል ፡ በጸሎቱ ፡
በረታ ፡፡ ወዙም ፡ እንደ ፡ ደም ፡ ነጠብጣብ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
ወረደ ፡፡ ከጸሎትም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡
መጣ ፡ ከኃዘንም ፡ የተነሣ ፡ ተኝተው ፡ አገኛቸው ፡፡ አላቸ
ውም ፡፡ ለምን ፡ ትተኛላችሁ ፡፡ ተነሡና ፡ ጸልዩ ፡ ወደ ፡ ፈተ
ና ፡ እንዳትገቡ ፡፡ እርሶም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ እነሆ ፡ ሰዎች ፡ መ
ጡ ፡፡ ይሁዳም ፡ የሚባል ፡ ካሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡ በፊታቸ
ው ፡ ሔደ ፡፡ ወደ ፡ የሶስም ፡ ሊስመው ፡ ቀረበ ፡፡ የሶ
ስ ፡ ግን ፡ አለው ፡፡ ይሁዳ ፡ ሆይ ፡ ስመህን ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ አ
ሳልፈኽ ፡ ትሰጣለኽ ፡፡ ከርሶም ፡ ጋራ ፡ የነበሩ ፡ የሚሆነው
ን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ አሉት ፡፡ አቤቱ ፡ በሰይፍ ፡ እንምታን ፡፡ ከር
ሳቸውም ፡ አንዱ ፡ የካህናቱን ፡ አለቃ ፡ ባርያ ፡ መታ ፡ ቀኝ ፡
ጀሮውንም ፡ ቈረጠው ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡፡ አሁ
ንስ ፡ ተው ፡፡ ጀሮውንም ፡ ዳሶ ፡ ፈወሰው ፡፡ የሱስም ፡ አለ ፡
ወደርሶ ፡ ለመጡት ፡ ለካህናት ፡ አለቆች ፡ ለመቅደስም ፡
አዛጆች ፡ ለሽማግሎችም ፡፡ በሌባ ፡ ላይ ፡ እንድትወጡን ፡
በሰይፍና ፡ በበትር ፡ ወጣችሁ ፡፡ ሁለግዜ ፡ ከላንት ፡ ጋራ ፡ ነ
በርሁ ፡ በመቅደስ ፡ እጃችሁንም ፡ አልዘረጋችሁብኝም ፡፡ ነ

ገር ፡ ግን ፡ ይህች ፡ ጊዜያችሁ ፡ ናት ፡ የጨለማውም ፡ ሥልጣን ። ወሰዱትም ፡ ይዘውትም ፡ መጡ ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቃ ፡ ቤትም ፡ አገቡት ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ ከሩቅ ፡ ተከተለው ። እሳትም ፡ አነደዱ ፡ በቤቱ ፡ መኻከል ። ባንድም ፡ በተቀመጡ ፡ ጊዜ ፡ ጴጥሮስም ፡ በማኽላቸው ፡ ተቀመጠ ። አንዲት ፡ ባሪያም ፡ አየችው ፡ ወደ ፡ ብርሃኑ ፡ ተቀምጦ ፡ በጣምም ፡ ተመለከተችው ፡ አለችም ። ይኽ ፡ ደግሞ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ካደው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። አንቺ ፡ ሴት ፡ አላውቀውም ። ጥቂትም ፡ ቈይቶ ፡ ሌላው ፡ አየው ፡ አለም ። አንተም ፡ ደግሞ ፡ ከርሳቸው ፡ ወገን ፡ ነኽ ። ጴጥሮስም ፡ አለው ። አንተ ፡ ሰው ፡ እኔ ፡ አይደለሁም ። ካንድ ፡ ሰዓትም ፡ በኋላ ፡ ሌላው ፡ ነገርን ፡ አጸናበት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። በውነት ፡ ይኽ ፡ ደግሞ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ገሊላዊ ፡ ነውና ። ጴጥሮስም ፡ አለ ። አንተ ፡ ሰው ፡ የምትለውን ፡ አላውቅም ። ድንገትም ፡ እርሱ ፡ ሲናገር ፡ ዶሮ ፡ ጮኸ ። ጌታም ፡ ተመልሶ ፡ ጴጥሮስን ፡ አየ ። ጴጥሮስም ፡ የጌታን ፡ ነገር ፡ አሰበ ፡ እንዳለው ። ዶሮ ፡ ሳይጮኽ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደኛለኽ ። ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጣ ፡ መራራ ፡ ልቅሶም ፡ አለቀሰ ። የሱስንም ፡ ያያዙት ፡ ሰዎች ፡ አፌዙበት ፡ መቱትም ። ሸፈነውም ፡ ፊቱን ፡ ጸፉት ። እንዲህ ፡ ሲሉም ፡ ጠየቁት ፡ ንገረን ፡ ማነው ፡ የመታኽ ። ሌላም ፡ እጅግ ፡ ነገር ፡ አሉት ፡ ኢየሰደቡት ። ቀንም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ተከማቹ ፡ የሕዝቡ ፡ ሽማግሎች ፡ የካህናቱ ፡ አለቆች ፡ ጻፎችም ። ወደ ፡ ሸንጎቻቸውም ፡ አወጡት ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆንኽ ፡ ንገረን ። አላቸውም ። ብነግራችሁም ፡ አታምኑኝም ። ደግሞም ፡ ብጠይቃችሁ ፡ አትመልሱልኝም ፡ አትፈቱኝምም ። ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ በኃይሉ ፡ ቀኝ ፡ የሚቀመጥ ፡ ይሆናል ። ሁሉም ፡ አሉ ። እንኪያስ ፡ አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅን ፡ ነኽ ። እርሱም ፡ አላቸው ። እላንት ፡ ትላላችሁ ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ። እርሳቸውም ፡ አሉ ። ምን ፡ እንሻለን ፡ ወደ ፡ ምስክሮች ። እኛ ፡ ካፉ ፡ ሰምተናልና ።



## ፈሲካውን ፡ የሚቀድም ፡ አሙስ ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፤ ቆሮንቶስ ፡ ፲፩፤ ፲፯—፴፬።

በዚኽ ፡ በማዛችሁ ፡ ግን ፡ አላመሰግናችሁም ። ላሚሻል ፡ አይደለም ፡ ለሚከፋ ፡ እንጂ ፡ ትሰበሰባላችሁና ። አስቀድሞ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በተሰበሰባችሁ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ክርክር ፡ እንዳለባችሁ ፡ እሰማለሁና ፡ ከፊዩም ፡ አምነዋለሁ ። መለያየት ፡ በመኻከላችሁ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ጊዜ ፡ አለውና ። የተፈተኑት ፡ ይታወቁባችሁ ፡ ዘንድ ። እላንት ፡ ግን ፡ ወደንድ ፡ ስፍራ ፡ በተሰበሰባችሁ ፡ ጊዜ ፡ የጌታችነን ፡ እራት ፡ የምትበሉ ፡ አይደላችሁም ። ሁላችሁ ፡ ወደ ፡ ምሳ ፡ ትቀዳደማላችሁና ፡ ትበሉማላችሁና ፡ አንዱ ፡ ተርቦ ፡ አንዱም ፡ ሰክሮ ። ቤት ፡ የላችሁምን ፡ የምትበሉበት ፡ የምጠጡበትስ ። ወይስ ፡ የእግዚአብሔርንን ፡ ማኅበሮች ፡ ትንቃላችሁ ። አንዳች ፡ የሌላቸውንም ፡ ታሳፍራላችሁ ። ምንስ ፡ ልበላችሁ ። በዚኽ ፡ ላመስግናችሁን ። አላመሰግናችሁም ። እኔ ፡ ለላንት ፡ አሳልፌ ፡ የሰጠኋችሁትን ፡ ከጌታ ፡ ወስጀለሁና ። ጌታችን ፡ የሱስ ፡ በዚያች ፡ በተያዘባት ፡ ሌት ፡ እንጀራ ፡ አንደ ፡ ወሰደ ። ባመሰገነም ፡ ጊዜ ፡ ቈረሰው ። አለም ፡ እንኩ ፡ ብሉ ። ይኽ ፡ ነው ፡ ስለላንት ፡ የሚሰበር ፡ ሥጋዬ ። ይህነን ፡ እኔን ፡ ለመታሰብ ፡ አድርጉት ። እንዲሁም ፡ ጽዋውን ፡ ወሰደ ፡ ራታቸውን ፡ ከበሉ ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ይኽ ፡ ጽዋ ፡ አዲስ ፡ ሥርዓት ፡ ነው ፡ በደሜ ። ይህነን ፡ አድርጉ ፡ ስትጠጡት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ለመታሰቤ ። ይህነንም ፡ እንጀራ ፡ ስትበሉ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ይህነንም ፡ ጽዋ ፡ ስትጠጡ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ የጌታን ፡ ሞት ፡ አውሩ ፡ እርሱ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ። ስለዚኽም ፡ ይህነን ፡ እንጀራ ፡ የሚበላ ፡ ሁሉ ፡ የጌታንም ፡ ጽዋ ፡ የሚጠጣ ፡ ሳይገባው ፡ በጌታ ፡ ሥጋ ፡ በደሙም ፡ በደይ ፡ ይሆናል ። ሰውም ፡ ራሱን ፡ ይፈትን ፡ እንዲሁም ፡ ይኽን ፡ እንጀራ ፡ ይብላ ፡ ይኽንም ፡ ጽዋ ፡ ይጠጣ ። ሳይገባው ፡ ግን ፡ ቢበላ ፡ ቢጠጣም ፡ ለራሱ ፡ ኵነኔ ፡ ይበላል ፡ ይጠጣልም ።

የጌታን ፡ ሥጋ ፡ አይለይምና ፡፡ ስለዚኽም ፡ ከላንተ ፡ ብዙ ፡ ድውያን ፡ አሉ ፡ ደካሞችም ፡፡ ብዙም ፡ የተኙ ፡ አሉ ፡፡ በራሳችንም ፡ ብንፈርድ ፡ ባልተፈረደብነም ፡፡ ቢፈርድብነም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚገሥጽን ፡ ነው ፡፡ ከዓለም ፡ ጋራ ፡ እንዳንኰነን ፡ ስለዚኽም ፡ ወንድሞቼ ፡ ለመብላት ፡ በተሰበሰባችሁ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ይጠባበቅ ፡፡ ማናቸው ፡ ግን ፡ ከላንተ ፡ ቢራብ ፡ በቤቱ ፡ ይብላ ፡፡ ለፍርድ ፡ እንዳትሰበሰቡ ፡፡ የቀረውንም ፡ ነገር ፡ ወደላንት ፡ ስመጣ ፡ ጊዜ ፡ እሠራላችኋለሁ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ሉቃስ ፡ ፳፫፤ ፩፤—፵፱፡፡

ጉባኤያውም ፡ ሁሉ ፡ ተነሡ ፡ ወደ ፡ ጲላጦስም ፡ ወሰዱት ፡፡ ያጻሉትም ፡ ጀመሩ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ይህነን ፡ አገኘነ ፡ ሕዝብን ፡ ሲገለብጥ ፡፡ ግብርም ፡ ለቄሳር ፡ እንዳይሰጥ ፡ ይከለክላል ፡ እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ ንጉሥም ፡ ነኝ ፡ ሲል ፡፡ ጲላጦስም ፡ ጠየቀው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አንተን ፡ ነኽ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡፡ እርሱም ፡ መለሰለት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አንተ ፡ አልኽ ፡፡ ጲላጦስ ፡ ግን ፡ ለካህናት ፡ አለቆች ፡ ለተከማቹትም ፡ አለ ፡፡ በዚኽ ፡ ሰው ፡ አንዲት ፡ ምክንያት ፡ አላገኘሁም ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ በረቱ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ሕዝቡን ፡ ያውካል ፡ ኢያስተማረ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ከገሊላ ፡ ጀምሮ ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡፡ ጲላጦስ ፡ ግን ፡ ገሊላን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ጠየቀ ፡ እርሱ ፡ የገሊላ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብሎ ፡፡ ከሄሮድስ ፡ ግዛትም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባወቀ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሄሮድስ ፡ ሰደደው ፡፡ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ በዚያች ፡ ወራት ፡ በየሩሳሌም ፡ ነበረና ፡፡ ሄሮድስም ፡ የሱስን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለው ፡፡ ከብዙ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ያየው ፡ ዘንድ ፡ ይመኝ ፡ ነበረና ፡፡ እጅግ ፡ ነገር ፡ በርሱ ፡ ስለ ፡ ሰማ ፡፡ ተስፋም ፡ ያደርግ ፡ ነበረ ፡ ታምራት ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ የሚያደርጋትን ፡፡ እጅግ ፡ ነገርም ፡ ጠየቀው ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አልመለሰለትም ፡፡ የካህናትም ፡ አለቆች ፡ ጻፎችም ፡ ቆሙ ፡ እጅግም ፡ አጻሉት ፡፡ ሄሮድስም ፡ አቃለለው ፡ ከወታደሮቹ ፡



ጋራ ፡ አፌዙበትም ፡፡ ብልጭልጭ ፡ የሚልም ፡ ልብስ ፡ አለበሰው ፡ መልሶም ፡ ወደ ፡ ጲላጦስ ፡ ሰደደው ፡፡ ጲላጦስና ፡ ሄሮድስም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ወዳጆች ፡ ሆኑ ፡፡ ቀድሞ ፡ በማኸላቸው ፡ ጽል ፡ ነበረና ፡፡ ጲላጦስ ፡ ግን ፡ የካህናቱን ፡ አለቆች ፡ ጸራ ፡ የሕዝቡንም ፡ ታላላቆች ፡፡ አላቸውም ፡፡ ይህነን ፡ ሰው ፡ ወደኔ ፡ አመጣችሁት ፡ ሕዝቡን ፡ እንደሚገለብጥ ፡፡ በፊታችሁም ፡ እነሆ ፡ መረመርሁት ፡ በዚኽ ፡ ሰውም ፡ ምክንያትን ፡ አላገኘሁበትም ፡ በምታጣሉት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡፡ ሄሮድስ ፡ ስንኳ ፡፡ ወደርሱ ፡ ሰድጃችሁ ፡ ነበርሁና ፡ እነሆም ፡ ያደረገው ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ሞት ፡ የሚገባበት ፡፡ አሁንም ፡ ቀጥቼ ፡ ልፈታው ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ግድ ፡ ነበረበት ፡ በየበዓሉ ፡ አንዲን ፡ ሰው ፡ ይፈታላቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ይኽን ፡ አንሣ ፡፡ በርባንንም ፡ ፍታልን ፡፡ ያም ፡ ባገር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሸፍጥ ፡ ስለ ፡ መግደልም ፡ ወደ ፡ ግዞት ፡ ተጥሎ ፡ ነበረ ፡፡ ጲላጦስም ፡ ደግሞ ፡ ተናገራቸው ፡ የሱስንም ፡ ሊፈታ ፡ ወደደ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ስቀለው ፡ ስቀለው ፡፡ እርሱም ፡ ሶስተኛ ፡ ጊዜ ፡ አላቸው ፡፡ ይኽ ፡ ምን ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፡፡ ሞት ፡ የሚገባው ፡ ምክንያት ፡ አላገኘሁበትም ፡፡ ልቀጣውና ፡ ልፈታው ፡፡ እርሳው ፡ ግን ፡ የግድ ፡ አሉት ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ኢየጮሁ ፡ ይሰቅለውም ፡ ዘንድ ፡ ለመኑት ፡፡ ቃላቸውም ፡ በረታ ፡ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ቃል ፡፡ ጲላጦስም ፡ ዘንድ ፡ ልመናቸው ፡ ይሆንላቸው ፡ ፈረደ ፡፡ ያነንም ፡ በሁከትና ፡ በመግደል ፡ በግዞት ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረውን ፡ የለመኑትን ፡ ፈታላቸው ፡፡ የሱስን ፡ ግን ፡ ለፈቃዳቸው ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፡፡ እርሳቸውም ፡ ይዘውት ፡ ሲሔዱ ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ ያዙ ፡ ሲሞን ፡ ቁሬናዊ ፡ የሚሉት ፡ ከሜዳ ፡ ሲመጣ ፡፡ መስቀልንም ፡ ጫኑበት ፡ ከየሱስ ፡ በኋላ ፡ ይሸከመው ፡ ዘንድ ፡፡ ከሕዝቡም ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ተከተሉት ፡ ሴቶችም ፡፡ እርሳቸው ፡ ደግሞ ፡ ያለቀሱለት ፡፡ የሱስም ፡ ወደርሳቸው ፡ ተመለሰ ፡ አለም ፡፡ እላንት ፡ የየሩሳሌም ፡ ልጆች ፡ ለኔ ፡ አታልቅሱልኝ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ራሳችሁ ፡ አልቅ

ሶ ፡ ስለ ፡ ልጆቻችሁም ፡፡ እነኋት ፡ ቀን ፡ ትመጻለችና ፡ የ
ሚሉባት ፡፡ ለመካኖች ፡ ምስጋና ፡ ይገባቸዋል ፡፡ ላልወለደ
ም ፡ ሆድ ፡ ላላጠባም ፡ ጡት ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይጀምራ
ሉ ፡ ተራሮችን ፡ ይሉ ፡ ዘንድ ፡፡ በላያችን ፡ ውደቁ ፡፡ ኮረፍ
ቶችንም ፡ ድፈኑን ፡፡ በርጥብ ፡ እንጨት ፡ እንደዚህ ፡ ቢያደርጉ ፡
በደረቀውስ ፡ እንዴት ፡ ይሆናልና ፡፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ደግሞ ፡ ሌ
ሎችን ፡ ሁለት ፡ ክፉ ፡ አድራጎችን ፡ ወሰዱ ፡ ሊገልዋቸው ፡፡
የራስ ፡ አጽንትም ፡ ወደሚሉት ፡ ቦታ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ከ
ዚያ ፡ ሰቀሉት ፡ ክፉ ፡ አድራጎችንም ፡ አንዱን ፡ በቀኙ ፡ ሁ
ለተኛውንም ፡ በግራው ፡፡ የሱስ ፡ ግን ፡ አለ ፡፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡
ስረይላቸው ፡፡ የሚያደርጉትን ፡ አያውቁምና ፡፡ ልብሱን
ም ፡ ተካፈሉ ፡ ዕፃም ፡ ተጣጣሉበት ፡፡ ሕዝብም ፡ ቁመው ፡
ያዩ ፡ ነበሩ ፡፡ አለቆችም ፡ ደግሞ ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ አፌዙ
በት ፡ እንደዚህ ፡ ሲሉ ፡፡ ሌሎችን ፡ አድንዋልና ፡ ራሱንም ፡
ያድን ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጠው ፡
ቢሆን ፡፡ ወታደሮችም ፡ ደግሞ ፡ አፌዙበት ፡፡ ወደርሱም ፡
ቀርበው ፡ መጣጣ ፡ አቀረቡለት ፡ እንደዚህ ፡ ሲሉ ፡፡ አንተስ ፡
የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ሆንኽ ፡ ራስኽን ፡ አድን ፡፡ ደግ
ሞም ፡ መጻፍ ፡ በላዩ ፡ ተጻፈ ፡ በፅርዕ ፡ በሮሚም ፡ በዕብራ
ይስጥም ፡ ፊደላት ፡ የሚል ፡፡ ይኽ ፡ ነው ፡ የአይሁድ ፡ ንጉ
ሥ ፡፡ ከክፉ ፡ አድራጎችም ፡ አንዱ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ከተሰቀ
ሉት ፡ ሰደበው ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ፡፡ አንተስ ፡ ክርስቶስ ፡ እን
ደ ፡ ሆንኽ ፡ ራስኽን ፡ አድን ፡ እኛንም ፡፡ ሁለተኛው ፡ ግን ፡
መለሰ ፡ ተጻየፈውም ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ፡፡ አንተም ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ አትፈራምን ፡ አንተ ፡ እንደዚኽ ፡ ባለ ፡ ኵነኔ ፡ ሳ
ለኽ ፡፡ እኛስ ፡ በውነት ፡ ፍዳችነን ፡ ተቀበልነ ፡ ባደረግነው ፡
የሚገባነን ፡፡ ይኽ ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ የማይገባውን ፡ አልሰራ
ም ፡፡ የሱስንም ፡ አለው ፡፡ አስበኝ ፡ አቤቱ ፡ በመንግሥት
ኽ ፡ በመጣኽ ፡ ጊዜ ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡፡ በውነት ፡ እልኻ
ለሁ ፡ ዛሬ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ትሆናለህ ፡ በገነት ፡፡ ስድስተኛ ፡ ሰዓ
ትም ፡ ጊዜ ፡ ነበረ ፡፡ ጨለማም ፡ ሆነ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላ
ይ ፡ እስከ ፡ ዘጠነኛ ፡ ሰዓት ፡ ድረሰ ፡፡ ፀሐዩም ፡ ጨለመች ፡፡



የመቅደስም ፡ መጋረጃ ፡ በማኸሉ ፡ ተቀደደ ፡፡ የሱስም ፡ በ
ታላቅ ፡ ቃል ፡ ጮኸ ፡ አለም ፡፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ በጅኽ ፡ መንፈሴ
ን ፡ አደራ ፡ እሰጣለሁ ፡፡ ይህንንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ነፍሱን ፡ ሰ
ጠ ፡፡ የመቶው ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ የሆነውን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ አመሰገነ ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ፡፡ በውነት ፡ ይኽ ፡ ሰ
ው ፡ ጻድቅ ፡ ነበረ ፡፡ ይህንንም ፡ ለማየት ፡ ተከማችተው ፡
የነበሩት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የሆነውን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ተመለሱ ፡
ደረታቸውን ፡ ኢየመቱ ፡፡ የሚያውቁትም ፡ ሁሉ ፡ በሩቅ ፡
ቁመው ፡ ነበሩ ፡፡ ከገሊላም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይከተሉት ፡ የነ
በሩ ፡ ሴቶች ፡፡ ይህንንም ፡ ያዩ ፡ ነበሩ ፡፡

## የሕማማት ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

1. ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ ይህችን ፡ ጌታችን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስለርስዋ ፡ በኃጥአን ፡ እጅ ፡ አልፎ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ በመስቀል ፡ ላይም ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ የወደደ ፡ ቤትህን ፡ በምህረት ፡ ታያት ፡ ዘንድ ፡ እንለምንሃለን ፡ በርሱ ፡ አሁን ፡ በሚኖር ፡ በሚገዛም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

2. ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ሁና ፡ በመንፈስህ ፡ ትገዛታለችና ፡ ተቀድሳለችም ፡፡ በተቀደሰች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ላለ ፡ ለሰው ፡ ንብረት ፡ ሁሉ ፡ የምናደርገውን ፡ ልመናና ፡ ጸሎት ፡ ሁሉ ፡ ስማ ፡ የጉባኤህ ፡ ብልት ፡ ሁሉ ፡ ኢያንዳንዱ ፡ በየመጸራቱና ፡ በየመልአክቱ ፡ በቀና ፡ ልብና ፡ በፍርሃት ፡ ያገለግልህ ፡ ዘንድ ፡ በጌታችንና ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

3. መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ሰውን ፡ ሁሉን ፡ የፈጠርህ ፡ ከፈጠርሀውም ፡ ሁሉ ፡ አንዳችን ፡ የማትጸላ ፡

የኃጢአተኛውንም ፡ ሞት ፡ የማትሻ ፡ ሊመለስ ፡ እንጂ ፡ ሊድንም ፡፡ አይሁድን ፡ ሁሉ ፡ እሥላሞችንም ፡ አረማውያንንም ፡ ካጀችንም ፡ መናፈቃንንም ፡ ሁሉ ፡ ማሬቸው ፡፡ አለማወቁንም ፡ ሁሉ ፡ የልብንም ፡ ድንዛዜ ፡ የቃልህንም ፡ መናቅ ፡ ውሰድባቸው ፡፡ እንዲህም ፡ ቡሩክ ፡ ጌታችን ፡ ሆይ ፡ ወደ ፡ መንጋህ ፡ ሰብስባቸው ፡ እርሳቸው ፡ ካደኖተኞች ፡ እሥራኤላውያን ፡ ጋራ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡ አንዲት ፡ መንጋም ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ካንድ ፡ ከውነተኛ ፡ ጠባቂ ፡ በታች ፡ እርሱም ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጌታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ኑሮ ፡ የሚገዛ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ዕብራውያን ፡ ፲፡ ፩፡—፳፫፡፡

ኦሪትም ፡ የሚመጣው ፡ የበጎ ፡ ነገር ፡ ጽላል ፡ አላት ፡፡ የነገሩ ፡ አይነተኛ ፡ ሥእል ፡ ግን ፡ አይደላትም ፡፡ ስለዚህም ፡ ባመት ፡ ባመት ፡ ደግመው ፡ በሚያቀርብዋቸው ፡ በማይጨርሱም ፡ ምሥዋዕቶች ፡ እሊያን ፡ የሚገቡባትን ፡ ትፈጽም ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ አይቻላትም ፡፡ ተፈጽመውስ ፡ ቢሆኑ ፡ ከማቅረብን ፡ ባያርፏ ፡ የሚያቀርብዋቸው ፡ ሕሊናቸው ፡ ከኃጢአት ፡ ስለ ፡ ነጻች ፡ እርሳቸው ፡ አንደግዜ ፡ ከነጹ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ በልያ ፡ መሥዋዕቶች ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ያስባሉ ፡ ባመት ፡ ባመት ፡፡ የበሬና ፡ የፍየል ፡ ደም ፡ ኃጢአትን ፡ ይደመስስ ፡ ዘንድ ፡ ተስንዋልና ፡፡ ስለዚኽም ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ሲገባ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡፡ ቍርባንን ፡ መሥዋዕትንም ፡ አልሻኽም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሥጋዬን ፡ አዘጋጀኽልኝ ፡፡ የምትቃጠለውን ፡ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ የምትቀርበውን ፡ መሥዋዕት ፡ አልወደድኽም ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አልሁ ፡፡ እነሆኝ ፡ እኔ ፡ እመጣለሁ ፡ (በመጽሐፍ ፡ ራስ ፡ ስለኔ ፡ ተጽፎዋል ፡) ፈቃድኽን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አቤቱ ፡፡ ከዚኽም ፡ በላይ ፡ ሲል ፡፡ መሥዋዕትን ፡ ቍርባንንም ፡ የምትቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ የምትቀርበውን ፡ አልወደድኽም ፡፡ (እሌህ ፡ በኦሪት ፡ ሥርዓት ፡ ይቀረባሉ ፡) የዚ



ያን ፡ ጊዜም ፡ አለ ፡፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ እመጣለሁ ፡ ፈቃድኽን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አቤቱ ፡፡ የፊተኛውን ፡ ነቀለ ፡ የኋለኛውን ፡ ሊያቀም ፡፡ በዚችም ፡ ፈቃድ ፡ እኛ ፡ የተቀደስነ ፡ ነነ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በሥጋው ፡ ቍርባን ፡ አንደግዜ ፡፡ ካህንም ፡ ሁሉ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ አገልጋይ ፡ ሁኖ ፡ ይቆማል ፡ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ እልያን ፡ መሥዋዕቶች ፡ ደግሞ ፡ ያቀርባል ፡ ኃጢአት ፡ ያስወግዱ ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ የማይቻላቸውን ፡፡ ይኽ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ አንዲትን ፡ መሥዋዕት ፡ ባቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ለዘላለም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ተቀመጠ ፡፡ ከዚያም ፡ ይጠብቃል ፡ ጸላቶቹ ፡ ከግሩ ፡ ጫማ ፡ በታች ፡ እስኪጣሉ ፡ ድረስ ፡፡ ባንዲት ፡ ቍርባን ፡ የሚቀደሱትን ፡ ለዘላለም ፡ ፈጽምዋልና ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ደግሞ ፡ መሰከረልነ ፡፡ አስቀድሞ ፡ ብልዋልና ፡፡ ይኽች ፡ ሥርዓቴ ፡ ናት ፡ የምሠራላቸው ፡ ከዚያች ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡፡ ሕገጋቴን ፡ በልባቸው ፡ አኖራለሁ ፡ በሕሊናቸውም ፡ እጽፈቸዋለሁ ፡፡ ደግሞም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ በደላቸውንም ፡ ደግሜ ፡ አላስብም ፡፡ የርሳቸውም ፡ ስርየት ፡ ሳለች ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ቍርባን ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ አያሻም ፡፡ አሁንም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ለኛ ፡ ድፍረት ፡ ሳለነ ፡ የመቅደስን ፡ መንገድ ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ደም ፡፡ ባደሰልነ ፡ አዲስና ፡ ሕያው ፡ መንገድ ፡ ሆኖ ፡፡ በመጋረጃ ፡ ማለቱ ፡ በሥጋው ፡፡ ታላቅ ፡ ካህንም ፡ ሳለነ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ላይ ፡፡ እንቅረብ ፡ በውነተኛ ፡ ልብ ፡ በፍጹምም ፡ ሃይማኖት ፡፡ ልባችንም ፡ ከክፏ ፡ ሕሊና ፡ ተረጭተን ፡፡ ሥጋችነንም ፡ በጽሩ ፡ ውኃ ፡ ታፅበን ፡፡ ተስፋችነንም ፡ በመግለጽ ፡ እንጽና ፡ ሳንዘነብል ፡፡ ተስፋ ፡ የሰጠነ ፡ እርሱ ፡ የታመነ ፡ ነውና ፡፡ እርሱ ፡ በርሳችንም ፡ እንጠባበቅ ፡ ለፍቅር ፡ ለመልካምም ፡ ነገር ፡ እናስቀና ፡ ዘንድ ፡፡ መከማቻችነንም ፡ አንተው ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡ ልማድ ፡ እንደደረጉ ፡፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ተጸናኑ ፡ እንጅ ፡፡ ይህነን ፡ በሚያሀል ፡ ጨምራችሁ ፡ ያቀን ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ አይታችሁ ፡፡

## የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፲፱፡ ፩፡—፴፯፡፡

የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጲላጦስ ፡ የሱስን ፡ ወሰደው ፡ ገረፈውም ፡፡
ጭፍሮችም ፡ የሾኽ ፡ አክሊል ፡ ጕንጕኑ ፡ በራሱ ፡ ላይም ፡
አኖሩት ፡፡ ቀይ ፡ ልብስም ፡ አለበሱት ፡፡ አሉትም ፡፡ እ
ንዴት ፡ ነኽ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡፡ በጥፊም ፡ መቱት ፡፡ ጲ
ላጦስም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጣ ፡ አላቸውም ፡፡ እነሆ ፡
ይህነን ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ አወጣላችኋለሁ ፡፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡
የፍርድ ፡ መክንያት ፡ አንዲት ፡ስንኳ ፡ እንደላገኘሁበት ፡፡
የሱስም ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጣ ፡ የሾኽ ፡ አክሊል ፡ ቀይ ፡ ልብ
ስም ፡ ለብሶ ፡፡ አላቸውም ፡፡ እነሆ ፡ ሰው ፡፡ የካህናት ፡ አ
ለቆችም ፡ ሎሌልትም ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲ
ሉ ፡፡ ስቀለው ፡፡ ስቀለው ፡፡ ጲላጦስም ፡ አላቸው ፡፡ እላን
ት ፡ ወስዳችሁ ፡ ስቀሉት ፡፡ እኔ ፡ መክንያትን ፡ አላገኘሁበ
ትምና ፡፡ አይሁድም ፡ መለሱለት ፡ አሉትም ፡፡ ሕግ ፡ አለን ፡፡
በሕጋችንም ፡ ሞት ፡ ይገባዋል ፡፡ ራሱን ፡ የእግዚአብሔር
ን ፡ ልጅ ፡ አድርጓልና ፡፡ ጲላጦስም ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡
ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ፈራ ፡፡ ደግሞም ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ገባ ፡ የ
ሱስንም ፡ አለው ፡፡ አንተ ፡ ከወዴት ፡ ነኽ ፡፡ የሱስ ፡ ግን ፡
ምላሽ ፡ አልሰጠውም ፡፡ ጲላጦስም ፡ አለው ፡፡ አትነግረ
ኝምን ፡፡ አታውቅምን ፡ ሥልጣን ፡ እንደለኝ ፡ እሰቅልኽ ፡
ዘንድ ፡ እፈታኽም ፡ ዘንድ ፡፡ መለሰ ፡ የሱስ ፡ አለም ፡፡ በ
ኔ ፡ ሥልጣን ፡ ባትኖርልህ ፡ ከሰማይ ፡ ካልተሰጠችኽ ፡፡ ስለ
ዚኽም ፡ ላንተ ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠኝ ፡ ኀጢአቱ ፡ ይበልጣል ፡፡
ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ጲላጦስ ፡ ይፈታው ፡ ዘንድ ፡ ፈለገ ፡፡ አ
ይሁድ ፡ ግን ፡ ጮሁ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ይህነንስ ፡ ብትፈታ ፡
የቄሳር ፡ ወዳጅ ፡ አይደለኽም ፡፡ ራሱን ፡ ንጉሥ ፡ የሚያደ
ርግ ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ የቄሳር ፡ ጸላት ፡ ነውና ፡፡ ጲላጦስም ፡ ይ
ህነን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ የሱስን ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ አወጣ
ው ፡፡ በወንበርም ፡ ተቀመጠ ፡ ሊቶስጥሮስ ፡ በዕብራይስጥ
ም ፡ ገበታ ፡ በሚሉት ፡ ስፍራ ፡፡ የፋሲካ ፡ ዓርብም ፡ ነበረ ፡
ጊዜውም ፡ ስድስተኛ ፡ ሰዓት ፡ ነበር ፡፡ አይሁድንም ፡ አላቸ
ው ፡፡ እነሆ ፡ ንጉሣችሁ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ጮሁ ፡ እንዲ



ህ ፡ ሲሉ ፡፡ አስወግደው ፡፡ አስወግደው ፡፡ ስቀለው ፡፡ ጲላጦ
ስም ፡ አላቸው ፡፡ ንጉሣችሁንን ፡ ልስቀል ፡፡ የካህናት ፡ አለ
ቆችም ፡ መለሱ ፡ አሉትም ፡፡ ንጉሥ ፡ የለነም ፡ ከቄሳር ፡ በ
ቀር ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፡ ሊሰቀል ፡፡ የ
ሱስንም ፡ ተቀበሉት ፡ ይዘውትም ፡ ሔዱ ፡፡ መስቀሉንም ፡
ተሸክሞ ፡ ወጣ ፡ የራስ ፡ አጽንት ፡ ወደሚሉት ፡ ስፍራ ፡ በ
ዕብራይስጥ ፡ ጎልጎታ ፡ የሚባል ። ሰቀሉትም ፡ ወደ ፡ ነበ
ረበት ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሌሎችን ፡ ሁለት ፡ በዚኽና ፡ በዚያ ፡
ሰቀሉ ፡፡ የሱስንም ፡ በመኻከላቸው ። ጲላጦስም ፡ ጽፈት
ን ፡ ጻፈ ፡ በመስቀሉም ፡ አኖራት ፡፡ ተጽፎም ፡ ነበረ ፡ እንዲ
ህ ፡ ሲል ፡፡ የሱስ ፡ የናዝሬቱ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡፡ ይህነን
ም ፡ ጽፈት ፡ ከአይሁድ ፡ ብዙ ፡ አነበቡት ፡፡ የሱስ ፡ የተሰ
ቀለበት ፡ ስፍራ ፡ ላገር ፡ ቅርብ ፡ ነበረና ፡፡ ተጽፎም ፡ ነበረ ፡ በ
ዕብራይስጥ ፡ በፅርዕም ፡ በሮምም ፡ ልሳን ፡፡ የአይሁድም ፡
ካህናት ፡ አለቆች ፡ ጲላጦስን ፡ አሉት ፡፡ የአይሁድ ፡ ንጉ
ሥ ፡ ብለህ ፡ አትጻፍ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ እኔ ፡ የአይሁድ ፡
ንጉሥ ፡ ነኝ ፡ እንደለ ፡፡ መለሰ ፡ ጲላጦስ ፡ አለም ፡፡ የጻፍ
ሁትን ፡ ጻፍሁ ፡፡ ወታደሮች ፡ ግን ፡ የሱስን ፡ በሰቀሉት ፡ ጊ
ዜ ፡ ልብሶቹን ፡ ወሰዱ ፡፡ ላራት ፡ ክፍልም ፡ አደረጉት ፡ ከ
ጭፍሮች ፡ ለያንዳንዱ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡፡ ቀሚሱንም ፡፡ ቀ
ሚሱም ፡ ያልተሰፋ ፡ ነበረ ፡፡ ሁለንትናው ፡ የተሰራ ፡ ነበር ፡
እንጅ ፡ ከላይ ፡ ጀምሮ ፡፡ እርሱ ፡ በርሳቸውም ፡ አሉ ፡፡ አን
ቀደደው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ዕፃ ፡ እንጣጣልበት ፡ ስለርሱ ፡ ለማ
ን ፡ እንዲደርስ ፡፡ መጽሐፍ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡፡ ል
ብሶቼን ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ተካፈሉ ፡ በቀሚሴም ፡ ላይ ፡
ዕፃውን ፡ ተጣጣሉ ። ወታደሮችም ፡ እንዲህ ፡ አደረጉ ፡፡ ከየ
ሱስ ፡ መስቀል ፡ አጠገብም ፡ ቆሙ ፡ እናቱ ፡ የናቱም ፡ እኅት ፡
ማርያም ፡ የቀለዮጳ ፡ ምሽት ፡ ማርያምም ፡ መግደላዊቱ ፡፡
የሱስም ፡ እናቱን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ የወደደውንም ፡ ደ
ቀ ፡ መዝሙሩን ፡ ከዚያ ፡ ቆሞ ፡፡ እናቱን ፡ አላት ፡፡ አንቺ ፡
ሴት ፡ እነሆት ፡ ልጅሽ ፡፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ደቀ ፡ መዝ
ሙሩን ፡ እነኋት ፡ እናትኽ ፡ አለው ፡፡ ከዚያችም ፡ ሰዓ

112



ት : ጀምሮ : ደቀ : መዝሙሩ : ወደ : ቤቱ : ወሰደት :: ከዚኽም : በኋላ : የሱስ : በመጻፉ : ያለው : ይፈጸም : ዘንድ : የነበረ : ሁሉ : እንደ : ተፈጸመ : ባወቀ : ጊዜ :: አለ :: እኔ : ተጸማሁ :: ከዚያም : እቃ : ተቀምጦ : ነበረ : መጣጣ : የመላበት :: እርሳቸውም : መጣጣውን : በሰፍነግ : መሉ :: ሁሮጽም : በሚባል : አኖሩት : ወደፉም : አቀረቡት :: የሱስም : መጣጣውን : በቀመሰ : ጊዜ : አለ :: ተፈጸመ :: ራሱንም : አዘነበለ : መንፈሱንም : ሰጠ :: አይሁድ : ግን : ሥጋቸው : በመስቀል : ላይ : በሰንበት : እንዲያድር :: (ዓርብ : ነበረና :: የዚያም : ሰንበት : ቀን : ታላቅ : ነበረና ::) ጲላጦስን : ጭናቸውን : ይሰብሩ : ዘንድ : ያወርድዋቸውም : ዘንድ : ለመኑት :: ወታደሮችም : መጡ : የፊተኛውንም : ጭን : ሰበሩ : የሌላውንም : ከርሱ : ጋራ : የተሰቀለውን :: ወደ : የሱስ : ግን : መጥተው : እርሱ : እንደ : ሞተ : ባዩ : ጊዜ : ጭኑን : አልሰበሩም :: ነገር : ግን : አንድ : ከወታደሮች : ጐኑን : በጦር : ወጋው :: የዚያን : ጊዜም : ወጣ : ደምና : ውኃ :: ያየውም : መሰከረ :: ምስክሩም : እውነት : ናት :: እርሱም : እውነት : እንደ : ተናገረ : ያውቃል : እላንት : ታምኑ : ዘንድ :: ይኽም : ሆነ : መጻፉ : ይፈጸም : ዘንድ : እንዲህ : ሲል : አፅንቱን : ከርሱ : አይሰብሩም :: ደግሞም : ሌላ : መጻፉ : ይላል :: የወጉትን : ያያሉ ::

ፈሲካውን : የሚቀድም : ቅዳሜ ::

ጸሎት ::

አቤቱ : ጸጋህን : ስጠነ : እኛ : በተባረከ : ልጅህ : በመድኃኒታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ሞት : እንደ : ተጠመቅነ : እንደሁም : እኛ : የከፋውን : መሻታችን : ወትሮ : ገድለን : ከርሱ : ጋራ : እንቀበር : ዘንድ : በመቃበርም : በሞት : ደጅ : አልፈን : ወደ : ደስታ : ትንሣኤያችን : እንደርስ : ዘንድ : ለኛ : ስለ : ሞተ : ስለ : ተቀበረም : ደግሞም : ስለ : ተነሣ : ስለ : ልጅህ : ስለ : የሱስ : ክርስቶስ : ስለ : ጌታችን : ምግባር :: አሜን ::



የመልእክት : ክፍል :: ፩ ጴጥሮስ : ፫ ፲፯—፳፪

መልካም : ስታደርጉ : መከራ : ትቀበሉ : ዘንድ : እግዚአብሔር : ቢወደው :: ክፉ : ስታደርጉ : መከራን : ከመቀበል : ይሻላልና :: ክርስቶስ : ደግሞ : አንደግዜ : ስለ : ኃጢአት : አሞታልና :: ጻድቁ : ስለ : ዓመፀኞች :: እኛን : ወደ : እግዚአብሔር : ያቀርበን : ዘንድ :: በሥጋም : ሞተ : በመንፈስ : ግን : ሕያው : ሆነ :: በርሱም : በግዞት : ወዳሉ : ነፍሶች : ሒደ : ሰበከላቸው :: ቀድሞ : እምቢ : ብለው : ለነበሩ : የእግዚአብሔር : ምሕረት : ረጅም : ዘመን : በዛገየች : ጊዜ :: በኖህ : ዘመን : እርሱ : መርከብን : ሲሰራ :: ጥቂቶች : እርሳቸውም : ስምንት : ሰዎች : በውኃ : አልፈው : የደኑባት :: ለርሱም : ዛሬ : ምሳሌ : ያለች : እርስዋም : ጥምቀት : ታድነናለች :: (ከሥጋ : እድፉን : ማፅብ : አይደለም : የበጎ : ሕሊና : ልመና : ወደ : እግዚአብሔር : እንጅ) :: በየሱስ : ክርስቶስ : ትንሣኤ :: እርሱ : በእግዚአብሔር : ቀኝ : ያለ :: ወደ : ሰማይ : ወጥቶ :: መላእክትም : አለቆችም : መኳንንትም : ያዘዙለታል ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፳፯ ፶፯—፳፯

በመሸም : ጊዜ : አንድ : ባለ : ጠጋ : ሰው : ከአርማትያስ : ስሙን : ዮሴፍ : የሚሉት : መጣ :: እርሱም : ደግሞ : ከየሱስ : ደቀ : መዛሙርት : ነበረ :: ይኽም : ወደ : ጲላጦስ : ሔደ : የየሱስንም : ሥጋ : ለመነው :: የዚያን : ጊዜም : ጲላጦስ : ሥጋውን : ይሰጡት : ዘንድ : አዘዘ :: ዮሴፍም : ሥጋውን : ወሰደ : በነጭም : በተልባግር : ስራ : ከፈነው :: ባደስ : መቃብሩም : አገባው : ለርሱ : በደንጊያ : ያስወቀረው : በነበረ :: ታላቅ : ደንጊያም : በመቃብሩ : አፍ : ገጠመና : ሔደ :: ከዚያም : ነበሩ : ማርያም : መግደላዊት : ሁለተኛዋም : ማርያም : በመቃብሩ : ፊት : ተቀምጠው :: በነገውም : ካርብ : በኋላ : በሆነው : የካህናት : አለቆች : ፈሪሳውያንም : ወደ : ጲላጦስ : ተሰበሰቡ : እንደህ : ሲሉ :: ጌታ : ሆይ : ያ : አሳች : ሕያው : ሳለ :: ከሮ

ስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ እነሣለሁ ፡ እንደለ ፡ አሰብነ ። ስለዚኽ ም ፡ እዘዝ ፡ መቃብሩ ፡ እስከ ፡ ሦስተኛ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ እን ዲጠበቅ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ በሌት ፡ መጥተው ፡ እንደይ ሰርቁት ። ለሕዝብም ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ እንደ ይሉ ። የኋለኛዪቱም ፡ ጥፋት ፡ ከፊተኛዪቱ ፡ እንደትከፋ ። ጲላጦስም ፡ አላቸው ፡ ጠባቆች ፡ አልዋችሁ ። ሒዷችሁ ፡ መቃብሩን ፡ ደህና ፡ አድርጋችሁ ፡ ጠብቁት ፡ እንደምታ ውቁ ። እርሳቸውም ፡ ሔደ ፡ መቃብሩንም ፡ አስታመኑ ። ደንጊያውንም ፡ አተሙ ፡ ከጠባቆች ፡ ጋራ ።

## የፋሲካ ፡ በዓል ።

በጵዋት ፡ ጸሎት ፡ ጊዜ ፡ በ፺፭፡ መዝሙር ፡ ፈንታ ፡ ከዚህ ፡ የሚከተል ፡ የመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ነገር ፡ ይደገም ፡ ወይስ ፡ ይዘመር ።

1. ክርስቶስ ፡ ፋሲካችን ፡ ስለኛ ፡ ታርድዋልና ፡ በዓልን ፡ እናድርግ ።

ባሮጌ ፡ እርሾ ፡ አይደለም ፡ በክፋትም ፡ በኃጢአትም ፡ እርሾ ፡ አይደለም ፡ በየውሃትና ፡ በውነት ፡ ቂጻ ፡ እንጀ ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፭፡ ፯፡ ፰።

2. ከሙታን ፡ የተነሣ ፡ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ አይሞትም ። ሞትም ፡ ደግሞ ፡ አይገዛበትም ።

በሞቱ ፡ ለኃጢአት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሙትዋልና ፡ በሕይ ወቱ ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ።

እንዲሁም ፡ እላንተ ፡ ራሳችሁን ፡ ከኃጢአት ፡ እንደ ፡ ሞታችሁ ፡ ቍጠሩ ፡ ሕያዋንም ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ ለእግዚ አብሔር ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ በጌታችን ። ሮሜ ፡ ፮፡ ፱—፲፩።

3. ክርስቶስ ፡ ከሙታን ፡ ተነሣ ፡ የንቀላፉትም ፡ መጀመ ርያ ፡ ፍሬ ፡ ሆነ ። ሞት ፡ በሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዲሁም ፡ በሰው ፡ የሙታን ፡ ትንሣኤ ፡ ሆነ ። ሁላቸውም ፡ በአደም ፡



እንደ ፡ ሞቱ ፡ እንዲሁም ፡ ሁላቸው ፡ በክርስቶስ ፡ ሕያዋን ፡ ይሆናሉ ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፲፭፡ ፳—፳፪።

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብና ፡ ለወልድ ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱ ስም ።

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ፡ ለዘ ወትርም ፡ እንደለው ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

## ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምለክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ ባንድ ፡ ልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሞትን ፡ አሸንፈህ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ ደጅ ፡ ከፍተህልናልና ። እኛ ፡ በትሕትና ፡ እንለ ምንሃለን ፡ የተለየች ፡ ጸጋህ ፡ ቀድማን ፡ አንተ ፡ በጎ ፡ ፈቃ ድን ፡ በልባችን ፡ እንድትሰጥ ፡ እንዲሁም ፡ አንተ ፡ ወትሮ ፡ ረድተህን ፡ እኛ ፡ በጎ ፡ ፈቃዳችነን ፡ እንፈጽም ፡ ዘንድ ፡ በየ ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ኑሮ ፡ የሚገዛ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

## የመልእክት ፡ ክፍል ። ቆሎሳይስ ፡ ፫፡ ፩—፯።

እንጊዲህ ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋራ ፡ የተነሣችሁ ፡ እንደ ፡ ሆቻች ሁ ፡ በላይ ፡ ያለውን ፡ እሹ ፡ ክርስቶስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደለበት ። በላይ ፡ ያለውን ፡ አስቡ ፡ በ ምድርም ፡ ያለውን ፡ አይደለም ። እላንተ ፡ ሙታችኋልና ፡ ሕይወታችሁም ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተሠ ውራለች ። ሕይወታችንም ፡ ክርስቶስ ፡ ሲገለጥ ፡ ጊዜ ፡ የዚ ያን ፡ ጊዜ ፡ እላንትም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ በክብር ፡ ትገለጣላች ሁ ። አሁንም ፡ በምድር ፡ ያሉትን ፡ ብልቶቻችሁን ፡ ግደሉ ። ዝሙት ። ርኵሰትም ። ሕማማትም ። ክፉ ፡ ፍትወትም ። የከብት ፡ መውደድም ፡ እርሱም ፡ ጣዖትን ፡ ማምለክ ፡ ነ ው ። ይህች ፡ ስለርስዋ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ የሚመ ጣ ፡ በእምቢተኝነት ፡ ልጆች ፡ ላይ ። እላንትም ፡ ደግሞ ፡ ቀ ድሞ ፡ ትመላለሱባት ፡ የነበራችሁ ፡ ሕይወታችሁ ፡ በርስዋ ፡ ስትሆንላችሁ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፳ ፩—፲።

ከሰንበትም ፡ በመጀመርያው ፡ ቀን ፡ ማርያም ፡ መግደላ
ዊት ፡ ማልደ ፡ ገና ፡ ጨለማ ፡ ሳለ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ መጣ
ች ። ድንጊያውንም ፡ ከመቃብር ፡ ተፈንቅሎ ፡ አየች ። ሮጠ
ችም ፡ ወደ ፡ ሲሞን ፡ ጴጥሮስም ፡ መጣች ፡ ወደ ፡ ሁለተኛው
ም ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ የሱስ ፡ ወደ ፡ ወደደው ። አለቻቸው
ም ፡ ጌታን ፡ ከመቃብር ፡ አነሡት ፡ ወዴትመ ፡ እንደ ፡ አኖሩ
ት ፡ አላውቅም ። ጴጥሮስም ፡ ወጣ ፡ ሁለተኛውም ፡ ደቀ ፡
መዝሙር ፡ ወደ ፡ መቃብርም ፡ መጡ ። እርሳቸውም ፡ ሁለ
ቱ ፡ ባንድ ፡ ይሮጡ ፡ ነበሩ ። ሁለተኛውም ፡ ደቀ ፡ መዝሙ
ር ፡ ጴጥሮስን ፡ ቀደመ ፡ አስቀድሞም ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ መ
ጣ ። ዝቅም ፡ ብሎ ፡ ከፈኑን ፡ ተቀምጦ ፡ አየ ። ነገር ፡ ግን ፡
አልገባም ። ሲሞን ፡ ጴጥሮስም ፡ ሲከተለው ፡ መጣ ፡ ወደ ፡
መቃብርም ፡ ገባ ። ከፈኑንም ፡ ትቀምጦ ፡ አየ ። በራሱ ፡ ላ
ይም ፡ የነበረ ፡ መሐረምያ ፡ ከከፈኑ ፡ ጋራ ፡ አልነበረም ። ነ
ገር ፡ ግን ፡ ለብቻው ፡ ተጠቅልሎ ፡ ነበረ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡
ሁለተኛው ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ አስቀድሞ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡
መጥቶ ፡ የነበረ ፡ ደግሞ ፡ ገባ ፡ አየም ፡ አመነም ። በመጻፉ ፡
ያለውን ፡ ገና ፡ አላወቁምና ፡ ከሙታን ፡ ይነሣ ፡ ዘንድ ፡ እን
ዳለው ። ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ስፍራቸ
ው ፡ ሔዱ ።

## የፋሲካ ፡ ሰኞ ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ ባንድ ፡
ልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሞትን ፡ አሸንፈህ ፡ የዘላለም ፡
ሕይወትን ፡ ደጅ ፡ ከፍተህልናልና ። እኛ ፡ በትሕትና ፡ እንለ
ምንሃለን ፡ የተለዩኝ ፡ ጸጋህ ፡ ቀድማን ፡ አንተ ፡ በጎ ፡ ፈቃ
ድን ፡ በልባችን ፡ እንድትሰጥ ፡ እንዲሁም ፡ አንተ ፡ ወትሮ ፡
ረድተህን ፡ እኛ ፡ በጎ ፡ ፈቃዳችንን ፡ እንፈጽም ፡ ዘንድ ፡ በየ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡



ጋራ ፡ ኑሮ ፡ የሚገዛ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ።
አሜን ።

### በመልእክት ፡ ፈንታ ። የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፲ ፴፬—፵፫።

ጴጥሮስም ፡ አፉን ፡ ከፈተ ፡ አለም ። በውነት ፡ አስተው
ላለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ እንደያደላ ። ነገር ፡
ግን ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የሚፈራው ፡ ቀን ፡ ነገርም ፡ የሚያደር
ግ ፡ እርሱ ፡ በርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ነው ። ወደ ፡ እሥራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ የላከውን ፡ ነገር ፡ የምስራች ፡ ይነግራቸው ፡
ዘንድ ፡ በዕርቅ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። እርሱ ፡ የሁሉ ፡ ጌ
ታ ፡ ነው ። ይኸነን ፡ ነገር ፡ እላንት ፡ ታውቃላችሁ ፡ በይሁዳ ፡
ሁሉ ፡ የሆነውን ፡ ከገሊላ ፡ ጀምሮ ፡ ዮሐንስ ፡ ከሰበከበት ፡
ጥመቀት ፡ በኋላ ። ስለ ፡ የሱስ ፡ ስለ ፡ ናዝሬቱ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስና ፡ በኃይል ፡ እንደ ፡ ቀባው ። ዙሮ ፡
መልካምን ፡ ያደረገ ፡ ሰይጣን ፡ ያሸነፋቸውንም ፡ ሁሉ ፡ የ
ፈወሰ ። እግዚአብሔር ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበረና ። እኛም ፡ ም
ስክሮች ፡ ነን ፡ ባደረገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ አገር ፡ በየሩ
ሳሌምም ። ይህነን ፡ በንጨት ፡ ላይ ፡ ሰቅለው ፡ ገደሉት ።
ይኸነንም ፡ እግዚአብሔር ፡ አስነሣው ፡ በሶስተኛ ፡ ቀን ። ሰ
ጠውም ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ። ለሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አይደለም ።
ለኛ ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔር ፡ አስቀድሞ ፡ ምስክሮች ፡ እ
ንሆን ፡ ዘንድ ፡ ለመረጠን ። ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የበላን ፡ የጠ
ጣነም ፡ ከሙታን ፡ ከተነሣ ፡ በኋላ ። ለሕዝብም ፡ እንሰብ
ክ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘን ፡ እንመሰክርም ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ እን
ደ ፡ ሆነ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተሠራ ፡ የሕያዋንና ፡ የሙታ
ን ፡ ፈራጅ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ለርሱም ፡ ነቢያት ፡ ሁሉ ፡ ይ
መሰክራሉ ፡ በርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ የኃጢአቱን ፡ ስር
የት ፡ እንዲወስድ ፡ በስሙ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፳፬ ፲፫—፴፭።

እነሆም ፡ ሁለት ፡ ከርሳቸው ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ወደገር ፡ ይ
ሔዱ ፡ ነበሩ ፡ ከየሩሳሌም ፡ ስድሳ ፡ ምዕራፍ ፡ የራቀች ።
ስምዋንም ፡ ኤማኁስ ፡ የሚልዋት ። እርሳቸውም ፡ ይጫወ

ቱ ፡ ነበረ ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ስለዚኽ ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡፡ ሆነም ፡ እርሳቸው ፡ ሲጫወቱ ፡ ሲጠያየቁም ፡ የሱስ ፡ ራሱን ፡ ወደርሳቸው ፡ ቀረበ ፡ ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ ሔደ ፡፡ ዓይናቸው ፡ ግን ፡ ተያዘች ፡ እንዳያውቁት ፡፡ አላቸውም ፡፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ይኽ ፡ ነገር ፡ እላንት ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ የምትናገገሩበት ፡ ስትመላለሱ ፡ ኢያዘናችሁ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አንዲ ፡ ስሙን ፡ ቀላዮጳ ፡ የሚሉት ፡ መለሰ ፡ አለውም ፡፡ አንተን ፡ ብቻኽን ፡ እንግዲ ፡ ነኽ ፡ በየሩሳሌም ፡ አታውቅምም ፡ በዚኽ ፡ ወራት ፡ የሆነባትን ፡፡ አላቸውም ፡፡ ምንድር ፡፡ እርሳቸውመ ፡ አሉት ፡፡ የየሱስ ፡ የናዝሬቱ ፡ ነገር ፡፡ ነቢይ ፡ ሰው ፡ የነበረ ፡ ብርቱ ፡ በማድረግም ፡ በቃልም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡፡ እንዴትስ ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ገዦቻችን ፡ ለሞት ፡ ፍርድ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጡት ፡ ሰቀሉትም ፡፡ እኛ ፡ ግን ፡ ተስፋ ፡ እናደርግ ፡ ነበርኒ ፡ እሥራኤልን ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ የሚመጣ ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከዚኽ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ለርሱ ፡ ዛሬ ፡ ሶስት ፡ ቀኑ ፡ ነው ፡ ይኽ ፡ ከሆነ ፡ ወዲህ ፡፡ ደግሞም ፡ አያሌ ፡ ሴቶች ፡ ከኛ ፡ አስደነቁነ ፡፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ማልደው ፡ ነበሩና ፡ ሥጋውንም ፡ ባላገኙት ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡ መጡ ፡ የመላእክትን ፡ ራእይ ፡ አየነ ፡ እርሱ ፡ ሕያው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚሉነ ፡፡ አያሌም ፡ ከባልንጀሮቻችን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ሔዱ ፡ ሴቶችም ፡ እንደ ፡ ተናገሩ ፡ እንዲሁም ፡ አገኙ ፡፡ እርሱን ፡ ግን ፡ አላዩትም ፡፡ እርሱም ፡ አላቸው ፡፡ እላንት ፡ ደናቍርት ፡ ልባችሁም ፡ የደነደነ ፡ ነቢያት ፡ በተናገሩበት ፡ ሁሉ ፡ እንዲታምኑ ፡፡ ለክርስቶስ ፡ ይገባው ፡ የለምን ፡ ይኽነን ፡ መከራ ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ክብሩም ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡፡ ከሙሴም ፡ ጀመረ ፡ ከነቢያትም ፡ ሁሉ ፡ አስተረጐመላቸውም ፡ በመጽሐፉ ፡ ሁሉ ፡ ስለርሱ ፡ የተጻፈውን ፡ ነገር ፡፡ ይሔዱባትም ፡ ወደ ፡ ነበሩባት ፡ አገር ፡ ደረሱ ፡፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ መራቅ ፡ ይሔድ ፡ ዘንድ ፡ አለ ፡፡ የግድም ፡ አሉት ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ እደር ፡፡ መሽቶዋልና ፡ ቀኑም ፡ ዘነበለ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ ለማደር ፡ ገባ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ በተ



ቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ እንጀራውን ፡ ወሰደ ፡ ባረከም ፡ ቈረሰም ፡ ሰጣቸውም ፡፡ ዓይናቸውም ፡ ተከፈተች ፡ አወቁትም ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ከማየታቸው ፡ ጠፋ ፡፡ አንዲም ፡ ባልንጀራውን ፡ አለው ፡፡ ልባችን ፡ ይቃጠልብን ፡ አልነበረምን ፡ በመንገድ ፡ በተናገረን ፡ ጊዜ ፡ መጽሐፍንም ፡ በፈታልን ፡ ጊዜ ፡፡ በዚያችም ፡ ጊዜ ፡ ተነሡ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌምም ፡ ተመለሱ ፡፡ አሥራ ፡ አንዱንም ፡ ተከማችተው ፡ አገኙ ፡ ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ የነበሩትን ፡፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ጌታ ፡ በውነት ፡ ተነሣ ፡ ለሲሞንም ፡ ታየ ፡፡ እርሳቸውም ፡ በመንገድ ፡ የሆነውን ፡ ነገሩ ፡፡ እርሱም ፡ እንጀራውን ፡ በመቊረስ ፡ እንደ ፡ ታወቀላቸው ፡፡

---

የፋሲካ ፡ መክሰኞ ፡፡

ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምለክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ ባንድ ፡ ልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሞትን ፡ አሸንፈህ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ ደጅ ፡ ከፍተህልናልና ፡፡ እኛ ፡ በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ የተለየች ፡ ጸጋህ ፡ ቀድማን ፡ አንተ ፡ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ በልባችን ፡ እንድትሰጥ ፡ እንዲሁም ፡ አንተ ፡ ወትሮ ፡ ረድተህን ፡ እኛ ፡ በጎ ፡ ፈቃዳችንን ፡ እንፈጽም ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ኑሮ ፡ የሚገዛ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፲፫፤ ፳፮፤—፴፩፤

እላንት ፡ ሰዎች ፡ ወንድማማች ፡፡ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ልጆች ፡ በመኻከላችሁም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሁሉ ፡፡ ለላንት ፡ ተላከ ፡ የዚህች ፡ መድኃኒት ፡ ነገር ፡፡ በየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ አለቆቻቸውም ፡ ይህነን ፡ ባያውቁ ፡ የነቢያትን ፡ ድምፅ ፡ ቅዳሜ ፡ ቅዳሜ ፡ የሚነበበውን ፡ በፈረዱበት ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመውታልና ፡፡ አንዲት ፡ ምክንያትንም ፡ እንኳ ፡ ለሞት ፡ የምታደርሰውን ፡ ሳያገኙበት ፡ ጲላጦስን ፡ ይገድለው ፡ ዘንድ ፡ ለመኑት ፡፡ ስለርሱም ፡ የተጻ

ፈውን ፡ ሁሉ ፡ በፈጸሙ ፡ ጊዜ ፡ ከንጨቱ ፡ አወረዱት ፡ በመቃብርም ፡ ጨመሩት ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከሙታን ፡ አስነሣው ፡፡ ብዙ ፡ ቀንም ፡ ተገለጠ ፡ ከገሊላ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ወጥተው ፡ ለነበሩ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ምስክሮቹ ፡ ናቸው ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡፡ እኛም ፡ የምስራች ፡ እንነግራችኋለን ፡ ላባቶቻችን ፡ በሆነች ፡ ተስፋ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ እርስዋን ፡ ለኛ ፡ ለልጆቻቸው ፡ እንደ ፡ ፈጸማት ፡ የሱስን ፡ ባስነሣ ፡ ጊዜ ፡፡ እንዲሁም ፡ ተጻፈ ፡ በሁለተኛው ፡ መዝሙር ፡፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ አንተ ፡ ልጄ ፡ ነኽ ፡፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወለድሁኽ ፡፡ እርሱም ፡ ከሙታን ፡ ስለ ፡ አስነሣው ፡ እንጊዲህም ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ እንዳይመለስ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡፡ የዳዊትን ፡ ምህረት ፡ የታመነችውን ፡ እሰጣችኋለሁ ፡፡ ስለዚኽም ፡ በሌላው ፡ ስፍራ ፡ ደግሞ ፡ ይላል ፡፡ ቅዱስህን ፡ ጥፋትን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አተውም ፡፡ ዳዊትስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ በዘመኑ ፡ ካገለገለ ፡ በኋላ ፡ አንቀላፋ ፡፡ ወደባቶቹም ፡ ሔደ ፡ ጥፋትንም ፡ አየ ፡፡ ይኽ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስነሣው ፡ ጥፋትን ፡ አላየም ፡፡ አሁንም ፡ በላንት ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ፡ እላንት ፡ ሰዎች ፡ ወንድማማች ፡ በዚህ ፡ እንዲነገርላችሁ ፡ የኃጢአት ፡ ስርየት ፡፡ በሙሴ ፡ ሕግም ፡ ከርስዋ ፡ ትጸደቁ ፡ ዘንድ ፡ ከተሳናችሁ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡፡ በዚህ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ ይጸደቃል ፡፡ አሁንም ፡ ተጠንቀቁ ፡ እንዳይመጣባችሁ ፡ በነቢያት ፡ የተባለው ፡፡ እዩ ፡ እላንት ፡ ቸልተኞች ፡ ተደነቁም ፡ ጥፉም ፡፡ እኔ ፡ በዘመናችሁ ፡ ስራውን ፡ እሰራለሁና ፡ ማንም ፡ ቢነግራችሁ ፡ የማታምኑትን ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፳፬፡ ፴፮፡—፵፰፡፡

እርሳቸውም ፡ ይህንን ፡ ሲናገሩ ፡ እርሱ ፡ የሱስ ፡ በመኻከላቸው ፡ ቆመ ፡፡ አላቸውም ፡፡ ሰላም ፡ ይሁንላችሁ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ፈሩ ፡ ደነገጡም ፡ መንፈስንም ፡ ያዩ ፡ ይመስላቸው ፡ ነበር ፡፡ አላቸውም ፡፡ ምን ፡ ሆናችሁ ፡ ትደነግጣላችሁ ፡፡ ለምንስ ፡ አሳብ ፡ በልባችሁ ፡ ይወጣል ፡፡ እጄንና ፡ እግሬን ፡ እዩ ፡፡ እኔ ፡ ራሴን ፡ ነኝና ፡፡ ደሱኝ ፡ እዩም ፡፡ መንፈ



ስ ፡ ሥጋና ፡ አጥንት ፡ የለውምና ፡ እንድታዩ ፡ ለኔ ፡ እንዳለኝ ፡፡ ይህነንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እጁንና ፡ እግሩን ፡ አሳያቸው ፡፡ እርሳቸውም ፡ ገና ፡ አላመኑምና ፡ ከደስታና ፡ ከማድነቃቸው ፡ የተነሣ ፡ እርሴ ፡፡ አላቸው ፡፡ ከዚህ ፡ አንዳች ፡ የሚበላ ፡ አላችሁን ፡፡ እርሳቸውም ፡ ከተጠበሰው ፡ ዓሣ ፡ የተከፈለ ፡ ሰጡት ፡፡ ከማር ፡ ወለላም ፡፡ ተቀበለም ፡ በፊታቸውም ፡ በላ ፡፡ አላቸውም ፡፡ ይኽ ፡ ነገር ፡ ከላንት ፡ ጋራ ፡ ሳለሁ ፡ የነገርኋችሁ ፡ ነው ፡፡ በሙሴ ፡ ኦሪት ፡ በነቢያትም ፡ በመዝሙርም ፡ ስለኔ ፡ የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ እንዲገባ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አእምርዋቸውን ፡ ከፈተ ፡ መጽሐፉን ፡ ያስተውሉ ፡ ዘንድ ፡፡ አላቸውም ፡፡ እንዲህ ፡ ተጻፈ ፡ እንዲህም ፡ ተገባ ፡ ክርስቶስ ፡ መከራ ፡ እንዲቀበል ፡ በሶስተኛው ፡ ቀን ፡ ከሙታንም ፡ እንዲነሣ ፡፡ በስሙም ፡ ይሰበካል ፡ በንስሐ ፡ ኃጢአትም ፡ በማስተስረይ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡፡ ከየሩሳሌም ፡ ጀምሮ ፡፡ እላንትም ፡ በዚኽ ፡ ምስክሮች ፡ ናችሁ ፡፡

---

## መጀመርያ ፡ እሁድ ፡ ከፋሲካ ፡ ከኋላ ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አብ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ አንድ ፡ ልጅህን ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችን ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ ለማጽደቃችንም ፡ ይነሣ ፡ ዘንድ ፡ ሰጥተሀዋልና ፡ እኛ ፡ የክፋትንና ፡ የኃጢአትን ፡ እርሾ ፡ እናርቅ ፡ ወትሮም ፡ በሕይወታችን ፡ ንጽሕና ፡ በውነትም ፡ እንገዛልህ ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ በርሱ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ምግባር ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ዮሐንስ ፡ ፭፡ ፬፡—፲፪፡፡

ከእግዚአብሔር ፡ የተወለደ ፡ ሁሉ ፡ ዓለምን ፡ ያሸንፋልና ፡፡ ዓለምንም ፡ የምናሸንፍበት ፡ ማሸነፊ ፡ ይኽች ፡ ናት ፡፡ ሃይማኖታችን ፡ ናት ፡፡ ማነው ፡ ዓለምን ፡ የሚያሸንፍ ፡ የሱስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚያምን ፡ እንጅ ፡፡ ይኽ ፡ ነው ፡ በውኃና ፡ በደም ፡ የመጣ ፡፡ እርሱም ፡ የ

ሶስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ በውኃ ፡ ብቻ ፡ አይደለውም ፡፡ በውኃና ፡ በደም ፡ እንጅ ፡፡ መንፈስም ፡ የሚመሰክር ፡ ነው ፡፡ መንፈስ ፡ እርሱ ፡ እውነት ፡ ነውና ፡፡ በሰማይ ፡ የሚመሰክሩ ፡ ሶስት ፡ ናቸውና ፡ እርሳቸውም ፡ አብ ፡ ቃልም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡ እሌህ ፡ ሶስትም ፡ አንድ ፡ ናቸው ፡፡ በምድርም ፡ የሚመሰክሩ ፡ ሶስት ፡ ናቸው ፡ እርሳቸውም ፡ መንፈስ ፡ ውኃም ፡ ደምም ፡፡ ሶስቱም ፡ ባንድ ፡ ይገጥማሉ ፡፡ የሰውን ፡ ምስክር ፡ ብንቀበል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስክር ፡ እጅግ ፡ ይበልጣል ፡፡ ይኸች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስክር ፡ ናትና ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ የመሰከረባት ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ የሚያምን ፡ ምስክር ፡ በነፍሱ ፡ አለው ፡፡ ለእግዚአብሔር ፡ የማያምን ፡ አሰተኛ ፡ አደረገው ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ በመሰከረባት ፡ ምስክር ፡ አላመነምና ፡፡ ምስክሪቱም ፡ ይኸች ፡ ናት ፡፡ እግዚአብሔር ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንደ ፡ ሰጠነ ፡፡ ይኸችም ፡ ሕይወት ፡ በልጁ ፡ አለች ፡፡ ወልድ ፡ ያለው ፡ ሕይወት ፡ አለችው ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅም ፡ የሌለው ፡ ሕይወት ፡ የለቸውም ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፳፡ ፲፱፡—፳፫፡፡

በዚያም ፡ ቀን ፡ እርሱም ፡ የሰንበት ፡ መጀመርያ ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡፡ ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ወደ ፡ ተከማቹበት ፡ ደጁ ፡ ተቈልፎ ፡ ሳለ ፡ አይሁድን ፡ ስለ ፡ ፈሩ ፡፡ መጣ ፡ የሱስ ፡ በማኸላቸውም ፡ ቆመ ፡ አላቸውም ፡፡ ሰላም ፡ ይሁንላችሁ ፡፡ ይህነንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እጁንና ፡ ጐኑን ፡ አሳያቸው ፡፡ ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ ጌታን ፡ ሲያዩ ፡፡ የሱስም ፡ ደግሞ ፡ አላቸው ፡፡ ሰላም ፡ ይሁንላችሁ ፡፡ አብ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ እንደሁም ፡ እኔ ፡ እልካችኋለሁ ፡፡ ይህነንም ፡ ብሎ ፡ እፍ ፡ አለባቸው ፡ አላቸውም ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተቀበሉ ፡፡ ኃጢአቱን ፡ ያስቀሬችሁለት ፡ ሁሉ ፡ ቀረችለት ፡፡ ያያዛችሁበትም ፡ ሁሉ ፡ ታያዘችበት ፡፡



## ሁለተኛ ፡ እሁድ ፡ ከፈሲካ ፡ በኋላ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንደን ፡ ልጅህን ፡ ምሥዋዕት ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ ምሳሌም ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ ለበጎ ፡ ሕይወት ፡ ሰጥተህልናልና ፡፡ ይህችን ፡ ልክ ፡ የሌላትን ፡ ቸርነቱ ፡ ወትሮ ፡ አመስግነነው ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ፡ የቅድስት ፡ ሕይወቱንም ፡ የተባረከውን ፡ ፈለጋ ፡ ለመከተል ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እንጋደል ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ በርሱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፩፡ ጴጥሮስ ፡ ፪፡ ፲፱፡—፳፭፡፡

ይኸች ፡ ጸጋ ፡ ናትና ፡ ማንም ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘንን ፡ ቢታገሥ ፡ ግፍ ፡ ባገኘው ፡ ጊዜ ፡፡ ምን ፡ ትምክሕት ፡ አላችሁና ፡ ኃጢአትን ፡ ሰርታችሁ ፡ መጽፈትን ፡ ብትታገሡ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ መልካም ፡ አደርጋችሁ ፡ መከራ ፡ ብትቀበሉ ፡ ብትታገሡም ፡ ይኸ ፡ ጸጋ ፡ ነው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡፡ ለዚኽ ፡ ተጸርታችኋልና ፡፡ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ስለኛ ፡ ሕማም ፡ ተቀብልዋልና ፡ ለኛ ፡ ምሳሌን ፡ ትቶ ፡ ፍለጋውን ፡ ትከተሉ ፡ ዘንድ ፡፡ ኃጢአት ፡ ያልሰራ ፡ አሰትም ፡ ባፉ ፡ ያልተገኘበት ፡፡ ሲሰድቡትም ፡ አልተሳደበም ፡፡ መከራም ፡ ሲያመጡበት ፡ አልተቃየመም ፡፡ እውነተኛውን ፡ ፍርድ ፡ ለሚፈርደው ፡ እንጅ ፡ ነፍሱን ፡ ሰጠ ፡፡ እርሱ ፡ ኃጢአታችነን ፡ በሥጋው ፡ የተሸከም ፡ በንጨት ፡ ላይ ፡፡ ከኃጢአት ፡ ወጥተን ፡ ለጽድቅ ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡፡ በቍስሉ ፡ የተፈወሳችሁ ፡፡ እንደ ፡ ጠፉ ፡ በጎች ፡ ነበራችሁና ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ነፍሳችሁ ፡ እረኛና ፡ ጠባቂ ፡ ተመለሳችሁ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፲፡ ፲፩፡—፲፯፡፡

እኔ ፡ ቸር ፡ ጠባቂ ፡ ነኝ ፡፡ ቸር ፡ ጠባቂ ፡ ራሱን ፡ ስለ ፡ በጎቹ ፡ ይለውጣል ፡፡ ብንደኛ ፡ ግን ፡ ጠባቂም ፡ ያይደለ ፡ በጎቹም ፡ የርሱ ፡ ያይደሉ ፡፡ ተኵላ ፡ ሲመጣ ፡ ያያል ፡ በጎችንም ፡ ትቶ ፡ ይሸሻል ፡፡ ተኵላም ፡ ይነጥቃቸዋል ፡ በጎችንም ፡ ይበትናል ፡፡ ብንደኛ ፡ ግን ፡ ብንድኛ ፡ ነውና ፡ ይሸሻል ፡ ለበጎች

ም : አያዝንም :: እኔ : ቸር : ጠባቂ : ነኝ :: በጎቼንም : አው ቃለሁ : በጎቼም : ያውቁኛል :: አብ : እኔን : እንዲያውቀኝ : እኔም : አብን : እንደውቅ :: ራሴንም : ስለ : በጎች : አለው ጣለሁ :: ደግሞም : ሌሎች : በጎች : አሉኝ : ከዚኽ : በረት : ያይደሉ :: እርሳቸውንም : አመጻቸው : ዘንድ : ጊዜ : አለ ኝ :: ቃሌንም : ይሰማሉ :: አንዲት : መንጋም : አንድ : ጠ ባቂም : ይሆናል ::

---

## ሶስተኛ : እሁድ : ከፋሲካ : በኋላ ::

### ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ : በስሕተት : ያሉ : ወደ : ጽድቅ : መንገድ : ይመለሱ : ዘንድ : የውነትህን : ብርሃን : አሳይተህላቸዋልና :: ወደ : ክርስቶስ : ሃይማኖት : አንድነት : ለገቡ : ጸጋ : ስጣቸው : ማምለካቸውን : ከሚ ጸላ : ነገር : ሁሉ : ሸሽተው : የሚወደውን : ነገር : ሁሉ : ይከተሉ : ዘንድ : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

### የመልእክት : ክፍል :: ፩፡ ጴጥሮስ : ፪፡ ፲፩፡—፲፯፡፡

ወዳጆቼ : ሆይ : እንደንግዶች : እንደ : መንገድም : አላፊ ች : እለምናችኋለሁ : ነፍስን : ከምትዋጋ : ከሥጋዊት : መ መኛት : ትርቁ : ዘንድ :: አካሔዳችሁም : በአሕዛብ : መኻ ከል : ያማረ : ይሁን :: በክፉ : የሚናገሩባችሁ : መልካሙ ን : ስራችሁን : ባዩ : ጊዜ : በጥያቄ : ቀን : እግዚአብሔርን : ያመሰግኑ : ዘንድ :: አሁንም : ለሰው : ፍጥረት : ሁሉ : ተ ገዙ : ስለ : እግዚአብሔር :: ለንጉሥ : ቢሆን : በሁሉ : ላይ : ሁንዋልና :: ለመኳንንትም : ለርሳቸው : በክፉ : አድራጎ ች : ለምቅሠፍት : ለበጎ : አድራጎችም : ለምስጋና : ከርሱ : ተልከዋልና :: ይኽች : የእግዚአብሔር : ፈቃድ : ናትና : በ ጎ : በማድረግ : የሰነፎችን : ያለማወቃቸውን : አፍ : ትዘ ጉ : ዘንድ :: የሰው : ልጆች : ሁናችሁ : የሰው : ልጅነታችሁ ም : ለክፋት : መሸፈኛ : አትሁን :: እንደ : እግዚአብሔር : ባሮች : እንጅ :: ሁሉን : አክብሩ :: ወንድሞችን : ውደዱ :: እግዚአብሔርን : ፍሩ :: ንጉሥን : አክብሩ ::



### የወንጌል : ክፍል :: ዮሐንስ : ፲፮፡ ፲፮፡፡

ያ : ከኔ : ይወስደል : ይነግራችሁማል :: በጥቂት : ጊዜ : አ ታዩኝምም :: ደግሞም : በጥቂት : ታዩኛላችሁም :: ወደ : አብ : እሔደለሁና :: ደቀ : መዛሙርቱም : እርሱ : በርሳቸ ው : አሉ :: ምንድር : ነው : ይኽ : እርሱ : የሚለን :: በጥቂ ት : አታዩኝምም :: ደግሞም : በጥቂት : ታዩኛላችሁም :: ወ ደ : አብም : እሔደለሁና :: አሉም :: ምንድር : ነው : ይኽ : ጥቂት : የሚለው :: አናውቅም : የሚናገርበቱን :: የሱስ ም : ይጠይቁት : ዘንድ : እንዲወዱ : አውቀ : አላቸው :: ስ ለዚኽን : እርሱ : በርሳችሁ : ትጠያየቃላችሁ :: በጥቂት : አታዩኝም : ደግሞም : በጥቂት : ታዩኛላችሁም : ብያለሁ ና :: እውነት : እውነት : እላችኋለሁ :: እላንት : እንብን : አፈሳችሁ : እንድታለቅሱ : ዓለም : ግን : ደስ : ይለዋል :: እ ላንትም : ታዝናላችሁ :: ነገር : ግን : አዘናችሁ : ወደ : ደስ ታ : ይለወጣል :: ሴት : ስትማጣ : ጊዜ : ታዝናለች : ጊዜዋ : ደርስዋልና :: ልጅን : ግን : በወለደች : ጊዜ : መከራዋን : ኋ ላ : አታስበውም : ስለ : ደስታ :: ሰው : ወደ : ዓለም : ተወ ልድዋልና :: እላንትም : ዛሬ : አዘን : አላችሁ :: ነገር : ግን : መልሼ : አያችኋለሁ : ልባችሁም : ደስ : ይለዋል :: ደስታ ችሁንም : ከላንት : የሚወስደው : የለም ::

---

## አራተኛ : እሁድ : ከፋሲካ : በኋላ ::

### ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ : አንተ : ብቻ : የኃ ጢአተኞችን : ሁከት : የመላበትን : ልብና : ፈቃድ : መግ ዛት : ትችላለህና :: ለወገኖችህ : ጸጋህን : ስጥ : ያዘዝሀ ውን : ነገር : የወዱ : ዘንድ : ተስፋም : ያስደረግሃቸውን : ደናፈቁ : ዘንድ : እንደሁም : በዓለም : መለዋወጥ : ሁሉ : አይነተኛ : ደስታ : ወደ : ሚገኝበት : ስፍራ : ከዚያም : ልባ ችን : ጸንቶ : ደኖር : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ያዕቆብ ፡ ፩፡ ፲፯፡—፳፩፡፡

በጎ ፡ ስጦታ ፡ ሁሉ ፡ ፍጹምም ፡ መስጠት ፡ ሁሉ ፡ ከላይ ፡ ነው ፡፡ ከብርሃናት ፡ አባት ፡ ወርደ ፡ በርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ መለወጥ ፡ የመተላለፍም ፡ ጽላል ፡ እንኳ ፡ የሌለው ፡፡ እርሱ ፡ በፈቃዱ ፡ በውነት ፡ ቃል ፡ ወለደን ፡፡ የቀደማያት ፡ አይነት ፡ ለርሱ ፡ ፍጥረት ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡፡ ስለዚኽም ፡ የተወደዳችሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ከላንት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለመስማት ፡ የፈጠነ ፡ ይሁን ፡ ለመናገርም ፡ የዘገየ ፡፡ ለቍጣም ፡ የዘገየ ፡፡ የሰው ፡ ቍጣ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጽድቅ ፡ አይሰራምና ፡፡ ስለዚኽም ፡ ርኵሰትን ፡ ሁሉ ፡ የክፋትንም ፡ መላት ፡ አርቁ ፡፡ የተተከለውንም ፡ ቃል ፡ በገርነት ፡ ተቀበሉ ፡፡ ችሎት ፡ ያለውን ፡ ነፍሳችሁን ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፲፮፡ ፯፡—፲፭፡፡

ዛሬ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ላከኝ ፡ እሔዳለሁ ፡ ከላንትም ፡ ማንም ፡ ወዴት ፡ ትሔዳለህ ፡ ብሎ ፡ አይጠይቀኝም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይህነን ፡ ስላልኋችሁ ፡ አዘን ፡ መላ ፡ በልባችሁ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡ ብሔድ ፡ ይጠቅማችኋል ፡፡ እኔ ፡ ባልሔድ ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ አይመጣላችሁምና ፡፡ ብሔድ ፡ ግን ፡ እርሱን ፡ እሰድላችኋለሁ ፡፡ ያም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ዓለሙን ፡ ይዘልፈዋል ፡ ስለ ፡ ኀጢአት ፡ ስለ ፡ ጽድቅም ፡ ስለ ፡ ፍርድም ፡፡ ስለ ፡ ኀጢአትስ ፡ አላመኑብኝምና ፡፡ ስለ ፡ ጽድቅም ፡፡ ወደባቴ ፡ እሔዳለሁና ፡ እንግዲህም ፡ አታዩኝምና ፡፡ ስለ ፡ ፍርድም ፡፡ የዚኽ ፡ ዓለም ፡ ገዢ ፡ ተፈርዶበታልና ፡፡ ደግሞ ፡ ብዙ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ የምነግራችሁት ፡ አለኝ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ ትሸከሙት ፡ ዘንድ ፡ አትችሉትም ፡፡ ያ ፡ ግን ፡ የውነት ፡ መንፈስ ፡ ሲመጣ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ እውነት ፡ ሁሉ ፡ ይመራችኋል ፡፡ ከራሱ ፡ አይናገርምና ፡፡ የሚሰማውን ፡ ይናገራል ፡ እንጂ ፡፡ የሚመጣውንም ፡ ይነግራችኋል ፡፡ ያም ፡ ያመሰግነኛል ፡፡ ከኔ ፡ ይወስዳልና ፡ ይነግራችሁማል ፡፡ ለአብ ፡ ያለ ፡ ሁሉ ፡ ለኔ ፡ ነው ፡፡ ስለዚኽም ፡ አልሁ ፡፡ ያ ፡ ከኔ ፡ ይወስዳል ፡ ይነግራችሁማል ፡፡



## አምስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከፋሲካ ፡ በኋላ ፡፡

ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ካንተ ፡ መጥትዋልና ፡ እኛ ፡ የተዋረድነ ፡ ባሮችህ ፡ በጎ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ እናስብ ፡ ዘንድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ ልባችነን ፡ አንቃ ፡ በምህረትህም ፡ እንፈጽመው ፡ ዘንድ ፡ አቅናን ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ያዕቆብ ፡ ፩፡ ፳፪፡—፳፯፡፡

ቃልንም ፡ አድራጎች ፡ ሁኑ ፡ ሰሞችም ፡ ብቻ ፡ አይደለውም ፡፡ ራሳችሁን ፡ እንዳታሉ ፡፡ ማንም ፡ ቃልን ፡ ሰሚ ፡ ቢሆን ፡ አድራጊም ፡ አይደለም ፡ ይኽ ፡ የፍጥረቱን ፡ ፊት ፡ በማስተወት ፡ የሚያየውን ፡ ሰው ፡ ይመስላልና ፡፡ ራሱንም ፡ ተመለከተና ፡ ሔደ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜውም ፡ የነበረውን ፡ ምሳሌ ፡ ይረሳል ፡፡ ፍጹም ፡ ሕግን ፡ ግን ፡ አርነት ፡ የምታወጣውን ፡ አጥልቆ ፡ የሚመለከት ፡ የሚጸናባትም ፡፡ ሰምቶም ፡ የማይረሳ ፡ ስራን ፡ የሚያደርግ ፡ እንጂ ፡፡ እርሱ ፡ በማድረጉ ፡ የተመሰገነ ፡ ይሆናል ፡፡ በመኻከላችሁ ፡ ማንም ፡ አምልኮኛ ፡ ሁኖ ፡ ቢመስለው ፡ ልሳኑን ፡ የማይለጉም ፡፡ ልቡን ፡ ያስታል ፡ እንጂ ፡፡ የርሱ ፡ አምልኮ ፡ ከንቱ ፡ ናት ፡፡ የነጻች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድም ፡ ያላደፈች ፡ አምልኮ ፡ ይኽች ፡ ናት ፡፡ ሰው ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የሌላቸውን ፡ ባልቴቶችንም ፡ በመከራቸው ፡ ይጐበኛቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ራሱንም ፡ ከዓለም ፡ ርኵሰት ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፲፮፡ ፳፫፡—፴፫፡፡

በዚያም ፡ ቀን ፡ አንዳች ፡ አትለምኑኝም ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ በስሜ ፡ ከአብ ፡ የምትለምኑትን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጣችኋል ፡፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አንዳችን ፡ በስሜ ፡ አለመናችሁም ፡፡ ለምኑ ፡ ትቀበላላችሁም ፡ ደስታችሁ ፡ እንዲፈጸም ፡፡ ይህነን ፡ በምሳሌ ፡ ነገርኋችሁ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሰዓት ፡ ትመጣለች ፡ ደግሞ ፡ በምሳሌ ፡ እንደልነግራችሁ ፡፡ ስለ ፡ አብ ፡ በግልጽ ፡ እነግራችኋለሁ ፡ እንጂ ፡፡ በዚያ ፡ ቀን ፡

በስሜ ፡ ትለምኖላችሁ ። እኔም ፡ አብን ፡ ስለላንተ ፡ እንድ
ለምንላችሁ ፡ የምላችሁ ፡ አይደለሁም ። እርሱ ፡ አብ ፡
ይወዳችኋልና ። እላንተ ፡ ወዳችሁኛልና ፡ እኔም ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ወጣሁ ፡ አምናችኋልና ። ከአብ ፡
ወጣሁ ፡ ወደ ፡ ዓለምም ፡ መጣሁ ። ደግሜም ፡ ዓለምን ፡
እሰነብታለሁ ፡ ወደ ፡ አብም ፡ እሔዳለሁ ። ደቀ ፡ መዛሙር
ቱም ፡ አሉት ። እነሆ ፡ ዛሬ ፡ በግልጥ ፡ ትናገራለኽ ፡ አንድ ፡
ምሳሌም ፡ ስንኳ ፡ አትልም ። ዛሬ ፡ በሁሉ ፡ እንድታውቅ ፡
ማንም ፡ ይጠይቅኽ ፡ ዘንድ ፡ እንደትሻ ፡ አወቅነ ። ስለዚኽ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ወጣኽ ፡ እናምናለን ። የሱስም ፡
መለሰላቸው ፡ አላቸውም ። አሁንን ፡ ታምናላችሁ ። እነ
ሆ ፡ ጊዜው ፡ ይደርሳል ፡ አሁንም ፡ ደረሰ ፡ ትበተኑ ፡ ዘንድ ፡
ኢያንዳንዳችሁ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ። ብቻዬንም ፡ ትተውኛላ
ችሁ ። ብቻዬንም ፡ አይደለሁም ። አብ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ነውና ።
ይኽነን ፡ በኔ ፡ ሰላም ፡ ይሆንላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ነገርኋችሁ ።
በዓለም ፡ መከራ ፡ ያገኛችኋል ። ነገር ፡ ግን ፡ አይዞዋችሁ ።
እኔ ፡ ዓለምን ፡ አሸነፍሁ ።

## የዕርገት ፡ በዓል ።

## ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ያንድ ፡ ልጅህን ፡
የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ዕርገት ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
እንደ ፡ አመነ ፡ እንዲሁም ፡ እኛ ፡ በልባችንና ፡ በመንፈሳ
ችን ፡ ወደዚያ ፡ እንወጣ ፡ ዘንድ ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ለወ
ትሮ ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ በርሱ ፡ካንተና ፡
ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ በሚኖር ፡ በሚገዛም ፡ አንድ ፡
አምላክ ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

በመልእክት ፡ ፈንታ ። የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፩፥ ፩—፲፩።

መጀመርያው ፡ ነገርስ ፡ ታኦፊላ ፡ ሆይ ፡ የሱስ ፡ ያስተ
ምር ፡ ዘንድ ፡ ያደርግም ፡ ዘንድ ፡ በጀመረው ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡
ጸፍሁ ። የመረጻቸውን ፡ ሐዋርያቱን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡



እስኪያዝበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡ እስኪወጣ ፡
ድረስ ። ደግሞም ፡ ሕማማትን ፡ ከተቀበለ ፡ በኋላ ፡ ራሱን ፡
ሕያው ፡ ሁኖ ፡ አሳያቸው ፡ በብዙ ፡ በማይጠራጠርበት ፡ ነገ
ር ፡ ተገልጾ ። ሲታያቸው ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡
መንግሥትንም ፡ ነገር ፡ ሲነግራቸው ። ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ አ
ብሮ ፡ ሳለ ፡ ከየሩሳሌም ፡ እንዳይወጡ ። የአብን ፡ ተስፋ ፡
ደጅ ፡ እንዲጸኑ ፡ እንጅ ፡ አዘዛቸው ። ከኔ ፡ የሰማችሁት
ን ፡ ብሎ ። ዮሐንስ ፡ በውኃ ፡ ያጠምቅ ፡ ነበርና ። እላንት ፡ ግ
ን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ትጠመቃላችሁ ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በ
ኋላ ። የተከማቹም ፡ ጠየቁት ፡ አሉትም ። አቤቱ ፡ በዚኽ
ን ፡ ወራት ፡ መንግሥት ፡ ለእሥራኤል ፡ ትመልሳለኽ ። አላ
ቸውም ። አብ ፡ በሥልጣኑ ፡ ያደረጋትን ፡ ዘመንና ፡ ጊዜው
ን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ለላንት ፡ አልተሰጠም ። ነገር ፡ ግን ፡ ኃ
ይልን ፡ ትቀበላላችሁ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሲወርድባችሁ ፡ ጊ
ዜ ። ምስክሮችም ፡ ትሆኑልኛላችሁ ፡ በየሩሳሌም ፡ በይሁ
ዳም ፡ ሁሉ ፡ በሰማርያም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ጫራሽም ፡ ድ
ረስ ። ይህነንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ከርሳቸው ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፡
እርሳቸው ፡ ሲያዩት ። ደመናም ፡ ተቀበለችው ፡ካደናቸው
ም ፡ ተሠወረ ። እርሳቸውም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ሲመለከቱ ፡ እ
ርሱ ፡ ሲወጣ ። እነሆ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በርሳቸው ፡ ዘንድ ፡
ቆሙ ፡ ነጭ ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ። ያልዋቸው ። እላንት ፡ የ
ገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ለምን ፡ ቆማችኋል ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ኢያያች
ሁ ። ይኽ ፡ የሱስ ፡ ከላንት ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣ ፡ ወደ ፡
ሰማይ ፡ ሲወጣ ፡ እንዳያችሁት ፡ እንዲሁም ፡ ይመጣል ።

## የወንጌል ፡ ክፍል ። ማርቆስ ፡ ፲፮፥ ፲፬—፳።

ኋላም ፡ ለሥራ ፡ አንዱ ፡ ታየ ፡ ተቀምጠው ፡ ሲበሉ ። ስ
ለ ፡ ሃይማኖታቸውም ፡ መጉደል ፡ ስለ ፡ ልባቸውም ፡ ጽና
ት ፡ ገሠፃቸው ፡ ያዩትን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ አላመኑምና ። አ
ላቸውም ። ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ሒዱ ፡ በወንጌልም ፡ ስበ
ኩ ፡ ለፍጥረት ፡ ሁሉ ። ያመነ ፡ የተጠመቀም ፡ ይድናል ።
ያላመነ ፡ ግን ፡ ይፈረድበታል ። ያመኑትንም ፡ ይኽች ፡ ታም

ራት ፡ ትከተላለች ። በስሜ ፡ አጋንንትን ፡ ያወጣሉ ። ባዲስ ፡ ቋንቋም ፡ ይናገራሉ ። እባብንም ፡ ይይዛሉ ። የሚገድል ፡ ነገርም ፡ ቢጠጡ ፡ አይጉዳቸውም ። እጆቸውን ፡ በድውያን ፡ ላይ ፡ ይጭናሉ ፡ እርሳቸውም ፡ ይድናሉ ። ጌታም ፡ ከነገራቸው ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ቀኝ ፡ ተቀመጠ ። እርሳቸው ፡ ግን ፡ ወጡ ፡ በስፍራውም ፡ ሁሉ ፡ አስተማሩ ። ጌታም ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ሰራ ፡ ነገራቸውንም ፡ አጸና ፡ እርሳቸውን ፡ በምትከተል ፡ ታምራት ። አሜን ።

---

## ከዕርገት ፡ በኋላ ፡ የሚከተል ፡ እሁድ ።

### ጸሎት ።

አምላክ ፡ ሆይ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ አንተ ፡ አንድ ፡ ልጅህን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ በታላቅ ፡ ምስጋና ፡ በሰማይ ፡ ወደለኸ ፡ መንግሥትህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርገሃልና ። ደስታ ፡ አልባኑረን ፡ አታሳድረን ፡ እንለምንሃለን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህን ፡ ያጸናን ፡ ዘንድ ፡ ስደድልን ፡ እንጅ ፡ መድኀኒታችንም ፡ ክርስቶስ ፡ ቀድሞ ፡ ወደ ፡ ሔደበት ፡ ወደዚያም ፡ ከፍ ፡ አድርግን ፡ እርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ይኖራል ፡ ይገዛልም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩ ጴጥሮስ ፡ ፬ ፯—፲፩ ።

የነገር ፡ ሁሉ ፡ መጨረሻ ፡ ቀርብዋል ። ስለዚህም ፡ አስተውሉ ፡ ለጸሎትም ፡ ትጉ ። ከሁሉም ፡ በፊት ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ የምትቃጠል ፡ ፍቅር ፡ ትኑርላችሁ ። ፍቅር ፡ የኃጢአትን ፡ ብዛት ፡ ትሠውራለችና ። እንግዶችን ፡ የምትወዱ ፡ ሁኑ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ያለ ፡ ማንጐራጐር ። ሁሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ በተቀበለው ፡ ጸጋ ፡ መጠን ፡ ባልንጀራውን ፡ ያገልግለው ። እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጸጋው ፡ ደህና ፡ መጋቦች ። የሚናገር ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይናገር ። የሚያገለግል ፡ እግዚአብሔር ፡ ኀይል ፡ እንደ ፡ ሰጠው ፡ ያገልግል ። እግዚአብሔር ፡ በሁሉ ፡ ይመሰ



ገን ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። ምስጋና ፡ ያለው ፡ ቸሎትም ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፲፭ ፳፮—፲፮ ፬ ።

የሚያጸና ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ ግን ፡ ሲመጻ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ለላንት ፡ የምሰደው ፡ ከአብ ፡ ዘንድ ። ከአብ ፡ የሚወጣ ። የውነት ፡ መንፈስ ። እርሱ ፡ ስለኔ ፡ ይመሰክራል ። እላንትም ፡ ደግሞ ፡ ትመሰክራላችሁ ። ከመጀመርያ ፡ጀምራችሁ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነበራችሁና ። ይህቺን ፡ ነገርኋችሁ ፡ እንደትጠራጠሩ ። ከጉባዕያቸው ፡ ያወጥዋችኋል ። ነገር ፡ ግን ፡ ጊዜ ፡ ትመጣለች ፡ የሚገድላችሁ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያገለግል ፡ እንዲመስለው ። ይህቺንም ፡ ያደርጉባችኋል ፡ አብን ፡ አያውቁምና ፡ እኔንም ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህቺን ፡ ነገርኋችሁ ፡ ጊዜው ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ እንድታስብዋት ፡ እንደልኋችሁ ።

---

## የጰራቅሊጦስ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

አቤቱ ፡ አንተ ፡ በዚህ ፡ ወራት ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስህን ፡ ብርሃን ፡ ሰደህ ፡ የታመኑ ፡ የሕዝብህን ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ አስተማርህ ፡ እንደሁም ፡ በዚያ ፡ መንፈስ ፡ ስጠን ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ቅን ፡ ፍርድ ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ በተቀደሰም ፡ መጽናቱ ፡ ደስ ፡ ይበለን ፡ ዘንድ ፡ በመድኀኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ምግባር ፡ እርሱም ፡ በዚያ ፡ መንፈስ ፡ አንድነት ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ኑሮ ፡ ይገዛል ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

### በመልእክት ፡ ፈንታ ። የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፪ ፩—፲፩ ።

የጰንጠቆስቴ ፡ ቀንም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ሁላቸው ፡ ያንድ ፡ ልብ ፡ ሁነው ፡ ባንድ ፡ ነበሩ ። ድንገትም ፡ ከሰማይ ፡ እንደ ፡ ዓውሎ ፡ ነፋስ ፡ ድምፅ ፡ ሆነ ። ተቀምጠውበት ፡ የነበሩትንም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ መላው ። የተከፋፈለችም ፡ የሳት ፡ ልሳን ፡ ታየቻቸው ። ከርሳቸውም ፡ በያንዳንዱ ፡ ተቀ

መጠባቸው :: በሁላቸውም : መንፈስ : ቅዱስ : መላባቸው :: በሌሎች : ቋንቋዎችም : ይናገሩ : ዘንድ : ጀመሩ : መንፈስ : ቅዱስ : ይነበቡ : ዘንድ : እንደ : ሰጣቸው :: በየሩሳሌምም : የተቀመጡ : ሰዎች : ነበሩ : አይሁድ : በጎ : ሰዎች :: ከሰማይ : በታች : ካሉ : ከአሕዛብ : ሁሉ :: ይኸችም : ድምጽ : በሆነች : ጊዜ : ሁሉ : ባንድ : ተሰበሰቡ : ተደነቁም :: ከርሳቸው : ኢያንዳንዱ : ይሰማቸው : ነበረና : በየቋንቋው : ሲናገሩ :: ሁሉም : ደነገጡ : አደነቁም : እንደህ : ሲሉ : እርሱ : በርሳቸው :: እሌኽ : ሁሉ : የሚናገሩ : የገሊላ : ሰዎች : አይደሉምን :: እንዴት : እኛ : ኢያንዳንዳችን : በተወለድንበት : በቋንቋችን : ሲናገሩ : እንሰማቸዋለን :: እኛ : ጳርትያውያን : ሜድያንም : ኤላሚጡኒም :: በወንዞች : ማኸልም : የተቀመጥን :: በይሁዳም : በቀጳዶቅያም :: በጰንጦስም : በእስያም :: በፈርጊያም :: በጰንፊልያም :: በምሥርም :: በደወለ : ልብያም : ወደ : ቀሬኔን : የቀረበች :: የሮምም : እንግዶች :: አይሁድም : መጻተኞችም :: ከእቅሬጥስም : ያሉ : ዓረቦችም :: የእግዚአብሔርን : ታላቅነት : ሲናገሩ : በኛ : ቋንቋ : እንሰማቸዋለን ::

## የወንጌል : ክፍል :: ዮሐንስ : ፲፬፡ ፲፭፡—፴፩፡፡

ብትወዱኝ : ትእዛዜን : ጠብቁ :: እኔም : አብን : እለምናለሁ : ሌላውንምም : የሚያጸና : ይሰጣችኋል : ከላንት : ጋራ : ለዘላለም : ይኖር : ዘንድ :: የእውነትን : መንፈስ : ዓለም : ይቀበለው : ዘንድ : የማይችለውን :: ኢያየውምና : አያውቀውምምና :: እላንት : ግን : ታውቁታላችሁ :: ከላንት : ዘንድ : ይኖራልና : በላንትም : ይሆናል :: አባትና : እናት : እንደሌላቸው : ሁናችሁ : አልተዋችሁም :: ወደላንት : እመጣለሁ :: ገና : ጥቂት : ዘመን : ዓለምም : ደግሞ : አያየኝም :: እላንት : ግን : ታዩኛላችሁ :: እኔ : ሕያው : ነኝና : እላንትም : ሕያዋን : ትሆናላችሁ :: የዚያን : ቀን : እኔ : ባባቴ : እንደ : ሆንሁ :: እላንትም : በኔ :: እኔም : በላንት : ታውቃላችሁ :: ትእዛዛቴ : ያሉት : የሚጠብቃቸውም : እር



ሱ : ነው : የሚወደኝ :: የሚወደኝንም : አባቴ : ይወደዋል :: እኔም : እወደዋለሁ :: ነፍሴንም : እገልጥለታለሁ :: አለው : ይሁዳ : ያስቆሮቱ : አይደለም :: ጌታ : ሆይ : ምንድር : ነው : ማለትህ : ነፍስኽን : ለኛ : ትገልጥ : ዘንድ : እንደለኽ : ለዓለምም : አይደለም :: መለሰ : የሱስ : አለውም :: ማንም : ቢወደኝ : ቃሌን : ይጠብቃል :: አባቴም : ይወደዋል :: ወደርሱም : እንመጣለን : በርሱም : ዘንድ : ማደርያ : እናደርጋለን :: የማይወደኝ : ቃላቴን : አይጠብቅም :: የምትሰሙትም : የኔ : አይደለም :: የላከኝ : የአብ : እንጂ :: ይህችን : ነገርኋችሁ : ከላንት : ጋራ : ሳለሁ :: የሚያጸና : ግን : እርሱም : መንፈስ : ቅዱስ : አብ : በስሜ : የሚሰደው : እርሱ : ሁሉን : ያስተምራችኋል :: ያልኋችሁንም : ሁሉ : ያሳስባችኋል :: ሰላምን : እተውላችኋለሁ :: የኔን : ሰላም : እሰጣችኋለሁ :: ዓለም : እንደሚሰጥ : እኔ : የምሰጣችሁ : አይደለም :: ልባችሁ : አይደንግጥ : አይፈራም :: እንደልኋችሁ : ሰማችሁ : እሔዳለሁ : ወደላንትም : እመጣለሁ :: ብትወዱኝስ : ደስ : ባላችሁ : ነበር : ወደ : አብ : እሔዳለሁ : ስላልኋችሁ :: አባቴ : እርሱ : ከኔ : ይበልጣልና :: አሁንም : አስቀድሞ : ሳይሆን : አልኋችሁ :: ሲደርስ : ጊዜ : ታምኑ : ዘንድ :: ደግሞ : ከላንት : ጋራ : እጅግ : አልናገርም :: የዚኽ : ዓለም : ገዢ : ይመጣልና : ለርሱም : በኔ : አንዳች : የለውም :: ነገር : ግን : ዓለም : ያውቅ : ዘንድ : ነው : እኔ : አብን : እንድወድ :: አብም : እንደዘዘኝ : እንደህ : አደርጋለሁ ::

## የጰራቅሊጦስ : ሰኞ ::

### ጸሎት ::

አቤቱ : አንተ : በዚህ : ወሪት : የመንፈስ : ቅዱስህን : አስተብርሃን : ሰደህ : የታመኑ : የሕዝብህን : ልብ : እንደ : አስተማርህ : እንዴሁም : በዚያ : መንፈስ : ስጠን : በነገር : ሁሉ : ቅን : ፍርድ : ይሆንልን : ዘንድ : በተቀደሰም : መጽናቱ :

ደስ : ይበለን : ዘንድ : በመድኃኒታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ምግባር : እርሱም : በዚያ : መንፈስ : አንድነት : ካንተ : ጋራ : አንድ : አምላክ : ኑሮ : ይገዛል : ለዘላለም ። አሜን ።

በመልእክት : ፈንታ ። የሐዋርያት : ሥራ : ፲፥ ፴፬—፵፫።

ጴጥሮስም : አፉን : ከፈተ : አለም ። በውነት : አስተውላለሁ : እግዚአብሔር : ለሰው : ፊት : እንደ ያደላ ። ነገር : ግን : በሕዝብ : ሁሉ : የሚፈራው : ቅን : ነገርም : የሚያደርግ : እርሱ : በርሱ : ዘንድ : የተወደደ : ነው ። ወደ : እሥራኤል : ልጆች : የላከውን : ነገር : የምስራች : ይነግራቸው : ዘንድ : በዕርቅ : በየሱስ : ክርስቶስ ። እርሱ : የሁሉ : ጌታ : ነው ። ይኽነን : ነገር : እላንተ : ታውቃላችሁ : በይሁዳ : ሁሉ : የሆነውን : ከገሊላ : ጀምሮ : ዮሐንስ : ከሰበከበት : ጥምቀት : በኋላ ። ስለ : የሱስ : ስለ : ናዝሬቱ : እግዚአብሔር : በመንፈስ : ቅዱስና : በኃይል : እንደ : ቀባው : ዞሮ : መልካምን : ያደረገ : ሰይጣን : ያሸነፋቸውንም : ሁሉ : የፈወሰ ። እግዚአብሔር : ከርሱ : ጋራ : ነበረና ። እኛም : ምስክሮች : ነን : ባደረገው : ነገር : ሁሉ : በይሁዳ : አገር : በየሩሳሌምም ። ይህነን : በንጨት : ላይ : ሰቅለው : ገደሉት ። ይኽነንም : እግዚአብሔር : አስነሣው : በሦስተኛ : ቀን ። ሰጠውም : ይገለጥ : ዘንድ ። ለሕዝብ : ሁሉ : አይደለም ። ለኛ : እንጅ : እግዚአብሔር : አስቀድሞ : ምስክሮች : እን ሆን : ዘንድ : ለመረጠን ። ከርሱም : ጋራ : የበላን : የጠጣንም : ከሙታን : ከተነሣ : በኋላ ። ለሕዝብም : እንሰብክ : ዘንድ : አዘዘን : እንመሰክርም : ዘንድ : እርሱ : እንደ : ሆነ : በእግዚአብሔር : የተሠራ : የሕያዋንና : የሙታን : ፈራጅ : ይሆን : ዘንድ ። ለርሱም : ነቢያት : ሁሉ : ይመሰክራሉ : በርሱ : የሚያምን : ሁሉ : የኃጢአቱን : ስርየት : እንዲወስድ : በስሙ ። ጴጥሮስም : ገና : ይህነን : ነገር : ሲናገር : መንፈስ : ቅዱስ : ነገሩን : በሰሙት : ሁሉ : ላይ : ወረደ ። ከግዝረት : ወገንም : የነበሩ : ምእምናን : ሁሉ :



ከጥጴሮስ : ጋራ : መጥተው : የነበሩ : ተደነቁ ። የመንፈስ : ቅዱስ : ስጥወታ : በአሕዛብም : ደግሞ : ፈስዋልና ። በሌላ : ቋንቋ : ሲናገሩ : እግዚአብሔርንም : ሲያከብሩ : ሰምተዋቸዋልና ። የዚያን : ጊዜም : መለሰ : ጴጥሮስ : አለም ። በውኑ : ማንም : ውኃውን : ይከለክልን : ዘንድ : ይችላል : እሌህ : እንደይጠመቁ ። መንፈስ : ቅዱስን : ወስደዋልና : እኛ : ደግሞ : እንደ : ወሰድነው ። በጌታ : ስምም : ይጠመቁ : ዘንድ : አዘዛቸው ። የዚያን : ጊዜ : ለመኑት : ከዚያ : አያሌ : ቀን : ይቀመጥ : ዘንድ ።

የወንጌል : ክፍል ። ዮሐንስ : ፫፥ ፲፮—፳፩።

እግዚአብሔር : እንዲሁ : ዓለሙን : ወድዋልና : አንድ : ልጁን : እስኪ ሰውጥ : ድረስ ። በርሱ : የሚያምን : ሁሉ : እንደይጠፋ ። የዘላለም : ሕይወት : እንድትሆንለት : እንጅ ። እግዚአብሔር : ልጁን : ወደ : ዓለም : አላከምና : ዓለምን : ሊኰንን ። ነገር : ግን : ዓለም : ይድንበት : ዘንድ ። በርሱ : የሚያምን : አይኰነንም ። የማያምንበትም : አሁን : የተኰነነ : ነው ። ባንድ : በእግዚአብሔር : ልጅ : ስም : አያምንምና ። ኵነኔዉቱም : ይህች : ናት ። ብርሃን : ወደ : ዓለም : መጥትዋልና : ሰዎችም : ጨለማውን : ወደዱ : ከብርሃን : ይልቅ ። ስራቸው : ክፉ : ናትና ። ክፉ : የሚያደርግ : ሁሉ : ብርሃንን : ይጠላልና ። ወደ : ብርሃንም : አይቀርብም : ስራው : እንደይዘለፍ ። እውነት : ግን : የሚያደርግ : ወደ : ብርሃን : ይመጣል : ስራው : ትገለጥ : ዘንድ : በእግዚአብሔር : የተደረገች : ናትና ።

የጰራቅሊጦስ : መክሰኞ ።

ጸሎት ።

አቤቱ : አንተ : በዚህ : ወራት : የመንፈስ : ቅዱስህን : ብርሃን : ሰደህ : የታመኑ : የሕዝብህን : ልብ : እንደ : አስተማርህ : እንደሁም : በዚያ : መንፈስ : ስጠን : በነገር : ሁሉ : ቅን : ፍርድ : ይሆንልን : ዘንድ : በተቀደሰም : መጽናቱ :

ደስ : ይበለን : ዘንድ : በመድኃኒታችን : በየሱስ : ክርስ ቶስ : ምግባር : እርሱም : በዚያ : መንፈስ : አንድነት : ካ ንተ : ጋራ : አንድ : አምላክ : ኑሮ : ይገዛል : ለዘላለም :: አሜን ::

በመልእክት : ፈንታ :: የሐዋርያት : ሥራ : ፰፤ ፲፬—፲፯::

በየሩሳሌምም : የነበሩ : ሐዋርያት : የሰማርያ : ሰዎች : የእግዚአብሔርን : ቃል : እንደ : ተቀበሉ : በሰሙ : ጊዜ : ጴጥሮስንና : ዮሐንስን : ሰደዱላቸው :: እርሳቸውም : ወደ ርሳቸው : በገቡ : ጊዜ : በላያቸው : ጸለዩ : መንፈስ : ቅዱስ ን : ይቀበሉ : ዘንድ :: ገና : ባንዳቸው : እንኳ : አይወርድ ም : ነበረና :: በየሱስ : ስም : ብቻ : ተጠምቀው : ነበሩ : እ ንጂ :: የዚያን : ጊዜም : እጃቸውን : ጫኑባቸው : መንፈ ስ : ቅዱስንም : ተቀበሉ ::

የወንጌል : ክፍል :: ዮሐንስ : ፲፤ ፩—፲::

እውነት : እውነት : እላችኋለሁ :: በደጅ : ያልገባ : ወደ : በጎች : በረት : በሌላ : ስፍራ : የሚገባ : እንጅ : እርሱ : ሌ ባና : ወንበዴ : ነው :: በደጅ : ግን : የሚገባ : እርሱ : የበጎ ች : ጠባቂ : ነው :: ለርሱም : በረኛው : ይከፍትለታል : በጎ ችም : ቃሉን : ይሰማሉ :: እርሱም : የርሱን : በጎች : በየስ ማቸው : ይጸራቸዋል : ያወጣቸዋልም :: የርሱንም : በጎች : ሲያወጣ : ጊዜ : በፊታቸው : ይሔደል :: በጎችም : ይከተሉ ታል :: ድምጹን : ያውቃሉና :: ሌላውን : ግን : አይከተሉም :: ከርሱ : ይሸሻሉ : እንጅ :: የሌሎችን : ድምጽ : አያውቁም ና :: ይህነን : ምሳሌ : አላቸው : የሱስ :: እርሳቸው : ግን : የ ነገራቸውን : ምን : እንደ : ሆነ : አላስተዋሉም :: የሱስም : ደግሞ : አላቸው :: እውነት : እውነት : እላችኋለሁ :: እኔ : የበጎች : ደጅ : ነኝ :: ከኔ : በፊት : የመጡ : ሁሉ : እርሳቸ ው : ሌቦችና : ወንበዴች : ናቸው :: ነገር : ግን : በጎች : አል ሰሟቸውም :: ደጁ : እኔ : ነኝ :: ማንም : በኔ : ቢገባ : ይ ድናል :: ይገባልም : ይወጣልም : መሰማርያውንም : ያገኛ ል :: ሌባው : አይመጣም : ሊሰርቅ : እንጅ : ሊገልም : ሊ



ያጠፋም :: እኔ : መጣሁ : ሕይወት : ሊሆንላቸው : እጅግ : ጽጋብም : እንዲሆንላቸው ::

---

የሥላሴ : እሁድ ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ : ሆይ :: እኛ : እውነተኛውን : ሃይማኖት : ታምነን : የዘላለምን : የሥላሴን : ክብር : እናስታውቀበት : ዘንድ : በአምለካዊትም : ልዕ ልና : ላንድነት : እንገዛ : ዘንድ : ለባሮችህ : ጸጋህን : ሰጥተ ህናልና : እንለምንሃለን : በዚች : ሃይማኖት : እንድታጸናን : ለዘወተርም : ከመከራ : ሁሉ : እንድጠብቀን : አንተ : ያ ለህ : የምትገዛም : ለዘላለም : አንድ : አምላክ :: አሜን ::

በመልእክች : ፈንታ :: ራእይ : ፬፤ ፩—፲፩::

ከዚያ : ወዲያም : አየሁ : በሰማይም : እነሆ : ደጅ : ተ ከፈተ :: የፊተኛውም : ድምፅ : እንደ : መለከት : ድምፅ : የሰማሁቱ : ተናገረኝ : እንዲህ : ሲል :: ወደዚኽ : ውጣ :: ከዚኽም : በኋላ : ይሆን : ዘንድ : ያለውን : አሳይኻለሁ :: የዚያን : ጊዜውም : በመንፈስ : ነበርሁ :: እነሆም : ዙፋ ን : በሰማይ : ቁምዋል :: በዙፋኑም : ላይ : ተቀማጭ :: የ ተቀመጠበትም : በማየት : የኢያስጲድን : ደንጊያ : መሰ ለ : ሰርዲኖስንም :: የደመና : ቀስትም : በዙፋኑ : ዙርያ : ነበረ : በማየት : የመረግድን : ደንጊያ : የሚመስል :: በዙፋ ን : ዙርያም : ሀያ : አራት : ዙፋኖች : ነበሩ :: በዙፋኖች ም : ላይ : ሀያ : አራት : ሽማግሎች : ተቀምጠው : ነጭ : ል ብስንም : ለብሰው : አየሁ :: በራሳቸውም : ላይ : የወ ርቅ : አክሊል : ነበረ :: ከዙፋኑም : ወጣ : መብረቅ : ነጐ ድጓድም : ድምፅም :: ሰባትም : የሳት : መብራቶች : በ ዙፋኑ : ፊት : ተቃጠሉ :: እርሳቸውም : የእግዚአብሔር : ሰባት : መናፍስት : ናቸው :: በዙፋኑም : ፊት : የብርጭቆ : ባሕር : ቢረሌን : የሚመስል : ነበረ :: በዙፋኑም : ውሥጥ : በዙፋኑም : ዙርያ : አራት : እንስሶች : ነበሩ : ዓይን : የመ ላባቸው : በፊትና : በኋላ :: የፊተኛውም : እንስሳ : አንበ

ሳውን ፡ መሰለ ፡፡ ሁለተኛውም ፡ እንስሳ ፡ ላምን ፡ መሰለ ፡፡ ሶስተኛውም ፡ እንሰሳ ፡ ፊት ፡ ነበረለት ፡ እንደ ፡ ሰው ፡፡ አራተኛውም ፡ እንስሳ ፡ የሚበረውን ፡ ንስር ፡ መሰለ ፡፡ አራት ፡ እንስሶችም ፡ ለያንዳንዱ ፡ በዙርያቸው ፡ ስድስት ፡ ክንፎች ፡ ነበሩላቸው ፡፡ በውሥጣቸውም ፡ ዓይን ፡ መልቶባቸዋል ፡፡ ዕረፍትም ፡ አልነበረላቸውም ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሁሉን ፡ ያያዘ ፡፡ የነበረ ፡ ያለም ፡ የሚመጣም ፡፡ እንስሶችም ፡ ክብር ፡ ገናንነትም ፡ ምስጋናም ፡ በሰጡ ፡ ጊዜ ፡ በዙፋን ፡ ላይ ፡ ለተቀመጠ ፡ ለዘላለሙ ፡ ሕያው ፡ ሁኖ ፡ ለሚኖር ፡፡ ሀያ ፡ አራቱ ፡ ሽማግሎች ፡ በዙፋን ፡ ላይ ፡ በተቀመጠው ፡ ፊት ፡ ይወድቃሉ ፡ ለዘላለሙም ፡ ሕያው ፡ ሁኖ ፡ ለሚኖር ፡ ይሰግዳሉ ፡፡ አካሊላቸውንም ፡ በዙፋን ፡ ፊት ፡ ይጥላሉ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡ ላንተ ፡ ይገባል ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ ምስጋና ፡ ክብርም ፡ ችሎትም ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡፡ አንተ ፡ ሁሉን ፡ ፈጥረኻልና ፡ ሁሉም ፡ በፈቃድኽ ፡ ሁንዋልና ፡ ተፈጠረም ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፫፤ ፩፤—፲፰፡፡

ከፈሪሳውያን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፡ ስሙም ፡ ኒቆዲሞስ ፡ የአይሁድ ፡ አለቃ ፡፡ ይኽ ፡ ወደ ፡ የሱስ ፡ መጣ ፡ በሌት ፡ አለውም ፡፡ ረቢ ፡ አንተ ፡ መምህር ፡ ሁነኽ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ መጣኽ ፡ እኛ ፡ እናውቃለን ፡፡ አንድም ፡ የሚችል ፡ የለምና ፡ አንተ ፡ የምታደርጋትን ፡ ተአምራት ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በርሱ ፡ ጋራ ፡ካለ ፡ በቀር ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለውም ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡ እልኻለሁ ፡፡ ማንም ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ካልተወለደ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፡፡ ኒቆዲሞስም ፡ አለው ፡፡ እንዴት ፡ ይችላል ፡ ሰው ፡ ይወለድ ፡ ዘንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ሲሆን ፡፡ ወደናቱ ፡ ሆድ ፡ ተመልሶ ፡ ሁለተኛ ፡ ይወለድ ፡ ዘንድ ፡ ይችላልን ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡ እልኻለሁ ፡፡ ማንም ፡ ከውኃና ፡ ከመንፈስ ፡ ካልተወለደ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ አይ



ችልም ፡፡ ከሥጋ ፡ የተወለደ ፡ ሥጋ ፡ ነው ፡፡ ከመንፈስም ፡ የተወለደ ፡ መንፈስ ፡ ነው ፡፡ አታድንቅ ፡ ስላልሁኽ ፡፡ ይገባችኋል ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ትወለዱ ፡ ዘንድ ፡፡ ንፋስ ፡ ወደ ፡ ወደደችው ፡ ትነፍሳለች ፡፡ ድምፅዋንም ፡ ትሰማለኽ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከወዴት ፡ ትመጻለች ፡ ወዴት ፡ ዘንድም ፡ ትሔዳለች ፡ አታውቅም ፡፡ እንዲሁም ፡ ከመንፈስ ፡ የሚወለድ ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡፡ ኒቆዲሞስም ፡ መለሰ ፡ አለውም ፡፡ እንዴት ፡ ይቻላል ፡ ይህ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለውም ፡፡ አንተ ፡ የእሥራኤል ፡ መምህር ፡ ነህ ፡ ይህነንም ፡ አታውቅምን ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡ እልኻለሁ ፡፡ በምናውቀው ፡ እንናገራለን ፡ ባየነውም ፡ እንመሰክራለን ፡፡ ምስክራችነንም ፡ አትቀበሉም ፡፡ የምድሩን ፡ ነገር ፡ ነግሬያችሁ ፡ ባታምኑ ፡፡ እንዴት ፡ የሰማዩን ፡ ነገር ፡ ብነግራችሁ ፡ ታምናላችሁ ፡፡ ማንምም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አልወጣም ፡ ከሰማይ ፡ ከወረደ ፡ በቀር ፡፡ እርሱም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በሰማይ ፡ የሚኖር ፡፡ ሙሴም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እባብን ፡ ከፍ ፡ እንደ ፡ አደረገ ፡፡ እንዲሁም ፡ ይገባዋል ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከፍ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡፡ በርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ እንዳይጠፋ ፡፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ እንድትሆንለት ፡ እንጂ ፡፡

---

መጀመርያ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

ጸሎት ፡፡

አምላክ ፡ ሆይ ፡ ባንተ ፡ ለሚታመኑ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ኃይላቸው ፡ ነህና ፡ ጸሎታችነን ፡ በምህረትህ ፡ ተቀበል ፡፡ እኛም ፡ ከሞት ፡ በታች ፡ ባለች ፡ ጠባያችን ፡ ደክመናለንና ፡ ያላንተም ፡ ምንምን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ለማድረግ ፡ አይቻልነምና ፡ በፈቃድና ፡ በስራ ፡ ትእዛዛትህን ፡ ጠብቀን ፡ ደስ ፡ እናሰኝህ ፡ ዘንድ ፡ የጸጋህን ፡ ረዴት ፡ ስጠነ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፩፤ ዮሐንስ ፡ ፬፤ ፯፤—፳፩፡፡

ወዳጆቼ ፡ ሆይ ፡ እርሱ ፡ በርሳችን ፡ እንዋደድ ፡፡ ፍቅር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ናትና ፡፡ የሚወድም ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔ

ር : የተወለደ : ነው : እግዚአብሔርንም : ያውቃል :: የማይወድም : እግዚአብሔርን : አያውቅም :: እግዚአብሔር : ፍቅር : ነውና :: በዚኽ : ተገለጠ : የእግዚአብሔር : ፍቅር : ወደኛ :: እግዚአብሔር : አንድ : ልጁን : ወደ : ዓለም : ላኪልና : በርሱ : እንድንበት : ዘንድ :: ፍቅርም : በዚኽ : ናት :: እኛ : እግዚአብሔርን : እንደ : ወደድነው : አይደለም :: እርሱ : እንደ : ወደደን : እንጂ :: ልጁንም : እንደ : ላከ : ማስተስረያ : ይሆን : ዘንድ : ስለ : ኀጢአታችን :: ወዳጆቼ : ሆይ : እግዚአብሔር : እንዲህ : የወደደን : ከሆነ : ለኛም : እርሱ : በርሳችን : እንዋደድ : ዘንድ : ይገባናል :: እግዚአብሔርን : ማንም : ከቶ : አላየውም :: እርሱ : በርሳችን : ብንዋደድ : እግዚአብሔር : ይኖርብናል :: ፍቅሩም : በኛ : የተፈጸመች : ትሆናለች :: በዚኽ : እናውቃለን : እኛ : በርሱ : እንድኖር : እርሱም : በኛ :: ከመንፈሱ : ሰጥቶናልና :: እኛም : አይተናል : እንመሰክርማለን : አብ : ልጁን : እንደ : ላከ : ዓለምን : ያድን : ዘንድ :: የሱስ : የእግዚአብሔር : ልጅ : እንደ : ሆነ : የሚያምን :: እግዚአብሔር : ይኖርበታል : እርሱም : በእግዚአብሔር :: እግዚአብሔርም : ወደኛ : ያለችውን : ፍቅር : እኛ : እናውቃለን : እናምንበትማለን :: እግዚአብሔር : ፍቅር : ነው :: በፍቅርም : የሚኖር : በእግዚአብሔር : ይኖራል : እግዚአብሔርም : በርሱ :: በዚኽ : ፍቅሩ : ከኛ : ጋራ : ተፈጸመች :: ድፍረት : ትሆንልን : ዘንድ : በፍርድ : ቀን :: እርሱ : እንደሆነ : እንዲሁም : እኛ : በዚኽ : ዓለም : ነን :: በፍቅር : ፍርሃት : የለም :: የተፈጸመች : ፍቅር : ፍርሃትን : ወደ : ሜዳ : አውጥታ : ትጥላለች : እንጂ :: በፍርሃት : ሥቃይ : ነውና :: የሚፈራም : በፍቅር : አልተፈጸመም :: እኛ : እንወደዋለን :: እርሱ : አስቀድሞ : ወደናልና :: እግዚአብሔርን : እወደዋለሁ : ብሎ : ወንድሙን : የሚጸላ : አሰተኛ : ነው :: ያየውን : ወንድሙን : ያልወደደ : ያላየውን : እግዚአብሔርን : ይወድ : ዘንድ : እንዴት : ይችላልና :: ይኽችንም : ትእዛዝ : ከርሱ : ተቀበልን :: እግዚአብሔርን : የሚወድ : ወንድሙን : ደግሞ : እንዲወድ ::



## የወንጌል : ክፍል :: ሉቃስ : ፲፮፡ ፲፱፡—፴፩፡፡

አንድ : ባለ : ጠጋ : ሰው : ነበረ :: እርሱም : ቀይ : ሐር : የተልባ : እግርም : ቃጭን : ሸማ : ለበሰ : ዕለት : ዕለትም : በጌጡ : ደስ : ይለው : ነበር :: አንድ : ድኻም : ስሙን : አልዓዛር : የሚሉት : ነበረ :: በደጅ : ሰላሙም : ተጣለ : ገላው : ሁሉ : በጨንኰር : ሲመላ :: ከባለ : ጠጋው : ማዕድም : ከሚወድቀው : ፍርፋሪ : ይጸግብ : ዘንድ : ተመኘ :: ውሾችም : መጥተው : ጨንኰሩን : ይልሱት : ነበር :: ድኻውም : እነሆ : ሞተ :: መላእክትም : ይዘውት : ወደ : አብርሃም : ብብት : ወሰዱት :: ባለ : ጠጋውም : እርሱ : ደግሞ : ሞተ : ተቀበረም :: በሲኦልም : በሥቃይ : ሳለ : ዓይኑን : ባነሣ : ጊዜ : እርሱ : አብርሃምን : ከሩቅ : አየ : አልዓዛርንም : በብብቱ : ተጠግቶ :: እርሱም : ጸራ : አለም :: አባቴ : ሆይ : አብርሃም : ማረኝ :: አልዓዛርንም : ስደድልኝ : የጣቱን : ጫፍ : በውኃ : ነክሮ : መላሴን : ያስቀዘቅዝልኝ : ዘንድ :: በዚኽ : እሳት : እሣቀያለሁና :: አብርሃምም : አለ :: ልጄ : ሆይ : አስብ : አንተ : በሕይወት : ሳለኽ : በጎ : ነገርህን : ፈጽመኽ : እንደ : ተቀበልኽ :: አልዓዛርም : እንዲሁ : መከራውን :: አሁንም : እርሱ : ደስ : ይለዋል : አንተም : ትሣቀያለኽ :: ከዚኽም : ሁሉ : ጋራ : በኛና : በላንተ : መኻከል : ታላቅ : ገደል : ጸንቶ : ተተከለ :: ከዚኽ : ወደላንተ : ማለፍ : የሚሹ : እንዳይችሉ :: ከዚያም : ያሉ : ወደኛ : እንዳያልፉ :: አለም :: እንኪያስ : እለምንኻለሁ : አባቴ : ሆይ : ወደባቴ : ቤት : ትሰደው : ዘንድ :: አምስት : ወንድሞች : አሉኝና :: እንዲመሰክርላቸው : እርሳቸውም : ደግሞ : ወደዚኽ : ወደ : ሥቃይ : ስፍራ : እንዳይመጡ :: አብርሃምም : አለው :: ሙሴና : ነቢያት : አልዋቸው : እርሳቸውን : ይስሙ :: እርሱም : አለ :: አይደለም : አባቴ : ሆይ : አብርሃም :: ነገር : ግን : ከሞቱት : አንድ : ቢሔድባቸው : ንስሐ : ይገባሉ :: አብርሃምም : አለው :: ከሙሴና : ከነቢያትስ : ካልሰሙ : ከሙታንም : አንድ : ቢነሣ : አያምኑትም ::

## ሁለተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ::

### ጸሎት ::

አቤቱ : አንተ : በጽኑ : ፍርሃትህና : ውድህ : የምታሳድ
ግሃቸውን : ሳትረደቸው : ሳትገዛቸውም : አትቀርምና : በ
ቸር : ዕውቀትህ : እንድትጠብቀን : እንለምንሃለን : ቅዱስ :
ስምህንም : ወትሮ : አስፍሬንና : አስውደድን : በየሱስ : ክ
ርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

### የመልእክት : ክፍል :: ፩ ዮሐንስ : ፫ ፲፫—፳፬ ::

አታድንቁ : ወንድሞቼ : ሆይ : ዓለም : ቢጸላችሁ :: እኛ :
ከሞት : ወጥተን : ወደ : ሕይወት : እንደ : ደረስነ : እናው
ቃለን :: ወንድሞችን : እንወደለንና :: ወንድሙን : የማይ
ወድ : በሞት : ይኖራል :: ወንድሙን : የሚጸላ : ሁሉ : ነ
ፍስ : ገደይ : ነው :: እላንተም : ነፍስ : ገደይ : ሁሉ : የዘ
ላለም : ሕይወት : እንደሌለው : ታውቃላችሁ :: በዚኽ : ፍ
ቅሩን : አወቅነ : ስለኛ : ሬሱን : ለውጦታልና :: ለኛም : ይ
ገባል : ሬሳችነን : ስለ : ወንድሞች : እንለውጥ : ዘንድ ::
የዚኽ : ዓለም : ጥሪት : ያለው : ወንድሙንም : አንደች :
ሲሻ : የሚያየው : ርኅራኄውንም : የሚከለክልበት : የእ
ግዚአብሔር : ፍቅር : እንዴት : ይኖርበታል :: ልጆቼ : ሆይ : አ
ንውደድ : በቃል : በመላስም :: በስራና : በውነት : እንጅ ::
በዚኽም : እናውቃለን : እኛ : ከውነት : እንደሆነ :: በፊቱ
ም : ልባችነን : እናጸናለን :: ልባችን : ቢነቅፈን : እግዚአብ
ሔር : ከልባችን : ይበልጣልና : ሁሉንም : ያውቃል :: ወደ
ጆቼ : ሆይ : ልባችንስ : ባይነቅፈን : ድፍረት : አለነ : ወደ : እ
ግዚአብሔር :: የምንለምነውንም : ሁሉ : ከርሱ : እንወስደ
ለን :: ትእዛዙንም : እንጠብቃለንና : በፊቱም : ደስ : የሚያ
ሰኘውን : ነገር : እናደርጋለንና :: ትእዛዙም : ይኸች : ናት :
እናምን : ዘንድ : በልጁ : በየሱስ : ክርስቶስ : ስም :: እር
ሱ : በርሳችንም : እንዋደድ : ዘንድ : ትእዛዙን : እንደ : ሰ
ጠነ :: ትእዛዙንም : የሚጠብቅ : በርሱ : ይኖራል : እርሱ
ም : ደግሞ : በርሱ : ይኖራል :: በዚኽም : እናውቃለን : እር
ሱ : በኛ : እንደ ኖር :: ለኛ : ከሰጠው : ከመንፈሱ ::



### የወንጌል : ክፍል :: ሉቃስ : ፲፬ ፲፯—፳፬ ::

አንድ : ሰው : ታላቅ : ምሳውን : አደረገ : ብዙ : ሰዎችን
ም : ጸሬ :: በምሳም : ጊዜ : ባርያውን : ላከ : የተጸሩትን :
ኑ : ሁሉ : ፈጽሞ : ተዘጋጅቷዋልና : ይል : ዘንድ :: ሁሉም :
ባንድ : እምቢ : ለማለታቸው : መክንያትን : ያመጡ : ዘ
ንድ : ጀመሩ :: የፊተኛው : አለው : ምድርን : ገዝቻለሁ :
የግድም : ወደርሱ : መውፀት : አየው : ዘንድ : ያሻኛል ::
እንድተወኝ : እለምንኻለሁ :: ሌላውም : አለ : አምስት :
ጽምድ : በሮች : ገዝቻለሁ : ልፈትናቸውም : እሔደለሁ ::
እለምንኻለሁ : ትተወኝ : ዘንድ :: ሌላውም : አለው : ም
ሽት : አግብቻለሁ : ስለዚኽም : መምጣት : አይቻለኝም ::
ያም : ባርያ : በመጣ : ጊዜ : ይህነን : ለጌታው : ነገረው :: የ
ዚያን : ጊዜም : ባለቤቱ : ተቈጣ : ባርያውንም : አለው ::
ፈጥነኽ : ወደገር : ገቢያና : አደባባይ : ውጣ : ድኆችንም :
ጕባጦችንም : አንካሶችንም : ዕውሮችንም : ወደዚኽ : አ
ግባ :: ባርያውም : አለ :: አቤቱ : እንደዘዝኸኝ : ሆነ : ገና
ም : ስፍሬ : አለ :: ጌታውም : ባርያውን : አለ :: ወደ : መ
ንገድ : ወደጥርም : ውጣ :: የግድም : ሊገቡ : በላቸው : ቤ
ቴ : ይመላ : ዘንድ :: እላችኋለሁና :: ከለዚኽ : ከተጸሩት :
ሰዎች : አንድ : ስንኳ : እራቴን : እንደይቀምስ ::

---

## ሶስተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ::

### ጸሎት ::

አቤቱ : በምህረት : እንድትሰማነ : እንለምንሃለን :: እን
ጸልይም : ዘንድ : ከለልባችን : እንደስወደድህነ : እንደ
ሁም : በብርቱ : ረዲትህ : በፍርሃትና : በመከሬ : ሁሉ :
እንጠበቅ : ዘንድ : ፍቀድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታ
ችን :: አሜን ::

### የመልእክት : ክፍል :: ፩ ጴጥሮስ : ፭ ፭—፲፩ ::

ሁላችሁም : እርሱ : በርሳችሁ : ተገዙ :: ትሕትናውን
ም : ልበሱ :: እግዚአብሔር : ልባቸውን : የሚያስታብዩ

ን ፡ ይጻላልና ፡ ለትሑታንም ፡ ጸጋውን ፡ ይሰጣል ። እንጊ ዴህ ፡ ዝቅ ፡ በሉ ፡ ከጸናችው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በታ ች ። በጊዜው ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋችሁ ፡ ዘንድ ። ትካዝያ ችሁንም ፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡ ጣሉት ። እርሱ ፡ ያስብላችኋል ና ። አቅሞውን ፡ ጠብቁ ። ትጉም ። ሰይጣን ፡ ጸላታችሁ ፡ እንደሚጮኽ ፡ አንበሳ ፡ ይዞራልና ፡ የሚውጠውን ፡ ሰው ፡ ሽቶ ። እርሱን ፡ በሃይማኖት ፡ ጸንታችሁ ፡ ተቃወሙት ። እ ንዴህም ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ በዓለም ፡ ባሉ ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ እንዲፈጸም ፡ እወቁ ። የጸጋም ፡ ሁሉ ፡ አምላክ ፡ እኛን ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ክብሩ ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ የጸራን ። ጥቂ ት ፡ መከራ ፡ ብትቀበሉ ፡ እርሱ ፡ ያበጃችኋል ። ያጸናችኋል ም ። ያበርታችኋልም ። ይመሠርታችኋልም ። ለርሱ ፡ ክ ብር ፡ ችሎትም ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፭፡ ፩፡—፲።

ወደርሱም ፡ ቀራጮችና ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ ሊሰሙት ፡ ቀረቡ ። ፈሪሳውያንና ፡ ጻፎችም ፡ አንጐረጐሩ ፡ እንዴህ ፡ ሲሉ ። ይኽስ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ ይቀበላል ፡ ከርሳቸውም ፡ ጋ ራ ፡ ይበላል ። ይህነንም ፡ ምሳሌ ፡ ነገራቸው ፡ እንዴህ ፡ ሲ ል ። ማን ፡ ሰው ፡ ከላንት ፡ መቶ ፡ በግ ፡ ያለው ፡ ከርሳቸው ፡ አንዲ ፡ ቢጠፋ ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙን ፡ በምድረ ፡ በደ ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ጠፋ ፡ አይሔድም ፡ እስኪያገኘው ፡ ድረስ ። ሲያገኘውም ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ ይሸከመዋል ። ወደ ፡ ቤትም ፡ ሲመጣ ፡ ጊዜ ፡ ወደጀቹን ፡ ይጸራል ፡ ጎረቤቶቹን ም ፡ እንዴህ ፡ ሲላቸው ። ከኔ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ የጠ ፋውን ፡ በጌን ፡ አገኘቻለሁና ። እላችኋለሁ ፡ እንዴሁም ፡ በሰማይ ፡ ደስታ ፡ ይሆናል ፡ ንስሐ ፡ በሚገባ ፡ ባንድ ፡ ኃጢ አተኛ ፡ ከዘጠና ፡ ዘጠኝ ፡ ጻድቃን ፡ ይልቅ ፡ ንስሐ ፡ ከማይሹ ። ወይስ ፡ ምን ፡ ሴት ፡ ናት ፡ አሥር ፡ ድሪም ፡ ያላት ። አንድ ፡ ድሪም ፡ ባጠፋች ፡ ጊዜ ፡ መብራት ፡ አብርታ ፡ ቤቱን ፡ የ ማትጸርግ ፡ እስክታገኘውም ፡ ድረስ ፡ ተግታ ፡ የማትሻው ። ባገኘችውም ፡ ጊዜ ፡ ወደጀችዋን ፡ ትጸራለች ፡ ጎረቤቶችዋን



ም ፡ እንዴህ ፡ ስትል ። ከኔ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ የጠፋ ብኝን ፡ ድሪሜን ፡ አገኘቻለሁና ። እንዴሁም ፡ እላችኋለሁ ፡ ደስታ ፡ ይሆናል ፡ በእግዚአብሔር ፡ መላእክት ፡ ፊት ፡ ንስሐ ፡ በሚገባ ፡ ባንድ ፡ ኃጢአተኛ ።

---

## አራተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሠላሴ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

አምላክ ፡ ሆይ ፡ ላምኑብህ ፡ ሁሉ ፡ ጠባቂ ፡ ያለህ ። ያላን ተ ፡ ከቶ ፡ ብርቱ ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ቅዱስ ፡ ነገርም ፡ የለም ። ምህረትህን ፡ ጨምርና ፡ አብዛልን ፡ አንተ ፡ ገዛችንና ፡ መ ርያችን ፡ ሁነህ ፡ ባለማዊ ፡ ነገር ፡ እንዴህ ፡ ታሳልፈን ፡ ዘንድ ፡ የዘላለምን ፡ ነገር ፡ በመጨረሻ ፡ እንደናጣ ። ይህነን ፡ ስጥ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መክንያት ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ሮሜ ፡ ፰፡ ፲፰፡—፳፫።

እኔ ፡ የዚህ ፡ ዘመን ፡ መከራ ፡ የሚመጣውን ፡ በኛ ፡ ይገለ ጥ ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡ ክብር ፡ እንዲይተካከለው ፡ እቈጥ ራለሁ ። የፍጥረት ፡ አለኝታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ልጆች ፡ መ ገለጥ ፡ ትቈያለችና ። ፍጥረት ፡ ለከንቱ ፡ ተገዝታለችና ፡ በ ፈቃድዋ ፡ አይደለም ። ነገር ፡ ግን ፡ በተስፋ ፡ ስላስገዛት ። ፍጥረትም ፡ እርስዋ ፡ ደግሞ ፡ አርነት ፡ ትወጣለችና ፡ ከጥፋ ት ፡ ባርነት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ክብር ፡ አርነት ። ፍ ጥረት ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንድትጣጣር ፡ እንድትማጣም ፡ እናውቃለን ። እርስዋም ፡ ብቻ ፡ አይደለ ም ። እኛም ፡ እንጅ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ቀደማያት ፡ ያለ ን ። እኛም ፡ በነፍሳችን ፡ እንጣጣራለን ፡ ልጅነትንም ፡ ማ ለት ፡ የሥጋችንን ፡ መደን ፡ እንቈያለን ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፮፡ ፴፮—፵፪።

እንጊዴህ ፡ የምትራሩ ፡ ሁኑ ፡ አባታችሁ ፡ ደግሞ ፡ እርሱ ፡ ርሩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ። አትፍረዱም ፡ አይፈረድባችሁምም ። አትኰንኑም ፡ አትኰነኑምም ። ይቅርም ፡ በሉ ፡ ይቅርም ፡

ይባልላችኋል ። ስጡም ፡ ይሰጣችሁማል ። መልካም ፡ መስፈርያ ፡ የመላ ፡ የተረፈም ፡ የፈሰሰም ፡ በብብታችሁ ፡ ይሰጥዋችኋል ። በምትሰፍሩት ፡ መስፈርያ ፡ በርሱ ፡ ይሰፍሩላችኋልና ። ምሳሌንም ፡ ነገራቸው ። ዕውር ፡ ዕውርን ፡ ሊመራ ፡ ይችላልን ። ሁለታቸው ፡ በጕድጓድ ፡ ይወድቁ ፡ የለምን ። ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ከመምህሩ ፡ የሚበልጥ ፡ አይደለም ። ፈጹም ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ መምህሩ ፡ ይሆናል ። ለምንስ ፡ ታያለኽ ፡ በወንድምኽ ፡ ዓይን ፡ ያለውን ፡ ጕድፍ ። ባይንኽም ፡ ያለውንም ፡ ጕንድ ፡ አታስተውለውም ። ወይስ ፡ እንዴት ፡ ትችላለኽ ፡ ወንድምኽን ፡ ትለው ፡ ዘንድ ። ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ተወኝ ፡ ጕድፏን ፡ ካይንኽ ፡ አወጣ ፡ ዘንድ ። አንተም ፡ ባይንኽ ፡ ያለውን ፡ ጕንድ ፡ አታይም ። አንተ ፡ ግብዝ ፡ አስቀድመኽ ፡ የዓይንኽን ፡ ጕንድ ፡ አውጣ ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ በወንድምኽ ፡ ዓይን ፡ ያለውን ፡ ጕድፍ ፡ ታወጣ ፡ ዘንድ ፡ ታያለህ ።

---

አምስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

ጸሎት ።

አቤቱ ፡ እንለምንሃለን ፡ የዚህ ፡ ዓለምን ፡ ሩጫ ፡ እንደ ፡ ህ ፡ ለርቅ ፡ ታቀና ፡ ዘንድ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ በቀስታ ፡ ሁሉ ፡ በደስታም ፡ እስክታገለግልህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፤ ጴጥሮስ ፡ ፫፤ ፰፤—፲፭።

የዚኽም ፡ ፈጻሜ ፡ ያንድ ፡ ልብ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ ከሚያዝንም ፡ ጋራ ፡ የምታዝኑ ። እንደ ፡ ወንድሞችም ፡ የምትወዱ ። መሓሮችም ። የተዋረዳችሁም ። በክፉም ፡ ክፉ ፡ አትመልሱ ፡ በስድብም ፡ ስድብ ። ይኽነን ፡ ትታችሁ ፡ ባርኩ ፡ እንጂ ። ለዚህ ፡ እንደ ፡ ተጸራችሁ ፡ አውቃችኋልና ፡ በረከትን ፡ ትወርሱ ፡ ዘንድ ። ሕይወትን ፡ ይወድ ፡ ዘንድ ፡ መልካምንም ፡ ዘመን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ የሚሻ ። መላሱን ፡ ከክፉ ፡ ይከልክል ። ከንፈሮቹንም ፡ ሸንግላውን ፡ እ



ንደይናገሩ ። ከክፉ ፡ ይራቅ ፡ መልካምም ፡ ያድርግ ። ሰላምን ፡ ይሻ ፡ ይከተላትም ። የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ በጸድቃን ፡ ላይ ። ጆሮቹም ፡ ወደ ፡ ልመናቸው ፡ ይላሉ ። የእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ ነው ። ማነው ፡ የሚጐዳችሁ ፡ የመልካም ፡ ተከታዮች ፡ ብትሆኑ ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ጽድቅ ፡ መከራ ፡ ብትቀበሉ ፡ ደግሞ ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ። ከፍርሃታቸውም ፡ አትፍሩ ፡ አትደንግጡም ። ነገር ፡ ግን ፡ ጌታን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በልባችሁ ፡ ቀድሱት ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፭፤ ፩፤—፲፩።

ሆነም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ወደርሱ ፡ በተጋፉ ፡ ጊዜ ። እርሱ ፡ በጌንሳሬጥ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ ቁሞ ፡ ነበረ ። ሁለት ፡ ሰምቡቆችንም ፡ አየ ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ ቁመው ። አጽማጆችም ፡ ከርሳቸው ፡ መርበብታቸውን ፡ ሊያጥቡ ፡ ይወጡ ፡ ነበሩ ። ለሲሞንንም ፡ ወደ ፡ ነበረችው ፡ ወደንዲቱ ፡ ወፅቶ ፡ ከምድር ፡ ጥቂት ፡ ፈቀቅ ፡ ያደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ለመነው ። በመርከብ ፡ ተቀምጦም ፡ አሕዛብን ፡ አስተማረ ። ነገሩንም ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ሲሞንን ፡ አለ ። በጥልቅ ፡ ላይ ፡ ስረር ፡ መርበባችሁንም ፡ ለማጽመድ ፡ ጣሉ ። ሲሞንም ፡ መለሰ ፡ አለውም ። መምህር ፡ ሆይ ፡ ሌቱን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመን ፡ ደከምነ ፡ ምንም ፡ አልያዝነም ። ነገር ፡ ግን ፡ በቃልኽ ፡ መርበብቱን ፡ እጥላለሁ ። ይህነንም ፡ ባደረጉ ፡ ጊዜ ፡ ካሣው ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ወሰዱ ፡ መርበባቸውም ፡ ተቀደደች ። በሌላ ፡ ሳምቡቅም ፡ የነበሩትን ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ መጥተው ፡ ያግዝዋቸው ፡ ዘንድ ፡ ጠቀሱ ። መጡም ፡ ሁለቱንም ፡ መርከቦች ፡ መሉ ፡ ለመሥጠም ፡ እስኪቀርቡ ፡ ድረስ ። ሲሞን ፡ ጴጥሮስም ፡ ያነን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ በየሱስ ፡ ጕልበት ፡ ዘንድ ፡ ወደቀ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ከኔ ፡ ራቅ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ። እኔ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ነኝና ። ድንጋጼ ፡ ይዞት ፡ ነበረና ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የነበሩትን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ አጸመዱት ፡ ዓሣ ። እንደዪሁም ፡ ያዕቆብንና ፡ ዮሐንስን ፡ የዘብዴዎስን ፡ ልጆች ፡ የሲሞን ፡ አንጋሮች ፡ የነበሩትን ። የሱስም ፡ ሲሞንን ፡ አለ

ው ፡፡ አትፍራ ፡፡ ከንጊዜህ ፡ ወዲህ ፡ ሰውን ፡ አጥማጅ ፡ ትሆናለኽ ፡፡ መርከቢቱንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ወሰዱ ፡ ሁሉንም ፡ ተውና ፡ ተከተሉት ፡፡

ስድስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

ጸሎት ፡፡

አምላክ ፡ ሆይ ፡ ለሚወዱህ ፡ የሰውን ፡ አእምሮ ፡ የሚያልፈውን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አዘጋጅተሃልና ፡፡ አንተን ፡ መውደድ ፡ በልባችን ፡ አፍስስ ፡ እኛ ፡ አንተን ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ወደን ፡ መሻታችንን ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጠውን ፡ ተስፋ ፡ እናገኝ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ሮሜ ፡ ፮ ፫—፲፩፡፡

ወይስ ፡ አታውቁምን ፡ እኛ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የተጠመቅነ ፡ በሞቱ ፡ እንደ ፡ ተጠመቅነ ፡፡ እንጊዜህ ፡ በጥምቀት ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ለሞት ፡ ተቀበርነ ፡፡ ክርስቶስ ፡ በአብ ፡ ክብር ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ እንዲሁም ፡ እኛ ፡ በሕይወት ፡ መታደስ ፡ እንመላለስ ፡ ዘንድ ፡፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ በሞቱ ፡ ምሳሌ ፡ የተተከልነ ፡ ከሆነ ፡ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ እንሆናለን ፡ በትንሣኤው ፡፡ ይህነን ፡ አውቀን ፡ ያረጀ ፡ ሰዋችን ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ተሰቀለ ፡፡ የኀጢአት ፡ ሥጋ ፡ ይሻር ፡ ዘንድ ፡ እኛ ፡ እንጊዜህ ፡ ለኀጢአት ፡ ባሮች ፡ እንዳንሆን ፡፡ የሞተ ፡ ከኀጢአት ፡ ተጸድቋልና ፡፡ ከክርስቶስ ፡ ጋራም ፡ ከሞትነ ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ በሕይወት ፡ እንድንኖር ፡ እናምናለን ፡፡ አውቀናልና ፡ ክርስቶስ ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ ደግሞም ፡ አይሞትም ፡፡ ሞትም ፡ ደግሞ ፡ አይገዛበትም ፡፡ በሞቱ ፡ ለኀጢአት ፡ እንደግዜ ፡ ሙትዋልና ፡፡ በሕይወቱ ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ፡፡ እንዲሁም ፡ እላንት ፡ ከኀጢአት ፡ እንደ ፡ ሞታችሁ ፡፡ በሕይወትም ፡ እንድትኖሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ በጌታችን ፡ ራሳችሁን ፡ ቍጠሩ ፡፡



የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፭ ፳—፳፮፡፡

እኔ ፡ እነግራችኋለሁና ፡ ጽድቃችሁ ፡ ከጸሐፎትና ፡ ከፈሪሳውያን ፡ ጽድቅ ፡ ካልበዛች ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አትገቡም ፡፡ ለቀደሙት ፡ የተባለውን ፡ ሰማችሁ ፡፡ አትግደል ፡፡ የገደለ ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋልና ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፡፡ በወንድሙ ፡ በከንቱ ፡ የተቈጣ ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ እንዲገባው ፡፡ ወንድሙንም ፡ ጨርቅ ፡ ለባሽ ፡ የሚለው ፡ በሸንጎ ፡ ይፈረድበታል ፡፡ ሰነፍም ፡ የሚለው ፡ የገሃነም ፡ እሳት ፡ ይገባዋል ፡፡ ቍርባንኽንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ብታቀርብ ፡፡ ከዚያም ፡ ወንድምኽን ፡ ባንዳች ፡ አሳዝነኽው ፡ እንደሆነ ፡ ብታስብ ፡፡ ቍርባንኽን ፡ ከዚያ ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ ተወው ፡ አስቀድመኽም ፡ ሒድ ፡ ከወንድምኽ ፡ ጋራም ፡ ታረቅ ፡፡ ኋላም ፡ ተመልሰኽ ፡ ቍርባንኽን ፡ አቅርብ ፡፡ ከጸላትኽ ፡ ጋራ ፡ ፈጥነኽ ፡ ተሰማማ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ በመንገድ ፡ ሳለኽ ፡፡ ጸላትኽ ፡ ለመኰንን ፡ አሳልፎ ፡ እንዳይሰጥኽ ፡ መኰንኑም ፡ ላሳሪ ፡ ይሰጥኻል ፡ ወደ ፡ ግዞትም ፡ ትጣላለኽ ፡፡ በውነት ፡ እልኻለሁ ፡ ኋለኛውን ፡ ዲዋኒ ፡ እስክትከፍል ፡ ድረስ ፡ ከዚያ ፡ እንዳትወጣ ፡፡

ሰባተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

ጸሎት ፡፡

የኃይልና ፡ የችሎት ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ የበጎ ፡ ነገርም ፡ ሁሉ ፡ ፈጣሪና ፡ ሰጭ ፡፡ ስምህን ፡ መውደድ ፡ በልባችን ፡ ቅረጽ ፡ አይነተኛውንም ፡ አምልኮ ፡ በውሥጣችን ፡ አብዛ ፡ በጐነትንም ፡ ሁሉ ፡ መግበን ፡ በርሱም ፡ በታላቅ ፡ ምህረትህ ፡ አኑርን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ሮሜ ፡ ፮ ፲፱—፳፫፡፡

እንደ ፡ ሰው ፡ እናገራለሁ ፡ ስለ ፡ ሥጋችሁ ፡ ድካም ፡፡ ብልቶቻችሁን ፡ ለርኵስነት ፡ ሕግንም ፡ ለመተላለፍ ፡ ባሮች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሕግን ፡ ለመተላለፍ ፡ እንደ ፡ ሰጣችሁ ፡፡ እ

ንደሁም : አሁን : ብልቶቻችሁን : ለጽድቅ : አስግዙ : ለቅድስና :: ለኃጢአት : ባሮች : ሳላችሁ : ከጽድቅ : አርነት : ወጥታችሁ : ነበረችሁና :: ነገር : ግን : ምን : ፍሬ : ነበራችሁ : የዚያን : ጊዜ : በስራችሁ : ዛሬ : ከርሶ : የምታፍሩበት :: የዚያ : ስራ : ፍጻሜ : ሞት : ነውና :: ዛሬ : ግን : ከኃጢአት : አርነት : ወጥታችሁ : ለእግዚአብሔር : ተገዝታችኋልና : ፍሬያችሁን : አላችሁ : ለቅድስና :: ፍጻሜውም : የዘላለም : ሕይወት : ናት :: የኃጢአት : ደመወዜ : ሞት : ነውና :: የእግዚአብሔር : ስጥወታ : ግን : የዘላለም : ሕይወት : ናት : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን ::

የወንጌል : ክፍል :: ማርቆስ : ፰፡ ፩፡—፱::

በዚያ : ወራት : ሰው : እጅግ : በበዛ : ጊዜ : የሚበሉትም : ባልነበራቸው : ጊዜ :: የሱስ : ደቀ : መዛሙርቱን : ወደርሱ : ጸራ :: አላቸውም :: እኔ : ለሕዝብ : አዝናለሁ :: ከኔ : ጋራ : ተቀምጠው : ሶስት : ቀን : ሁንዋቸዋልና : የሚበሉትም : የላቸውም :: ጾም : አድረውም : ወደ : ቤታቸው : ብሰደቻቸው : በመንገድ : ደደክማሉ :: ከርሳቸው : አያሌ : ከሩቅ : መጥተው : ነበሩና :: ደቀ : መዛሙርቱም : መለሱለት : እንደህ : ሲሉ :: ከወዴት : ይችላል : ሰው : እሌህን : ከዚህ : በምድረ : በዳ : እንጀራ : ያጸግብ : ዘንድ :: ጠየቃቸውም : ስንት : እንጀራ : አላችሁ : ብሎ :: እርሳቸውም : ሰባት : አሉት :: ሰዎችንም : በምድር : ላይ : ይቀመጡ : ዘንድ : አዘዛቸው :: ሰባቱንም : እንጀራ : ወሰደ : ባረከውም : ቈረሰውም :: ለደቀ : መዛሙርቱም : ያቀርቡላቸው : ዘንድ : ሰጣቸው : ለሕዝብም : አቀረቡ :: ጥቂት : ዓሣም : ነበረችላቸው : ባረካትም : እርስዋም : ደግሞ : ትቀርብ : ዘንድ : አዘዘ :: በሉም : ጸገቡም :: የቍራሾንም : ትራፊ : አነሡ : ሰባት : ቅርጫት :: የበሉትም : አራት : ሺህ : ያህላሉ ::

---



ስምንተኛ : እሁድ : ከሠላሴ : በኋላ ::

ጸሎት ::

አምላክ : ሆይ : ከቶ : የማትገድፍ : ዕውቀትህ : በሰማይና : በምድር : ያለውን : ነገር : ሁሉ : አቅንታለችና :: እኛ : በትሕትና : እንለምንሃለን : የሚጐዳውን : ነገር : ሁሉ : ከኛ : ታርቅ : ዘንድ : የሚጠቅምንም : ትሰጥን : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ሮሜ : ፰፡ ፲፪፡—፲፯::

አሁንም : ወንድሞቼ : ሆይ : ባልደች : ነነ : ደሮ : ለሥጋ : አይደለም : እንደ : ሥጋ : እንኖር : ዘንድ : አይደለም : እንደ : ሥጋ : ብትኖሩ : ልትሞቱ : ናችሁና :: በመንፈስ : ግን : የሥጋን : ስራ : ብትገድሉ : በሕይወት : ትኖራላችሁ :: በእግዚአብሔር : መንፈስ : የሚሔዱ : ሰዎች : እርሳቸው : የእግዚአብሔር : ልጆች : ናቸውና :: የባርነትን : መንፈስ : አልወሰዳችሁምና : ደግማችሁ : ለመፍራት :: የልጅነትን : መንፈስ : ወሰዳችሁ : እንጅ : አብ : ሆይ : አባታችን : ብለን : የምንጸራበት :: ያ : መንፈስም : ከመንፈሳችን : ጋራ : እኛ : የእግዚአብሔር : ልጆች : እንደ : ሆነ : ይመሰክራል :: ልጆችም : ከሆነ : ወራሾችም : ነነ :: የእግዚአብሔር : ወራሾች :: ከክርስቶስም : ጋራ : እንወርሳለን :: ከርሶ : ጋራ : መከራ : ብንቀበል : ከርሶ : ጋራ : ደግሞ : እንከብር : ዘንድ ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፯፡ ፲፭፡—፳፩::

ተጠንቀቁ : ካሰተኞች : ነቢያት :: የበግ : ለምድ : ለብሰው : የሚመጡባችሁ :: በውሥጣቸው : ግን : የሚነጥቁ : ተኵሎች : ናቸው :: ከፍሬያቸው : ታውቋቸዋላችሁ :: ከሾክ : ወይን : ደለቀማልን : ከአሜከላስ : በለስን :: እንደሁም : መልካም : ዛፍ : ሁሉ : መልካም : ፍሬን : ታፈራለች :: ክፉ : ዛፍም : ክፉ : ፍሬን : ታፈራለች :: መልካም : ዛፍ : ክፉ : ፍሬን : ማፍራት : አይቻላትም :: ክፉ : ዛፍም : መልካም : ፍሬን : ማፍራት : አይቻላትም :: መልካም : ፍሬንም : የማታፈራ : ዛፍ : ሁሉ : ትቈረጣለች : ወደሳትም : ትጨመ

ራለች ::እንግዲህም ፡ከፍሬያቸው ፡ ታውቋቸዋላችሁ :: አቤቱ ፡ አቤቱ ፡ የሚለኝ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የሚገባ ፡ አይደለም :: በሰማይ ፡ ያለውን ፡ ያባቴን ፡ ፈቃድ ፡ የሚያደርግ ፡ እንጂ ::

## ዘጠኛኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ::

### ጸሎት ::

አቤቱ ፡ እንለምንሃለን ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ ወትሮ ፡ ለማሰብና ፡ ለመስራት ፡ በጎ ፡ መንፈስን ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ እኛ ፡ ያላንተ ፡ አንዳችን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ ለማድረግ ፡ የማንችል ፡ እንደ ፡ ፈቃድህ ፡ለመኖር ፡ ባንተ ፡ ኃይልን ፡ እናገኝ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፲፡ ፩፡—፲፫፡፡

እኔም ፡ እወዳለሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ አባቶቻችን ፡ ሁሉ ፡ ከደመና ፡ በታች ፡ እንደ ፡ ነበሩ :: ሁሉም ፡ ባሕርን ፡ ተሻገሩ :: ሁሉም ፡ ለሙሴ ፡ ተጠመቁ ፡ በደመናና ፡ በባሕር ::ያንንም ፡ አንድ ፡ መንፈሳዊ ፡ መብል ፡ ሁላቸው ፡ በሉ :: ያንንም ፡ አንድ ፡ መንፈሳዊ ፡ መጠጥ ፡ ሁላቸው ፡ ጠጡ :: ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ይከተል ፡ ከነበረው ፡ ከመንፈሳዊ ፡ ደንጊያ ፡ ጠጥተዋልና :: ያም ፡ ደንጊያ ፡ ክርስቶስ ፡ ነበረ :: እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከርሳቸው ፡ በሚበዙት ፡ ደስ ፡ አላለውም :: በምድረ ፡ በዳ ፡ ወድቀዋልና :: ይኽም ፡ ለኛ ፡ ምሳሌ ፡ ሆነልን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደንወድ ፡ ኢሊያ ፡ እንደ ፡ ወደዱ :: ጣዖትም ፡ የምታመልኩ ፡ አትሁኑ ፡ ከርሳቸው ፡ ተከፍለው ፡ እንደመለኩ :: እንደ ፡ ተጻፈ :: ሕዝብ ፡ ሊበሉ ፡ ሊጠጡም ፡ ተቀመጡ :: ሊዘፍኑም ፡ ተነሡ :: ዝሙትንም ፡ አናድርግ ፡ ከርሳቸው ፡ ተከፍለው ፡ እንደደረጉ :: ከርሳቸውም ፡ ወደቁ ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ እልፍ ፡ ከሦስት ፡ ሽህ :: ክርስቶስንም ፡ አንፈታተን ፡ ከርሳቸው ፡ ተከፍለው ፡ እንደ ፡ ተፈታተኑት :: በእርዌም ፡ ጠፉ :: አታንጐርጕሩም ፡ ከርሳቸው ፡ ተከፍለው ፡ እንደንጐረጐሩ :: አጥፊውም ፡ አ



ጠፋቸው :: ይኽም ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ፡ ሁኖ ፡ በለዚያ ፡ ደረሰ :: ለኛም ፡ ተጻፈልን ፡ እኛን ፡ የዘመኑ ፡ ፍጻሜ ፡ የደረሰብነን ፡ ሊገሥጽን :: ስለዚኽም ፡ ቁሚያለሁ ፡ ብሎ ፡ የሚመስለው ፡ ይጠንቀቅ ፡ እንዳይወድቅ :: ሌላ ፡ መከራ ፡ አላገኛችሁም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ እንጂ :: እግዚአብሐርም ፡ እውነተኛ ፡ ነው ፡ በማትችሉትም ፡ ትፈተኑ ፡ ዘንድ ፡ አይተዋችሁም :: ነገር ፡ ግን ፡ ከመከራችሁ ፡ ጋራ ፡ መውጫውንም ፡ ያደርግላችኋል ፡ ታገሡ ፡ ዘንድ ፡ እንድችሉ ::

### የወንጌል ፡ ክፍል :: ሉቃስ ፡ ፲፮፡ ፩፡—፱፡፡

ደግሞም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ አለ :: አንድ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፡ መጋቢ ፡ የነበረለት :: ይኽም ፡ ወደርሱ ፡ ተሰማበት ፡ ከብቱን ፡ እንዲበትን :: ጸራውም ፡ አለውም :: ይኽ ፡ ባንተ ፡ የምሰማው ፡ ምንድር ፡ ነው :: የመጋቢነትኽን ፡ ቍጥር ፡ ስጠኝ :: እንግዲህ ፡ መጋቢ ፡ ትሆነኝ ፡ ዘንድ ፡ አትችልምና :: መጋቢውም ፡ በልቡ ፡ እንዲህ ፡ አለ :: ምን ፡ ላድርግ :: ጌታዬ ፡ መጋቢነትን ፡ ከኔ ፡ ይወስዷልና :: መቈፈርን ፡ አልችልም ፡ ከመለመንም ፡ አፍራለሁ :: መጋቢነት ፡ ከኔ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ይቀበሉኝ ፡ ዘንድ ፡ የማደርገውን ፡ አውቃላሁ :: የጌታውንም ፡ ባለዳች ፡ ኢያንዳንዳቸውን ፡ ጸራ :: ፊተኛውንም ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ አለብኽ ፡ ለጌታዬ ፡ አለው :: እርሱም ፡ መቶ ፡ ማድጋ ፡ ዘይት ፡ አለው :: እርሱም ::ደብዳቤኽን ፡ እንካ ፡ ቶሎም ፡ ተቀመጥ ፡ አምሳ ፡ ብለኽም ፡ ጻፍ ፡ አለው :: ደግሞ ፡ ሌላውንም ፡ አለ :: አንተስ ፡ ስንት ፡ አለብኽ :: እርሱም ፡ አለ :: መቶ ፡ መስፈርያ ፡ ስንዴ :: አለውም ፡ ደብዳቤክን ፡ እንካ ፡ ስማንያም ፡ ጻፍ :: ጌታም ፡ የግፍ ፡ መጋቢውን ፡ አመሰገነ ፡ በብልሐት ፡ አድርጓልና :: የዚኽ ፡ ዓለም ፡ ልጆች ፡ ለትውልዳቸው ፡ ብልሐተኞች ፡ ናቸውና ፡ ከብርሃን ፡ ልጆች ፡ ይልቅ :: እኔም ፡ እላችኋለሁ :: ለላንትም ፡ ወዳጆች ፡ አድርጉላችሁ ፡ ከግፍ ፡ ከብት :: ሲጐድልባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ድንኳኖች ፡ ይቀበልዋችሁ ፡ ዘንድ ::

x

## አሥረኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

የምህረት ፡ ጆሮህ ፡ አቤቱ ፡ ለተዋረድን ፡ ባሮችህ ፡ ጸሎት ፡ የተከፈተች ፡ ትሁን ፡ ልመናችንንም ፡ እናገኝ ፡ ዘንድ ፡ የምትወደውን ፡ ነገር ፡ አስጠይቅን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፲፪፡ ፩፡—፲፩፡፡

ስለ ፡ መንፈሳዊት ፡ ስጥወታ ፡ ግን ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ አወደለሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ። አሕዛብ ፡ እንደ ፡ ነበራችሁ ፡ ታውቃላችሁና ፡ ድምፅ ፡ ወደ ፡ ሌላቸው ፡ ጣዖታት ፡ የሔዳችሁ ፡ እንደ ፡ ተነዳችሁ ። ስለዚኽም ፡ አስታውቃችኋለሁ ፡ ማንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ የሚናገር ፡ የሱስን ፡ ውጉዝ ፡ እንደይለው ። የሱስንም ፡ ጌታ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ የሚቻለው ፡ የለም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንጂ ። ለስጥወታ ፡ ግን ፡ ልዩነት ፡ አለች ። ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ አንድ ፡ ነው ። ለማገልገልም ፡ ልዩነት ፡ አለች ። ጌታው ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ አንድ ፡ ነው ። ለኀይልም ፡ ልዩነት ፡ አለች ። ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ በሁሉ ፡ የሚያደርግ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንድ ፡ ነው ። ለኢያንዳንዱ ፡ ግን ፡ የመንፈስ ፡ መገለጽ ፡ ለጥቃሚ ፡ ተሰጠው ። ላንዱም ፡ በመንፈስ ፡ የጥበብ ፡ ነገር ፡ ይሰጠዋል ። ለሌላውም ፡ የውቀት ፡ ነገር ፡ እንደዚያው ፡ መንፈስ ። ለሌላውም ፡ ሃይማኖት ፡ ይሰጠዋል ፡ በዚያ ፡ መንፈስ ። ለሌላውም ፡ የመፈወስ ፡ ስጥወታ ፡ በዚያው ፡ መንፈስ ። ለሌላውም ፡ ተአምራት ፡ ለማድረግ ፡ ኀይል ፡ ተሰጠቸው ። ለሌላውም ፡ ትንቢት ፡ ተሰጠች ። ለሌላውም ፡ መናፍስትን ፡ መለየት ። ለሌላውም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቋንቋ ። ለሌላውም ፡ ቋንቋውን ፡ መተርጐም ። ይህንንም ፡ ሁሉ ፡ ያ ፡ አንድ ፡ መንፈስ ፡ ይሰራል ፡ ለሁሉም ፡ ለያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ይከፍለዋል ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፱፡ ፵፩፡—፵፯፡፡

በቀረበም ፡ ጊዜ ፡ አገሪቱንም ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አለቀሰላት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። አንቺ ፡ ብታውቂስ ፡ በዚኽ ፡ በቀንሽ ፡ ለሰላምሽ ፡ ያለውን ፡ ነገር ። አሁን ፡ ግን ፡ ካይንሽ ፡ ተሠውርዋል ። ጸላቶችሽ ፡ ቅጥር ፡ ቀጥረው ፡ የሚዞሩሽ ፡ ቀን ፡ ይመጣብሻልና ። ይከቡሻልም ። በዚኽና ፡ በዚኽም ፡ ያስጨንቁሻል ። ይገለብጡሻልም ፡ ልጆችሽንም ፡ በውሥጥሽም ፡ ያሉትን ። ደንጊያም ፡ በደንጊያ ፡ ላይ ፡ አይተውልሽም ። የተጐበኘሽበትን ፡ ዘመን ፡ አላወቅሽምና ። ወደ ፡ መቅደስም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የሚሸጡበትን ፡ የሚገዙበትንም ፡ ያወጣ ፡ ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ ሲላቸው ። የተጻፈ ፡ ነው ፡ ቤቴ ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ነው ፡ ብሎ ። እላንተ ፡ ግን ፡ የሌቦችን ፡ ዋሻ ፡ አደረጋችሁት ። ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመቅደስ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ።



## አሥራ ፡ አንደኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥለሴ ፡ በኋላ ።

### ጸሎት ።

አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ያልተወሰነቸውን ፡ ኀይልህን ፡ ከሌላ ፡ ይልቅ ፡ ምህረትንና ፡ ርኅራኄን ፡ በማድረግ ፡ ትገልጻለህና ። እንዲህ ፡ ያለውን ፡ የጸጋህን ፡ ልክ ፡ ስጠን ፡ እኛ ፡ የትእዛዛትህን ፡ መንገድ ፡ ሩጠን ፡ የምህረትህን ፡ ተስፋ ፡ እንድናገኝ ፡ የሰማዩንም ፡ መዝገብህን ፡ እንድንካፈል ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፲፭፡ ፩፡—፲፩፡፡

አስታውቃችሁማለሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ያስተማርኋችሁትን ፡ ወንጌል ። የተቀበላችሁትም ፡ የቆማችሁበትም ። በርሱም ፡ የምትድኑ ። ያወራሁላችሁትን ፡ የምስራች ፡ ምን ፡ ሆነ ፡ ታስቡት ፡ እንደ ፡ ሆን ። በከንቱ ፡ ያመናችሁ ፡ ባትሆኑ ። አስቀድሜ ፡ ሰጥቻችኋለሁና ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ የተቀበልሁትን ። ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ኀጢአታችን ፡ ሙትዋልና ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ። ተቀብሮማልና ። በሶስተኛም ፡ ቀን ፡ ተነሥትዋልና ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ። ለጴጥሮስም ፡ ታይቶታልና ። በኋላም ፡ ለሥራ ፡ ሁለቱ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ካምስት ፡ መቶ ፡ ለሚበዙ ፡ ወንድሞች ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ታየ ። ከርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ እስ

ክ : ዛሬ : ድረስ : ያሉ :: ከርሳቸውም : ደግሞ : የተኙ : ሰዎች : አሉ :: ከዚያም : በኋላ : ለያዕቆብ : ታየ :: በኋላም : ለሐዋርያት : ሁሉ :: ከሁላቸውም : በኋላ : ለኔ : ደግሞ : ታየ : ለኔ : ጭንጋፍ : ለምመስል :: እኔ : ከሐዋርያት : አንሳለሁና :: ሐዋርያ : አባል : ዘንድ : የማይገባኝ : የእግዚአብሔርን : ቤተ : ክርስቲያን : ስላሳደድሁ :: በእግዚአብሔር : ጸጋ : ግን : የሆንሁት : ነኝ :: የሆነችልኝም : ጸጋ : ከንቱ : አልሆነችም :: ነገር : ግን : ከሁላቸው : ይልቅ : እኔ : ደከምሁ :: እኔ : ግን : አይደለሁም :: ከኔ : ጋራ : ያለችው : የእግዚአብሔር : ጸጋ : እንጂ :: እኔም : ብሆን : እርሳቸውም : ቢሆኑ :: እንደሁ : እንሰብካለን : እንዲሁም : አመናችሁ ::

የወንጌል : ክፍል :: ሉቃስ : ፲፰፡ ፱—፲፬፡፡

ይህነንም : ምሳሌ : አለ : ሰውነታቸውን : ጻድቃን : እንደ : ሆኑ : ያመኑትን : ሌሎችንም : የናቁትን : ሰዎች :: ሁለት : ሰዎች : ሊጸልዩ : ወደ : ቤተ : መቅደስ : ወጡ : አንዱ : ፈሪሳዊ : ሁለተኛውም : ቀራጭ :: ፈሪሳዊም : ቁሞ : ይህነን : ሲል : በልቡ : ጸለየ :: አቤቱ : አመሰግንሃለሁ : እንደ : ሌሎች : ሰዎች : አይደለሁምና :: እንደ : ቀማኞች :: እንደ : ግፈኞችም :: እንደ : አመንዝሮችም :: እንደዚኽም : ቀራጭ :: በየሳምንቱ : ሁለት : ግዜ : እጾማለሁ :: ከብቴን : ሁሉ : አሥራት : አወጣለሁ :: ቀራጩ : ግን : ከሩቅ : ቁሞ : ነበር : ወደ : ሰማይም : ዓይኑን : ስንኳ : ሊያነሣ : አይሻም : ነበር :: ደረቱን : መታ : እንጂ : እንዲህ : ሲል :: አቤቱ : ይቅር : በለኝ : እኔን : ኃጢአተኛውን :: እላችኋለሁ : ይኽ : ወደ : ቤቱ : ጸድቆ : ወረደ : ከዚያ : ይልቅ :: ነፍሱን : ከፍ : ከፍ : የሚያደርግ : ሁሉ : ይዋረዳልና :: ነፍሱንም : ዝቅ : ዝቅ : የሚያደርግ : ከፍ : ይላል ::



አሥሬ : ሁለተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ : ሆይ :: አንተ : ወትሮ : ለመስማት : ተዘጋጅተሃልና : እኛ : ለመጸለይ : ከተዘጋጀነ : ይልቅ : እኛም : ከምንሻው : ከሚገባነም : ይልቅ : አንተ : ትሰጥ : ዘንድ : ለምደሃልና :: የምህረትህን : ምላት : በላያችን : አፍስስ : ልባችንም : የሚፈራውን : ነገር : ይቅር : በለና : በጎ : ነገርንም : ስጠነ : እኛ : እንለምን : ዘንድ : የማይገባነውን : በየሱስ : ክርስቶስ : በልጅህ : በጌታችን : ምግባር : እንጂ :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ፪፡ ቆሮንቶስ : ፫፡ ፬—፲፰፡፡

እንዲህም : ያለውን : ማመን : አለን : በክርስቶስ : ወደ : እግዚአብሔር : አንደችን : ከራሳችን : እንደ : በግዛጃችን : እናስብ : ዘንድ : የምንችል : አይደለነም :: ኃይላችን : ከእግዚአብሔር : ነው : እንጂ :: ላዲስ : ኪዳን : እናገለግል : ዘንድ : ያስቻለነ :: በፊደልም : ላለች : አይደለም : በመንፈስ : ላለች : እንጂ :: ፊደል : ይገላልና : መንፈስ : ግን : ሕያው : ያደርጋል :: የሞትም : መልእክት : በፊደላት : በደንጊያ : የተቀረጸች : የተመሰገነች : ከሆነች :: የእሥራኤል : ልጆች : የሙሴን : ፊት : ማየት : እስኪሳናቸው : ድረስ : ስለዚያ : ስላለፈው : ስለ : ፊቱ : ብርሃን :: እንደ : ምን : የመንፈስ : መልእክት : ከርስዋ : በብርሃንና : በምስጋና : አትበልጥምን :: ለኵነኔ : መልእክት : ክብር : ከሆነች :: እንዴት : እጅግ : የጽድቅ : መልእክት : በክብር : ትመላለች ::

የወንጌል : ክፍል :: ማርቆስ : ፯፡ ፴፩—፴፯፡፡

ደግሞም : ከጢሮስና : ከሲደና : ደርቻ : ወጣ :: ወደ : ገሊላም : ባሕር : መጣ : ባሥሩ : አገር : ደርቻ : ማኽል :: ደንቆሮም : ድዳም : ይዘው : ወደርሱ : መጡ :: እጁንም : ይጭንበት : ዘንድ : ለመኑት :: ከሰዎችም : ለይቶ : ብቻውን : ወሰደው :: ጻቱንም : በጆሮው : አገባለት :: ተፋቶም : መ

ላሱን ፡ ደሰሰ ፡፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡ አየ ፡ ተጻረም ፡ አለው
ም ፡፡ ኤፈታ ፡ እርሱም ፡ ተከፈት ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ የዚያን ፡
ጊዜም ፡ መስሚያው ፡ ተከፈተ ፡ የመላሱም ፡ እሥራት ፡ ተ
ፈታ ፡ ጸፍ ፡ አድርጎም ፡ ተናገረ ፡፡ ለማንምም ፡ እንዳይናገ
ሩት ፡ አዘዛቸው ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ ባዘዛቸው ፡ መጠን ፡
እጅግ ፡ በብዙ ፡ ያወሩት ፡ ነበሩ ፡፡ እጅግም ፡ ያደንቁ ፡ ነበ
ሩ ፡ እንዲህ ፡ ኢያሉ ፡፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ መልካም ፡ አደረገ ፡፡
ደናቁርት ፡ እንዲሰሙ ፡ ድዳችም ፡ እንዲናገሩ ፡ ያደርጋል ፡፡

አሥራ ፡ ሶስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሠላሴ ፡ በኋላ ፡፡

ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የታመኑ ፡
ሕዝብህ ፡ አይነተኛውንና ፡ የሚመሰገነውን ፡ መገዛት ፡ እን
ዲገዙልህ ፡ ያንተ ፡ ስጥወታ ፡ ብቻ ፡ ነውና ፡፡ እኛ ፡ በመጨ
ረሻ ፡ የሰማዩን ፡ ተስፋህ ፡ ሳናገኝ ፡ እንዳንቀር ፡ በዚች ፡ ሕ
ይወት ፡ ታምነን ፡ እንገዙልህ ፡ ዘንድ ፡ ጸጋ ፡ ስጠን ፡ በየሱስ ፡
ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ምግባር ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ገላትያን ፡ ፫፤ ፲፮፤—፳፪፡፡

ለአብርሃም ፡ ግን ፡ ለዘሩም ፡ ተስፋ ፡ ተደረገች ፡፡ ለዘሮች
ም ፡ አይልም ፡ ለብዙ ፡ እንደባል ፡፡ ላንድ ፡ እንዲባል ፡ አን
ድ ፡ ለዘርኽ ፡ እርሱም ፡ ክርስቶስ ፡፡ ይኽነንም ፡ እላለሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ ለክርስቶስ ፡ አስቀድሞ ፡ ያቆመቸውን ፡ ኪ
ዳን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ከሠላሳ ፡ አመት ፡ በኋላ ፡ የሆነች ፡ ሕ
ግ ፡ አታፈርሰውም ፡ ተስፋውን ፡ ታስቀረው ፡ ዘንድ ፡፡ መው
ረስም ፡ በኦሪት ፡ ከሆነ ፡ በተስፋ ፡ ባይሆን ፡ ነበር ፡፡ ለአብር
ሃም ፡ ግን ፡ በተስፋ ፡ ሰጥቶታል ፡ እግዚአብሔር ፡፡ ኦሪት ፡
እንጊዴህ ፡ ለምንድር ፡ ናት ፡፡ ኦሪትስ ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ ተሰ
ራች ፡፡ ተስፋ ፡ ያለው ፡ ዘር ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡፡ ከመላ
እክት ፡ ጋራም ፡ ተሰራች ፡ በመካከለኛው ፡ እጅ ፡፡ መካከ
ለኛውም ፡ ላንድ ፡ አይደለም ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አን
ድ ፡ ነው ፡፡ እንጊዴህ ፡ ኦሪት ፡ የእግዚአብሔርንን ፡ ተስፋ ፡



ትጻላለች ፡፡ አይሁን ፡፡ ሕይወትን ፡ መስጠት ፡ የሚቻላት ፡
ኦሪት ፡ ከተሰጠች ፡ ጽድቅ ፡ በውነት ፡ በኦሪት ፡ ትሆን ፡ ዘን
ድ ፡ ነበረች ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ መጽሐፍ ፡ ሁሉን ፡ ከኃጢአት ፡ በታ
ች ፡ ዘጋው ፡፡ ተስፋ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሃይማኖት ፡ ለሚ
ያምኑ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ሉቃስ ፡ ፲፤ ፳፫፤—፴፯፡፡

ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ተመለሰ ፡ ለብቻቸውም ፡ አ
ለ ፡፡ እላንት ፡ ያያችሁትን ፡ የምታይ ፡ ዓይን ፡ የተመሰገነች ፡
ናት ፡፡ እላችኋለሁና ፡ ብዙ ፡ ነቢያት ፡ ነገሥታትም ፡ እላን
ት ፡ የምታዩትን ፡ ሊያዩ ፡ ወደዱ ፡ አላዩምም ፡፡ እላንት ፡ የ
ምትሰሙትንም ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ወደዱ ፡ አልሰሙትም
ም ፡፡ እነሆም ፡ የኦሪት ፡ ሰው ፡ ሊፈትነው ፡ ተነሣ ፡ እንዲህ
ም ፡ አለው ፡፡ መምህር ፡ ሆይ ፡ ምን ፡ ላድርግ ፡ የዘላለም
ን ፡ ሕይወት ፡ እወርስ ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱም ፡ አለው ፡፡ በሕግ ፡
የተጻፈ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡፡ እንዴትስ ፡ ታነባለኽ ፡፡ እርሱም ፡
መለሰ ፡ አለም ፡፡ እግዚአብሔርን ፡ አምላክኽን ፡ ውደድ ፡
በኃይልህ ፡ ሁሉ ፡፡ ባሳብህም ፡ ሁሉ ፡፡ ባልንጀራኽንም ፡ እ
ንደ ፡ ነፍስኽ ፡፡ አለውም ፡ በውነት ፡ መለስኽ ፡፡ ይህነን ፡ አ
ድርግ ፡ ትድንማለኽ ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ሰውነቱን ፡ ጻድቅ ፡ ያ
ደርግ ፡ ዘንድ ፡ ወደደ ፡ የሱስንም ፡ አለው ፡፡ ባልንጀራዬስ ፡
ማነው ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከየሩ
ሳሌም ፡ ወደ ፡ ኢያሪኮ ፡ ወረደ ፡፡ በወንበዴችም ፡ ማኸል ፡
ወደቀ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ገፈፏት ፡ አቍሰሉትም ፡፡ ሔዱ
ም ፡ በሕይወትና ፡ በሞትም ፡ ማኸል ፡ ተውት ፡፡ አንድ ፡ ካ
ህንም ፡ እንዲያው ፡ በዚያች ፡ መንገድ ፡ ወረደ ፡፡ አ
ይቶትም ፡ አለፈ ፡፡ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የሌዊ ፡ ወገን ፡
ሰው ፡ ወደዚያ ፡ ስፍራ ፡ መጣ ፡፡ አይቶትም ፡ አለፈ ፡፡
አንድ ፡ ሳምራዊ ፡ መንገደኛ ፡ ግን ፡ አለፈበት ፡ ባየውም ፡
ጊዜ ፡ አዘነለት ፡፡ ወደርሱም ፡ ቀረበ ፡ ቍስሉንም ፡ አጋጠ
መለት ፡ ዘይትና ፡ ጸጅም ፡ አፈሰሰበት ፡፡ ባሕያውም ፡ ላይ ፡
አስቀመጠው ፡፡ ወደ ፡ መንገደኛ ፡ ቤትም ፡ ወሰደው ፡ የሚ

በጀውንም ፡ ነገር ፡ አየለት ፡፡ በነገውም ፡ ሲወጣ ፡ ሁለት ፡ ዲናርን ፡ አወጣ ፡ ለመንገደኛ ፡ ቤተ ፡ ባለቤትም ፡ ሰጠው ፡ አለውም ፡ አገልግለው ፡፡ ከዚህም ፡ በላይ ፡ የምትፈጅለት ፡ ስመለስ ፡ ጊዜ ፡ እሰጥኻለሁ ፡፡ ከለዚኽ ፡ ሦስትም ፡ ማናቸው ፡ ይመስልኻል ፡ በወንበዴች ፡ ማኽል ፡ ለወደቀው ፡ ባልንጀራ ፡ የሆነው ፡፡ እርሱም ፡ አለ ፡ ምሕረት ፡ ያደረገለት ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡፡ ሒድ ፡ አንተም ፡ እንደዩህ ፡ አድርግ ፡፡

---

## አሥራ ፡ አራተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ሃይማኖትን ፡ አለኝታውንም ፡ ፍቅርንም ፡ አብዛልን ፡ ተስፋህንም ፡ እናገኝ ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዝህን ፡ አስውደድን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ገላትያን ፡ ፭፡ ፲፮፡—፳፮፡፡

እላለሁም ፡፡ በመንፈስ ፡ ተመላለሱ ፡ የሥጋንም ፡ መመኘት ፡ አትፈጽሙም ፡፡ ሥጋ ፡ መንፈስ ፡ የሚጻላውን ፡ ይወደልና ፡፡ መንፈስም ፡ ሥጋ ፡ የሚጻላውን ፡፡ እሌህም ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ይጻላሉ ፡፡ እላንተ ፡ የምትወድዋትን ፡ ነገር ፡ እንደታደርጊት ፡፡ በመንፈስ ፡ ግን ፡ ብትሔዱ ፡ ከኦሪት ፡ በታች ፡ አይደላችሁም ፡፡ የሥጋም ፡ ስራ ፡ የተገለጠች ፡ ናት ፡፡ እርስዋም ፡ ምንዝር ፡፡ ዝሙትም ፡፡ ርኵሰትም ፡፡ አለማፈርም ፡፡ ጣዖትንም ፡ ማምለክ ፡፡ መሠሪነትም ፡፡ ጠላትነትም ፡፡ ጸብም ፡፡ መቅናትም ፡፡ መቈጣትም ፡፡ መከራከርም ፡፡ ሁከትም ፡፡ መለያየትም ፡፡ ቅናተኝነትም ፡፡ መግደልም ፡፡ ስካርም ፡፡ መሶልሶልም ፡፡ ይህነንም ፡ ሁሉ ፡ የሚመስል ፡፡ አስቀድሜም ፡ እንደልኋችሁ ፡ እንዲሁም ፡ አሁን ፡ እላለሁ ፡፡ እንደዚች ፡ ያለችውን ፡ የሚያደርጉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ አይወርሱም ፡፡ የመንፈስ ፡ ፍሬ ፡ ግን ፡ ፍቅር ፡ ናት ፡፡ ደስታም ፡፡ ሰላምም ፡፡ ትዕግሥትም ፡፡ ቸርነትም ፡፡ በጐነትም ፡፡ ሃይማኖትም ፡፡ ገርነትም ፡፡ መሻትንም ፡ መግዛት ፡፡ በዚች ፡ ተይዘው ፡ በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ሕግ ፡ የለባቸውም ፡፡ የክርስቶስ ፡ ወገኖችም ፡ ሥጋቸውን ፡ ፈጽመው ፡ ሰቀሉ ፡ ከሕማማትና ፡ ከመመኘት ፡ ጋራ ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ሉቃስ ፡ ፲፯፡ ፲፩፡—፲፱፡፡

ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ሲሔድ ፡ በሰማርያና ፡ በገሊላ ፡ መኻከል ፡ አለፈ ፡፡ እርሱም ፡ ወደንደ ፡ ት ፡ መንደር ፡ ሲገባ ፡ ተቀበሉት ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ ለምጻሞች ፡ ከሩቅ ፡ የቆሙ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ድምፃቸውን ፡ አሰሙ ፡ እንደዩህ ፡ ሲሉ ፡፡ የሱስ ፡ ሆይ ፡ መምህሩ ፡ ማረን ፡፡ አየም ፡ አላቸውም ፡፡ ሒዱ ፡ ራሳችሁንም ፡ ለካህናት ፡ አስዩ ፡፡ እርሳቸውም ፡ ሲሔዱ ፡ ነጹ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አንዱ ፡ እንደ ፡ ተፈወሰ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ኢያመሰገነ ፡ ተመለሰ ፡፡ በግምባሩም ፡ ወደግሩ ፡ ወደቀ ፡ እርሱን ፡ ኢያመሰገነ ፡፡ እርሱም ፡ ሳምራዊ ፡ ነበር ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለመ ፡፡ የነጹ ፡ አሥር ፡ አይደሉምን ፡፡ ዘጠኙም ፡ የታሉ ፡፡ አልተገኙም ፡ ሊመለሱ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ምስጋና ፡ ሊሰጡ ፡ ከዚኽ ፡ ከልዩ ፡ ወገን ፡ በቀር ፡፡ አለውም ፡፡ ተነሣ ፡ ሒድም ፡፡ ሃይማኖትኽ ፡ አዳነኽ ፡፡

---

## አሥራ ፡ አምስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ቤተ ፡ ክርስቲያንህን ፡ አቤቱ ፡ በዘላለም ፡ ምህረትህ ፡ ጠብቃት ፡ እንለምንሃለን ፡፡ የሰው ፡ ድካምም ፡ ያላንተ ፡ ሳይወድቅ ፡ አይቀርምና ፡ ወትሮ ፡ በረዲትህ ፡ ከሚጐዳን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ጠብቀን ፡ ለመድኃኒታችንም ፡ ወደሚጠቅመን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አድርሰን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ገላትያን ፡ ፮፡ ፲፩፡—፲፰፡፡

እዩ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ መጻፍ ፡ በጄ ፡ ጻፍሁላችሁ ፡፡ በሥጋ ፡ ይመኩ ፡ ዘንድ ፡ የሚወዱ ፡ ሰዎች ፡ እርሳቸው ፡ የግድ ፡

ትገዘረ ፡ ዘንድ ፡ ይልዋችኋል ፡ ለሌላ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ መስቀል ፡ እንዳይሰደዱ ፡ ነው ፡ እንጂ ። እርሳቸውም ፡ የሚገዘረ ፡ እንኳ ፡ ኦሪትን ፡ አይጠብቁም ። ነገር ፡ ግን ፡ በሥጋችሁ ፡ ይመኩ ፡ ዘንድ ፡ ብለው ፡ ትገዘረ ፡ ዘንድ ፡ ይሹዋችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ አልመካም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መስቀል ፡ እንጂ ። በርሱ ፡ ዓለሙ ፡ ተሰቅሎልኛልና ፡ እኔም ፡ ለዓለም ። በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ ዘንድ ፡ ግዝረት ፡ አንዳች ፡ አትጠቅምምና ፡ ቍላፍነትም ። አዲስ ፡ ፍጥረት ፡ እንጂ ። በዚች ፡ ቃኖናም ፡ በሚሔዱ ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ፡ ምሕረትም ። በእግዚአብሔር ፡ እሥራኤል ፡ ላይም ። ከዚኽም ፡ በኋላ ፡ ማንም ፡ አያስታክተኝ ። የጌታን ፡ የየሱስን ፡ ምልክት ፡ በሥጋዬ ፡ ተሸክሚያለሁና ። የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ ከመንፈሳችሁ ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ። አሜን ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፮፥ ፳፬—፴፬።

ማንም ፡ ለሁለት ፡ ጌቶች ፡ መገዛት ፡ አይቻለውም ። አንደኜን ፡ ጸልቶ ፡ አንደኜን ፡ ካልወደደ ፡ ወደንድም ፡ ጠግቶ ፡ ሁለተኛውን ፡ ካልናቀ ። ለእግዚአብሔርና ፡ ለከብት ፡ ትገዙ ፡ ዘንድ ፡ አትችሉም ። ስለዚኽ ፡ እላችኋለሁ ። ለነፍሳችሁ ፡ አትተክዙ ፡ በምትበሉት ፡ በምጠጡትም ፡ ለሥጋችሁም ፡ በምትለብሱት ። ነፍስ ፡ ከመብል ፡ የምትበልጥ ፡ አይደለችምን ፡ ሥጋም ፡ ከልብስ ። ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዖፎች ፡ ተመልከቱ ። እርሳቸው ፡ አይዘሩምና ፡ አያጭዱምና ፡ በጎታም ፡ አይከቱምና ። የሰማዩም ፡ አባታችሁ ፡ ደግሞ ፡ ይመግባቸዋል ። እላንትም ፡ ከርሳቸው ፡ እጅግ ፡ አትሻሉዋቸውምን ። ማነው ፡ ከላንት ፡ አስቦ ፡ በቁመቱ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ መጨመር ፡ የሚችል ። ለምንስ ፡ በልብስ ፡ ትተክዛላችሁ ። የምድረ ፡ በደን ፡ አበቦች ፡ አስቡ ፡ እንዲያድጉ ። አይደክሙም ፡ አይፈትሉምም ። እላችሁማለሁ ፡ ሰሎሞን ፡ እንኳ ፡ በክብሩ ፡ ሁሉ ፡ ከርስዋ ፡ እንደንዲቱ ፡ አለበሰም ። የምድረ ፡ በደም ፡ ሣዕር ፡ ዛሬ ፡ የሚገኝ ፡ ነገም ፡ ወደ ፡ እቶ



ን ፡ የሚጣል ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡ የሚያለብሰው ፡ ከሆነ ። እላንትንን ፡ እጅግ ፡ አብዝቶ ፡ አያለብሳችሁም ፡ እላንት ፡ ሃይማኖት ፡ የጐደላችሁ ። አትተክዙ ፡ እንጊዲህ ፡ አትሉም ። ምን ፡ እንበላለን ፡ ምንስ ፡ እንጠጣለን ፡ ምንስ ፡ እንለብሳለን ። ይህን ፡ ሁሉ ፡ አሕዛብ ፡ ይሹታልና ። የሰማዩ ፡ አባታችሁ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እንድትሹ ፡ ያውቃልና ። የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ጽድቁንም ፡ አስቀድማችሁ ፡ እሹ ፡ እንጂ ፡ ይኽም ፡ ሁሉ ፡ ይጨመርላችኋል ። ለነገም ፡ አታስቡ ። ነገ ፡ ለራሱ ፡ ያስባልና ። የቀኑስ ፡ ክፋቱ ፡ ይበቃዋል ።

አሥራ ፡ ስድስተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

ጸሎት ።

አቤቱ ፡ የማትጨረስ ፡ ርኅራኄህ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህን ፡ እንድታነጻ ፡ እንድትጠብቃትም ፡ እንለምንሃለን ፡ አንተም ፡ ሳታገዛትም ፡ በምነት ፡ መኖር ፡ አይቻላትምና ፡ በረዴትህና ፡ በቸርነትህ ፡ ወትሮ ፡ ጠብቃት ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፫፥ ፲፫—፳፩።

ስለዚኽም ፡ በላንት ፡ ምክንያት ፡ በምትደርስብኝ ፡ በመከራዬ ፡ እንዳትደክሙ ፡ እለምናለሁ ፡ ክብራችሁ ፡ ናትና ። ስለዚኽም ፡ በጕልበቴ ፡ እምበረከካለሁ ፡ ወደ ፡ ጌታችን ፡ ወደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አብ ። በርሱ ፡ ስም ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ያለች ፡ አባትነት ፡ ሁሉ ፡ የሚጸራ ። እንደ ፡ ክብሩ ፡ ባለጠግነት ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ። በመንፈሱ ፡ ኃይል ፡ ትበርቱ ፡ ዘንድ ፡ በውሥጡ ፡ ሰውነታችሁ ። ክርስቶስ ፡ በሃይማኖት ፡ በልባችሁ ፡ ያድርባችሁ ፡ ዘንድ ። ሥርንም ፡ መሠረትንም ፡ በፍቅር ፡ ቲዙ ፡ ዘንድ ። ትችሉ ፡ ዘንድ ፡ ለመድረስ ፡ ከቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ። ምንድር ፡ ነው ፡ ስፋቱ ፡ ርዝመቱም ፡ መጥለቁም ፡ ቁመቱም ። የክርስቶስንም ፡ ፍቅር ፡ ከመታወቅ ፡ የምትበልጠውን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ። ትፈጸ

ሙ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምሉ ፡ ፍጻሜ ። ለርሱም ፡
በላያችን ፡ በጸናች ፡ በኀይሉ ፡ ከምንለምነው ፡ ተስፋም ፡ ከ
ምናደርገው ፡ ሁሉ ፡ አብልጦ ፡ ሊያደርግልን ፡ ለሚችል ። ለ
ርሱ ፡ ምስጋና ፡ ይሁን ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ በየሱስ ፡ ክርስ
ቶስ ፡ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለሙም ። አሜን ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፯፡ ፲፩፡—፲፯።

በሚመጣውም ፡ ቀን ፡ ሆነ ፡ ወደንዲት ፡ አገር ፡ ስምዋ
ን ፡ ናይን ፡ የሚሏዋት ፡ እንደ ፡ ሔደ ። ክርሱ ፡ ጋራም ፡ ብ
ዙ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሔዱ ፡ እጅግ ፡ ሕዝብም ። ወደገ
ሩ ፡ ደጅም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ሙቶ ፡ የተሸከሙትን ፡
አገኘ ። ለናቱም ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ የነበረ ፡ ይህቺም ፡ ባልቴ
ት ፡ ነበረች ። ክርስዋ ፡ ጋራም ፡ እጅግ ፡ ሕዝብ ፡ ካገሩ ፡ ወገ
ን ፡ ነበረች ። ጌታም ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ አዘነላት ። አላትም ፡ አ
ታልቅሽ ። ደርሶም ፡ ቃሬዛውን ፡ ነካ ። ተሸካሚዎቹም ፡ ቆ
ሙ ። አለም ። አንተ ፡ ብላቴና ፡ ተነሣ ፡ እልኻለሁ ። የሞ
ተውም ፡ ተቀመጠ ፡ ይጫወትም ፡ ጀመረ ። ለናቱም ፡ አሳ
ልፎ ፡ ሰጣት ። ሁሉንም ፡ ፍርሃት ፡ ያዛቸው ፡ እግዚአብሔ
ርንም ፡ አመሰገኑ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ታላቅ ፡ ነቢይ ፡ በመኻ
ከላችን ፡ ተነሣ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቡን ፡ ጐበኘትዋ
ል ። ይኽም ፡ ነገር ፡ ስለርሱ ፡ ወጣ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ በዙር
ያውም ፡ ባለች ፡ አገር ፡ ሁሉ ።

አሥራ ፡ ሰባተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

ጸሎት ።

አቤቱ ፡ ጸጋህ ፡ ወትሮ ፡ እንድትቀድምንና ፡ እንድትከተ
ልን ፡ ወትሮም ፡ ለበጎ ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ እንድታዘነብልን ፡ እን
ለምንሃለን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፬፡ ፩፡—፯።

አሁንም ፡ እኔ ፡ የጌታ ፡ እሡር ፡ ለተጸራችሁባት ፡ መጸራታ
ችሁ ፡ እንደገባችሁ ፡ ትሔዱ ፡ ዘንድ ፡ እለምናችኋለሁ ። ብት



ሕትናና ፡ በገርነት ፡ ሁሉ ፡ ከትዕግሥት ፡ ጋራ ። እርሱ ፡
በርሳችሁ ፡ ስትቻቻሉ ፡ በፍቅር ። የመንፈስንም ፡ አንድነ
ት ፡ በሰላም ፡ ማሠርያ ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ስትጋደሉ ።
አንድ ፡ ሥጋ ፡ ነው ፡ አንድ ፡ መንፈስም ። ለመጸራታችሁ ፡
የተጸራችሁለት ፡ ተስፋ ፡ አንዲት ፡ እንደ ለች ። አንድ ፡ ጌ
ታም ፡ አንዲት ፡ ሃይማኖትም ፡ አንዲት ፡ ጥምቀትም ። አ
ንድ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የሁሉም ፡ አባት ። እርሱም ፡ ከ
ሁሉ ፡ በላይ ። በሁሉም ። በላንትም ፡ ሁሉ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፬፡ ፩፡—፲፩።

ወደንዱም ፡ ከፈሪሳውያን ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ በሰንበ
ት ፡ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ እርሳቸው ፡ ይጠባ
በቁት ፡ ነበር ። እነሆም ፡ የተኰደኰደ ፡ ሰው ፡ ሆዱ ፡ የተነፋ ፡
በፊቱ ፡ ነበረ ። የሱስም ፡ መለሰ ፡ ባለ ፡ ኦሪቶችንና ፡ ፈሪሳ
ውያንንም ፡ ተናገረ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። በሰንበት ፡ መፈወስ ፡
ይገባልን ። እርሳቸው ፡ ግን ፡ ዝም ፡ አሉ ። እርሱም ፡ ወሰ
ደው ፡ ፈወሰውም ፡ ሰደደውም ። መለሰላቸውም ፡ አለ
ም ። ማነው ፡ ከላንት ፡ አህያው ፡ ወይስ ፡ በሬው ፡ በጉድ
ጓድ ፡ ቢወድቅበት ፡ ቶሎ ፡ የማያነሣው ፡ በሰንበት ፡ ቀን ።
በዚኽም ፡ ይመልሱለት ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ። ምሳሌም ፡
ተናገረ ፡ ለተጸሩት ። የመቀመጫውን ፡ ላይኛውን ፡ ስፍራ ፡
እንደ መርጡ ፡ ያይ ፡ ነበረና ። አላቸውም ። ከማንም ፡ ወ
ደ ፡ ሰርግ ፡ በተጸራኽ ፡ ጊዜ ፡ በላይኛው ፡ መቀመጫ ፡ አትቀ
መጥ ። ምን ፡ አልባት ፡ ካንተ ፡ የሚበልጥ ፡ ሰው ፡ ተጸርቶ ፡
እንደ ፡ ሆን ። አንተንም ፡ እርሱንም ፡ የጸራ ፡ ይመጣል ፡ ይ
ልኻልም ። ለዚኽ ፡ ስፍራውን ፡ ተው ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡
ታፍር ፡ ትጀምራለኽ ፡ ታችኛውንም ፡ ስፍራ ፡ ትወስዳለኽ ።
ነገር ፡ ግን ፡ በተጸራኽ ፡ ጊዜ ፡ ሒድና ፡ በመጨረሻው ፡ ስፍ
ራ ፡ ተቀመጥ ። ያ ፡ የጸራኽ ፡ መጥቶ ። ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ወደ ፡
ላይ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ክብር ፡ ይ
ሆንልኻል ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ በተቀመጡት ፡ ፊት ። ራሱን ፡ ከ
ፍ ፡ ያደረገ ፡ ሁሉ ፡ ይዋረዳልና ። ራሱንም ፡ ያዋረደ ፡ ከፍ ፡
ይላል ።

## አሥራ ፡ ስምንተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

አቤቱ ፡ እንለምንሃለን ፡ ለሕዝብህ ፡ ጸጋህን ፡ ስጥ ፡ ያለ
ምን ፡ የሥጋውንም ፡ የድያብሎስንም ፡ ፈተና ፡ ይቃወሙ ፡
ዘንድ ፡ በንጹሕ ፡ ልብም ፡ አንተን ፡ ብቻህን ፡ አምላክ ፡ የ
ምትሆን ፡ ይከተሉህ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታ
ችን ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፩፡ ቆሮንቶስ ፡ ፩፡ ፬፡—፰፡፡

አምላኬን ፡ ሁልጊዜ ፡ ስለላንተ ፡ አመሰግናላሁ ፡ በክርስ
ቶስ ፡ የሱስ ፡ በተሰጣችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡፡ በሁሉ ፡
ባለ ፡ ጸጎች ፡ ሁናችኋልና ፡ በርሱ ፡፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ በውቀት
ም ፡ ሁሉ ፡፡ የክርስቶስ ፡ ምስክር ፡ በላንት ፡ እንደ ፡ ጸናች ፡፡
አልጐደለባችሁምና ፡ ስጥወታው ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡፡ የጌታችን
ንም ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ መገለጥ ፡ ደጅ ፡ ትጸናላችሁ ፡፡
እርሱም ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ያጸናችኋል ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ እን
ድትሆኑ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቀን ፡፡

### የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳፪፡ ፴፬፡—፵፮፡፡

ፈሪሳውያንም ፡ እርሱ ፡ የሰዱቃውያንን ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ዘ
ጋ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ወደርሱ ፡ ባንድ ፡ ተሰበሰቡ ፡፡ ከርሳቸ
ውም ፡ ወገን ፡ አንድ ፡ ኦሪታዊ ፡ ጠየቀው ፡ ሲፈትነው ፡ እን
ዲህም ፡ ሲለው ፡፡ መምህር ፡ ሆይ ፡፡ ከኦሪት ፡ ማናቸይቱ ፡
ትእዛዝ ፡ ትበልጣለች ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ አምላክኽን ፡ ትወድ ፡ ዘንድ ፡ በፍጹም ፡ ልብኽ ፡ በፍ
ጽምትም ፡ ነፍስኽ ፡ በፍጹምም ፡ አሳብኽ ፡፡ ይኽች ፡ መ
ጀመርያይቱ ፡ ትእዛዝ ፡ የምትበልጥም ፡ ናት ፡፡ ሁለተኛዪ
ቱም ፡ ትመስላታለች ፡፡ ባልንጀራኽን ፡ እንደ ፡ ነፍስኽ ፡ ት
ወድ ፡ ዘንድ ፡፡ በለዚኽ ፡ በሁለቱ ፡ ትእዛዛት ፡ ኦሪት ፡ ሁ
ሉ ፡ ነቢያትም ፡ ተሰቅለዋል ፡፡ ፈሪሳውያንም ፡ ተከማችተ
ው ፡ ሳሉ ፡ ጠየቃቸው ፡ የሱስ ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ፡፡ ስለ ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ምን ፡ ይመስላችኋል ፡፡ የማን ፡ ልጅ ፡ ነው ፡፡ አሉት ፡



የደዊት ፡ ልጅ ፡፡ እርሱም ፡ አላቸው ፡ ደዊት ፡ እንኪያ ፡ እ
ንዴት ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጌታ ፡ ይለዋል ፡፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡
ጌታ ፡ ጌታዬን ፡ አለው ፡፡ በቀኜ ፡ ተቀመጥ ፡ ጸላቶችኽን ፡ ከ
ግርኽ ፡ ጫማ ፡ በታች ፡ እስክጥል ፡ ድረስ ፡፡ ደዊት ፡ ጌታ ፡ ብ
ሎ ፡ ከጸራው ፡፡ እንዴት ፡ ልጁ ፡ ይሆናል ፡፡ ማንም ፡ በነገር ፡
ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ፡፡ ማንም ፡ ከቶ ፡ ከዚያ
ን ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ይጠይቀው ፡ ዘንድ ፡ አልደፈረም ፡፡

---

## አሥራ ፡ ዘጠነኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ፡፡

### ጸሎት ፡፡

አምላክ ፡ ሆይ ፡ ያላንተ ፡ ደስ ፡ እናሰኝህ ፡ ዘንድ ፡ ተስና
ናልና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ልባችነን ፡ እንደ
ገዛም ፡ እንዲያቀናም ፡ ምህረትህን ፡ ስጠኝ ፡ በየሱስ ፡ ክርስ
ቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

### የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ኤፌሶን ፡ ፬፡ ፲፯፡—፴፪፡፡

ይህነንም ፡ እላለሁ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ እመሰክራለ
ሁ ፡ እንደትሔዱ ፡ የቀረት ፡ አሕዛብ ፡ እንዲሔዱ ፡ በከን
ቱ ፡ ማሰባቸው ፡፡ በምክራቸው ፡ ተጨልመው ፡ ከእግዚአ
ብሔር ፡ ሕይወት ፡ የተለዩ ፡፡ እውቀት ፡ ስለ ፡ ሌለባቸው ፡
ስለ ፡ ልባቸውም ፡ ዕውርነት ፡፡ ኢሊያ ፡ ልባቸውም ፡ ደነዞ ፡
ራሳቸውን ፡ ለሴሰኝነት ፡ አሳልፈው ፡ የሰጡ ፡ ርኩሰትን ፡
ሁሉ ፡ በስስት ፡ ለማድረግ ፡፡ እላንተ ፡ ግን ፡ ክርስቶስን ፡ እ
ንዲህ ፡ አልተማራችሁትም ፡፡ በርሱ ፡ ሰምታችሁበት ፡ እንደ ፡
ሆናችሁ ፡ እውነቱንም ፡ በየሱስ ፡ እንደለች ፡ አውቃችሁ ፡ እ
ንደ ፡ ሆናችሁ ፡፡ እንደ ፡ ቀደመ ፡ አካሔድ ፡ ያለውን ፡ አሮጌ
ውንም ፡ ሰው ፡ በስሕተት ፡ ፈቃድ ፡ የጠፋውን ፡ ታወጡ ፡ ዘ
ንድ ፡፡ በሕሊናችሁም ፡ መንፈስ ፡ ታደሱ ፡ ዘንድ ፡፡ አዲስን
ም ፡ ሰው ፡ ትለብሱ ፡ ዘንድ ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ አምሳል ፡
በጽድቅ ፡ በውነትም ፡ ቅድስና ፡ የተፈጠረውን ፡፡ ስለዚኽ
ም ፡ አሰትን ፡ ሁሉ ፡ ከላንት ፡ አውልቃችሁ ፡፡ በውነት ፡ ተና
ገሩ ፡ ሁሉ ፡ ኢያንደንዱ ፡ ከባልንጀራው ፡ ጋራ ፡ እኛ ፡ እር

ሱ : በርሳችን : ብልቶች : ሁነናልና :: ተቈጡ : ኀጢአትም : አትስሩ :: በቍጣችሁ : ፀሐይ : አይግባባችሁ :: ለሰይጣንም : ስፍራውን : አትስጡ :: የሰረቀም : እንግዲህ : አይስረቅ :: በጁ : ይድከም : እንጂ : መልካምንም : ያድርግ : ለሚሻ : ለመስጠት : ያገኝ : ዘንድ :: የማይጠቅም : ነገር : ሁሉ : ካፋችሁ : አይውጣ :: መሻትን : ለመሥራት : መልካም : ያለ : እንጂ : ለሚሰሙት : ጸጋ : ታመጻ : ዘንድ :: የእግዚአብሔርንም : ቅዱስ : መንፈሱን : ለመድኀኒት : ቀን : የታተማችሁበትን : አታሳዝኑ :: የመረረ : ነገር : ሁሉ : መዓትም : ቍጣም : ጩኸትም : ስድብም : ከላንት : ይራቅ : ከክፋት : ሁሉ : ጋራ :: እርሱ : በርሳችሁም : ቸሮች : የምትራሩም : ሁኑ :: እርሱ : በርሳችሁም : ይቅር : በሉ :: እግዚብሔር : ደግሞ : እላንትን : በክርስቶስ : ይቅር : እንደለላችሁ ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፱፤ ፩፤—፰።

ወደ : ሳምቡቅም : በወፃ : ጊዜ : ወደ : ማደ : ተሻገረ :: ወደገሩም : መጣ :: እነሆም : መፃጉውን : አመጡለት : ባልጋ : ተኝቶ :: የሱስም : ሃይማኖታቸውን : ባየ : ጊዜ : መፃጉውን : አለው :: አይዞህ : ልጄ : ሆይ :: ኀጢአትኽ : ቀረችልኽ :: እነሆም : ከጻፎች : አያሌ : በልባቸው : ይኽ : ይሳደባል : አሉ :: የሱስም : አሳባቸውን : አወቀ : አለም :: ለምን : እላንት : በልባችሁ : ክፉ : ታስባላችሁ :: ማናቸው : ይጨንቅ : 'ኀጢአትኽ : ቀረችልኽ' : ማለት : ወይስ : 'ተነሣና : ሒድ' :: ነገር : ግን : ታውቁ : ዘንድ : ለሰው : ልጅ : ሥልጣን : እንደለው : ኀጢአት : ይቅር : ይል : ዘንድ : በምድር : ላይ :: (የዚያን : ጊዜ : መፃጉውን : አለው ::) ተነሣ : አልጋኽን : አንሣ : ወደ : ቤትኽም : ሒድ :: ተነሥቶም : ወደ : ቤቱ : ሔደ :: የተሰበሰቡትም : አይተው : አደነቁ : እግዚአብሔርንም : አመሰገኑ : እንደዚህ : ያለቸውን : ሥልጣን : ለሰው : ሰጥትዋልና ::



ህያ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ::

ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : በሁሉም : መሐሪ : እግዚአብሔር : ሆይ :: በቸር : በጐነትህ : ከሚጐዳን : ነገር : ሁሉ : ትጠብቀን : ዘንድ : እንለምንሃለን : እኛ : በሥጋና : በነፍስ : ተዘጋጅተን : አንተ : የምትወደውን : ነገር : በደስታ : እንፈጽም : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

የመልእክት : ክፍል :: ኤፌሶን : ፭፤ ፲፭፤—፳፩።

አሁንም : እዩ : እንዴት : ተጠንቅቃችሁ : እንድትመላለሱ :: እንደ : ሰነፎች : አይደለም :: እንደ : ጠቢባን : እንጂ :: ዘመኑን : የምትዋጁ : ሁኑ :: ይህች : ወራት : ክፉ : ወራት : ናትና :: ስለዚኽም : ሰነፎች : አትሁኑ :: እግዚአብሔር : የሚወደውን : አስተውሉ : እንጂ :: በጸጅም : አትስከሩ : ጥፋት : ያለበት :: መንፈስ : ይምላባችሁ : እንጂ :: እርሱ : በርሳችሁም : ተናጋገሩ : በመዝሙር : በምስጋናም :: በመንፈሳዊም : ዝማሬ :: ለእግዚአብሔር : ስትቀኙ : ስታዘምሩም : በልባችሁ :: ሁለግዜም : ስለ : ሁሉም : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን : ስም : ለእግዚአብሔርና : ለአብ : አመስግኑ :: እርሱ : በርሳችሁም : በእግዚአብሔር : ፍርሃት : ትገዙ ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፳፪፤ ፩፤—፲፬።

የሱስም : መለሰ : ደግሞም : በምሳሌ : ነገራቸው : እንደህ : ሲል :: መንግሥተ : ሰማያት : ንጉሥ : ሰውን : ትመስላለች : ለልጁ : ሰርግን : ያደረገውን :: ባሮችንም : ላከ : ወደ : ሰርጉ : የታደሙትን : ይጸሩ : ዘንድ :: ይመጹም : ዘንድ : እንቢን : አሉ :: ደግሞ : ሌሎች : ባሮችን : ላከ : እንዴህ : ሲል :: የታደሙትን : በልዋቸው :: እነሆ : ምሳዬን : አዘጋጀሁ : ላሞቼ : ገቾቼም : ታርደዋል : ሁሉም : ተዘጋጅትዋል :: ኑ : ወደ : ሰርግ :: እርሳቸውም : ቸል : ብለው : ሔዱ : አንዱ : ወደርሻው : አንዱም : ወደ : መሸጥና : መለወጡ :: የቀሩትም : ባሮቹን : ይዘው : አስነወርዋቸው : ገደልዋቸው

ም ። ንጉሡም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ተቈጣ ። ጭፍሮችንም ፡ ላክ ፡ ኢሊያንም ፡ ገደሎች ፡ አጠፋ ፡ አገራቸውንም ፡ አቃጠለ ። ከዚያ ፡ ወደ ፡ ያም ፡ ባሮቹን ፡ አለ ። ሰርጉስ ፡ ተዘጋጅቷል ። የተጸሩት ፡ ግን ፡ አይገባቸውም ፡ ነበሩ ። እንጊዲህ ፡ ወደ ፡ መንገዱ ፡ መተላላፊያ ፡ ሒዱ ፡ የምታገኙትንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሰርጉ ፡ ጽሩት ። ኢሊያም ፡ ባሮች ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ ወጥተው ፡ ያገኙትን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰቡ ፡ ክፉችንም ፡ በጎችንም ። ሰርጉም ፡ በተቀማጮች ፡ መላ ። ንጉሡም ፡ የተቀመጡትን ፡ ለማየት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ከዚያ ፡ አንዱን ፡ የሰርግ ፡ ልብስ ፡ ያለበሰውን ፡ ሰው ፡ አየ ። አለውም ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ። እንዴት ፡ የሰርግን ፡ ልብስ ፡ ሳትለብስ ፡ ወደዚኽ ፡ ገባኽ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ዝም ፡ አለ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ሎላልቱን ፡ አለ ፡ እጁንና ፡ እግሩን ፡ እሠሩ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ አውጥታችሁም ፡ ወደ ፡ ጭራሽ ፡ ጨለማ ፡ ጣሉት ፡ ልቅሶ ፡ ወደ ፡ ሚሆንበት ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨትም ። የተጸሩ ፡ ብዙ ፡ ናቸውና ፡ የተመረጡ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ናቸው ።

ህያ ፡ አንደኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

ጸሎት ።

መሐሪ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ ለታመኑች ፡ ሕዝብህ ፡ ስርየትንና ፡ ሰላምን ፡ እንድሰጣቸው ፡ እንለምንሃለን ፡ እርሳቸው ፡ ከኃጢአታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይነጹ ፡ ዘንድ ፡ ባራፊም ፡ ልብ ፡ ያገለግሉህ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፮፡ ፲፡—፲፱፡፡

በቀረውም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ በኃይሉም ፡ ችሎት ። የእግዚአብሔርን ፡ እቃ ፡ ጦር ፡ ሁሉ ፡ ልበሱ ። የሰይጣንን ፡ ተንኰል ፡ ትቋቋሙ ፡ ዘንድ ፡ እንድትቻላችሁ ። መታገላችን ፡ ከሥጋና ፡ ደም ፡ ጋራ ፡ አይደለምና ። ከገዦችና ፡ ከሥልጣናት ፡ ጋራ ፡ እንጅ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጨለማ ፡ ላይ ፡ ከሚገዙ ፡ ጋራ ፡ እንጅ ። በሰማይም ፡ ከምትኖር ፡ ከመንፈሳዊት ፡ ዓመፃ ፡ ጋራ ። ስለዚኽም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ እቃ ፡



ጦር ፡ ልበሱ ። በክፉ ፡ ቀን ፡ መቋቋም ፡ ስራውንም ፡ ሁሉ ፡ በፈጸማችሁ ፡ ጊዜ ፡ መቆም ፡ እንድትችሉ ። አሁንም ፡ ቁሙ ፡ ወገባችሁንም ፡ በውነት ፡ ታጠቁ ። የጽድቅንም ፡ ጥሩር ፡ ልበሱ ። እግራችሁም ፡ ተጫምታ ፡ ትሁን ፡ በሰላም ፡ ወንጌል ፡ መዘጋጀት ። ከዚኽም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ የሃይማኖትን ፡ ጋሻ ፡ ውሰዱ ። እሳት ፡ የምታቃጥለውን ፡ የክፉውን ፡ ፍላፃ ፡ ሁሉ ፡ ታጠፉ ፡ ዘንድ ፡ የምትችሉበት ። በራሳችሁም ፡ የመድኃኒት ፡ ራስ ፡ ቍር ፡ ጫኑ ። የመንፈስንም ፡ ሰይፍ ፡ ውሰዱ ። እርሱም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ያለ ። በጸሎትና ፡ በልመናም ፡ ሁሉ ፡ ሁለግዜ ፡ በመንፈስ ፡ ጸልዩ ። ለዚኽም ፡ ትጉ ፡ አዘውትራችሁ ፡ ስትለምኑ ፡ ለቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ለኔም ፡ ደግሞ ፡ ነገር ፡ ይሰጠኝ ፡ ዘንድ ፡ ባፌ ፡ መክፈቻ ። የወንጌልን ፡ ምሥጢር ፡ ገልጬ ፡ ለመናገር ። እኔ ፡ በምክንያቱ ፡ በሰንሰለት ፡ ታሥሬበት ፡ ያለሁ ፡ መልክተኛው ፡ ስሆንለት ። እገልጠው ፡ ዘንድ ፡ መናገር ፡ እንዲገባኝ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፬፡ ፵፮፡—፶፬፡፡

በቅፍርናሆምም ፡ ሰው ፡ ነበረ ፡ የንጉሥ ፡ ወገን ፡ ልጁም ፡ ታሞ ፡ ነበር ። ይኽም ፡ የሱስ ፡ ከይሁዳ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደርሱ ፡ ሒደ ፡ ለመነውም ፡ ይወርድ ፡ ዘንድ ፡ ልጁንም ፡ ይፈውስ ፡ ዘንድ ። ለሞት ፡ ቀርቦ ፡ ነበረና ። የሱስም ፡ አለው ፡ ምልክትና ፡ ተአምራት ፡ ካላያችሁ ፡ አታምኑም ። የንጉሥም ፡ ሰው ፡ አለው ። ጌታ ፡ ሆይ ፡ ውረድ ፡ ብላቴናዬ ፡ ሳይሞት ። የሱስም ፡ አለው ። ሒድ ፡ ልጅኽ ፡ ዳነልኽ ። ያም ፡ ሰው ፡ የሱስ ፡ ባለው ፡ ነገር ፡ አመነ ፡ ሔደም ። እርሱም ፡ አሁን ፡ ሲወርድ ፡ ባሮቹ ፡ ተቀበሉት ፡ የምስራችም ፡ ነገሩት ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። ልጅኽ ፡ ዳነ ። ከርሳቸውም ፡ የዳነባትን ፡ ጊዜ ፡ ጠየቀ ። አሉትም ። ትላንት ፡ በሰባተኛ ፡ ሰዓት ፡ መንቮዪቱ ፡ ተወችው ። አባቱም ፡ አሁን ፡ አወቀ ፡ የሱስ ፡ ልጅኽ ፡ ዳነ ፡ ባለው ፡ ሰዓት ፡ እንደ ፡ ሆነች ። እርሱም ፡ አመነ ፡ ቤቱም ፡ ሁሉ ። ይህችን ፡ ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ተአምራት ፡ አደረገ ፡ የሱስ ፡ ከይሁዳ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ።

## ህያ : ሁለተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ።

### ጸሎት ።

አቤቱ : እንለምንሃለን : ቤተ : ሰቦችህን : እርሳቸውም : ቤተ : ክርስቲያንህን : በሚዘወትር : አምልኮ : አኑራቸው : እርሳቸው : ከመጠበቅህ : በታች : ሁነው : ፈተና : ሁሉ : እንዳይጉዳቸው : በበጎ : ስራም : ለማገልገልህ : ልባቸው : በጣም : ተሰጥቶ : እንዲኖር : ለስምህ : ምስጋና : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት : ክፍል ። ፊልጵስዩስ : ፩፤ ፫፤—፲፩።

አምላኬን : አመሰግናለሁ : በማስባችሁ : አሳብ : ሁሉ ። ሁልግዜ : በልመናዬ : ሁሉ : ስለላንተ : ስለ : ሁላችሁ : ልመናዬን : ሳደርግ : በደስታ :: በወንጌል : ስላለቻችሁ : አንድነት : ከፊተኛው : ቀን : ጀምራችሁ : እስከ : ዛሬ : ድረስ :: በዚህ : አምኜ : በላንት : መልካሙን : ስራ : የጀመረ : እርሱ : ደግሞ : እንደ ፈጽመው : እስከ : የሱስ : ክርስቶስ : ቀን : ድረስ :: ለኔ : እንደሚገባ : ይህነን : በላንት : በሁላችሁ : አምን : ዘንድ :: በልቤ : ስለ : ኖራችሁ :: በሥራቴም : በምላሼም : በወንጌልም : መጽናት : እላንት : ሁላችሁ : ከኔ : ጋራ : በጸጋ : ተካፈዮች : ናችሁና :: እግዚአብሔር : ይመሰክርልኛልና : ለሁላችሁ : እንድናፈቅላችሁ : በየሱስ : ክርስቶስ : ምህረት :: ይህነንም : እጸልያለሁ : ፍቅራችሁ : ኢያደገች : ትበዛ : ዘንድ : በብዙ : እውቀት : በመንፈሳዊት : ፍርድም : ሁሉ :: የሚሻለውን : ነገር : ትፈትኑ : ዘንድ :: ፈጹማንም : ትሆኑ : ዘንድ : ያለ : ዕንቅፋትም : እስከ : ክርስቶስ : ቀን : ድረስ :: ከየሱስ : ክርስቶስም : የሚገኘውን : የጽድቅን : ፍሬ : ትመሉ : ዘንድ :: ለእግዚአብሔር : ምስጋናና : ክብር ::

### የወንጌል : ክፍል ። ማቴዎስ : ፲፰፤ ፳፩፤—፴፭።

የዚያን : ጊዜ : ጴጥሮስ : ወደርሱ : መጻ : አለም :: አቤቱ : ስንት : ጊዜ : ወንድሜ : ቢበድለኝ : ይቅር : ልበለው :: እስከ : ሰባትን : ጊዜ ። የሱስም : አለው :: ሰባት : ጊዜ : አልልኽም :: ሰብዓ : ጊዜ : ሰባት : እንጂ :: ስለዚኽ : ትመስላለች : መንግሥተ : ሰማያት : ንጉሥ : ሰውን : ከባሮቹ : ጋራ : ይቈጠር : ዘንድ : የወደደውን :: ከርሳቸውም : ጋራ : መቈጠር : በጀመረ : ጊዜ : አንደን : ወደርሱ : አመጡት : እልፍ : መክሊት : የነበረበት :: የሚከፍለውም : ባይኖረው : ጌታው : አዘዘ : ይሸጥ : ዘንድ : እርሱ : ምሽቱም : ልጆቹም : ያለውም : ሁሉ : ዕዳውም : ይከፈል : ዘንድ :: ያም : ባርያ : ወደቀ : ሰገደለትም : እንዲህ : ሲል :: አቤቱ : ታገሠኝ : ከብትኽንም : ሁሉ : እከፍልኻለሁ :: የዚያም : የባርያው : ጌታ : አዘነለት :: ፈታውም : ዕዳውንም : ተወለት :: ያ : ባርያ : ግን : ወጥቶ : አንደን : ባልንጀራውን : ባርያ : መቶ : ዲናር : ለርሱ : ያለበትን : አገኘ :: ያዘውም : አነቀውም : እንዲህ : ሲል :: ያለብህን : ከብቴን : ስጠኝ :: ባልንጀራውም : ባርያ : በግሩ : በታች : ወደቀ : ለመነውም : እንዲህ : ሲል :: ታገሠኝ : እኔም : ከብትኽን : ሁሉ : እከፍልኻለሁ :: እርሱ : ግን : እምቢ : አለው :: ወስደም : ወደ : ግዞት : አገባው : ዕዳውን : እስኪከፍል :: ባሮችም : ባልንጅሮቹ : አይተው : እጅግ : አዘኑ :: መጥተውም : የሆነውን : ሁሉ : ለጌታቸው : ነገሩት :: ከዚያ : ወዲያም : ጌታው : ጸራውና : አለው :: አንተ : ክፉ : ባርያ :: ያነን : ሁሉ : ዕዳ : ልመነኸኛልና : ተውሁልኽ :: አንተስ : አይገባኽምን : ደግሞ : ባርያውን : ባልንጅራኽን : ትምር : ዘንድ : እኔ : አንተን : እንደ : ማርሁኽ :: ጌታውም : ተቈጣና : ለሚሣቀዩት : አሳልፎ : ሰጠው : ያለበትን : ሁሉ : እስኪከፍል : ድረስ :: እንዲሁም : ደግሞ : የሰማዩ : አባቴ : ያደርግባችኋል :: ከላንት : ሁሉ : ኢያንዳንዳችሁ : የወንድሙን : ኃጢአት : ከልልባችሁ : ይቅር : ባትሉ ::

---

## ህያ : ሶስተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ።

### ጸሎት ።

አምላክ : ሆይ : መጸጀችንና : ኃይላችን : ያምልኮ : ሁሉ :

ፈጣሪ ፡ ያለህ ። እሺ ፡ በልለን ፡ እንለምንሃለን ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንህን ፡ የልባቸውን ፡ ጸሎት ፡ ለመስማት ፡ እኛም ፡ በሃይማኖት ፡ የምንለምነውን ፡ ነገር ፡ በውነት ፡ እናገኘው ፡ ዘንድ ፡ ስጠነ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ፊልጵስዩስ ፡ ፫፡ ፲፯፡—፬፡፩።

እኔን ፡ የምትመስሉ ፡ ሁኑ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ። እንዲህም ፡ የሚሔዱትን ፡ ተመልከቱ ፡ እኛ ፡ ምሳሌ ፡ እንደ ፡ ሆነላችሁ ። ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይሔዳሉና ፡ እርሳቸውም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ አልኋችሁ ። አሁንም ፡ ደግሞ ፡ አልቅሼ ፡ እላለሁ ፡ የክርስቶስ ፡ የመስቀሉ ፡ ጸላቶች ፡ ሁነው ። ፍጻሜያቸው ፡ ጥፋት ፡ ያለ ። አምላካቸው ፡ ሆዳቸው ፡ ያለ ። ክብሪቸውም ፡ በኅፍረታቸው ፡ ያለ ። አሳባቸውም ፡ በምድር ፡ ያለ ። እኛ ፡ ግን ፡ አገሬችን ፡ በሰማይ ፡ ናት ። ከዚያም ፡ መድኃኒታችንን ፡ ጌታችንን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ እንጠብቃለን ። እርሱ ፡ የተዋረደውን ፡ ሥጋችንን ፡ የሚለውጥ ። ለክብሩም ፡ ሥጋ ፡ የሚያስመስለው ። ሁሉን ፡ ያስገዛባት ፡ ዘንድ ፡ በሚችል ፡ በኃይሉ ፡ ታላቅነት ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፳፪፡ ፲፭፡—፳፪።

የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሔዱ ፡ ፈሪሳውያን ፡ በነገርም ፡ ያስቱት ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ። ደቀ ፡ መዛሙርታቸውንም ፡ ላኩበት ፡ ከሄሮድስ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። መምህር ፡ ሆይ ። እናውቃለን ፡ አንተ ፡ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆንኽ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ መንገድ ፡ በውነት ፡ ታስተምራለኽ ። ማንም ፡ አይገድህም ። የሰውን ፡ ፊት ፡ አታደላምና ። ንገረንም ፡ ምን ፡ ይመስልኻል ። ይገባልን ፡ ለቄሳር ፡ ግብር ፡ መስጠት ፡ ወይስ ፡ አይገባምን ። የሱስም ፡ ክፋታቸውን ፡ አወቀ ፡ አለም ። ለምን ፡ ትፈታተኑኛላችሁ ፡ እላንት ፡ ግብዞች ። የግብሩን ፡ ቅርጽ ፡ አስዩኝ ። እርሳቸውም ፡ ዲናርን ፡ አመጹ ። አላቸውም ። የማናት ፡ ይኽች ፡ መልክና ፡ ጽፈቲቱ ። አሉትም ፡ የቄሳር ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አላቸው ። እንኪያስ ፡ የቄሳርን ፡ ለቄሳር ፡ ስጡ ፡ የእግዚአብርንም ፡ ለእግዚአብሔር ። ሰምተውም ፡ ተደነቁ ፡ ትተውትም ፡ ሔዱ ።



ሀያ ፡ አራተኛ ፡ እሁድ ፡ ከሥላሴ ፡ በኋላ ።

ጸሎት ።

አቤቱ ፡ እንለምንሃለን ፡ ጉባኤህን ፡ ከመበደላቸው ፡ ሁሉ ፡ ፍታቸው ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡ በድካማችን ፡ ከሰራነው ፡ ከኃጢአታችን ፡ ማሠርያ ፡ ሁሉ ፡ በለጋስ ፡ ምህረትህ ፡ እንፈታ ፡ ዘንድ ። ይህነን ፡ ውደድ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በተባረከ ፡ ጌታችንና ፡ መድኃኒታችን ፡ በመክንያቱ ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ቆሎሰይስ ፡ ፩፡ ፫፡—፲፪።

እግዚአብሔርን ፡ የጌታችንንም ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ አባት ፡ እናመሰግናለን ። ሁለግዜ ፡ ስለላንት ፡ስንጸልይ ። ከሰማነ ፡ ጊዜ ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ ማመናችሁን ። ቅዱሳንንም ፡ ሁሉ ፡ መውደዳችሁን ። በሰማይ ፡ ስለ ፡ ተዘጋጀላችሁ ፡ ስለ ፡ ተስፋችሁ ። ቀድሞ ፡ የሰማችሁበት ፡ በወንጌል ፡ እውነት ፡ ነገር ። ወደላንት ፡ የደረሰች ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ እንደለች ። እርስዋም ፡ ፍሬን ፡ የምታፈራ ፡ ናት ፡ በላንት ፡ እንደፈራች ፡ ደግሞ ። የእግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ በውነት ፡ ከሰማችሁ ፡ ካወቃችሁም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ። እንደ ፡ ተማራችሁም ፡ ከኤጳፍራ ፡ ከወደጃችንና ፡ ባልንጀራችን ፡ በማገልገል ። እርሱ ፡ የታመነ ፡ አገልጋይ ፡ በክርስቶስ ፡ ስለላንት ፡ ያለ ። ፍቅራችሁንም ፡ በመንፈስ ፡ ያስታወቀነ ። ስለዚኽም ፡ እኛ ፡ ከሰማነ ፡ ጀምረን ፡ ጸሎት ፡ አልተውነም ፡ ስለላንት ። ኢየለመነ ፡ የፈቃደን ፡ እውቀት ፡ በጥበብ ፡ ሁሉ ፡ በመንፈሳዊም ፡ ማስተዋል ፡ ትመሉበት ፡ ዘንድ ። ለእግዚአብሔር ፡ የሚገባውን ፡ አካሔድ ፡ ትሔዱ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ሁሉ ። የመልካሙን ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፡ አፍርታችሁ ። እግዚአብሔርንም ፡ በማወቅ ፡ አድጋችሁ ። በኃይልም ፡ ሁሉ ፡ በርትታችሁ ፡ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ችሎት ። ለ

ትዕግሥት : ሁሉ : ልብንም : ለማስፈት : በደስታ ። አብን : ስታመሰግኑ : ለቅዱሳን : ርስት : መክፈልት : በብርሃን : ያበቃንውን ::

የወንጌል : ክፍል ። ማቴዎስ : ፱፤ ፲፰—፳፮።

ይህነንም : ሲነግራቸው : እነሆ : መኰንን : መጣ : ሰገደለትም : እንደህ : ሲል :: ልጄ : አሁን : ሞተች :: ነገር : ግን : ና : እጅኽን : ጫንባትና : ትድናለች :: የሱስም : ተነሥቶ : ተከተለው : ደቀ : መዛሙርቱም : ደግሞ :: እነሆም : ካሥራ : ሁለት : አመት : ጀምራ : ደም : የሚፈሳት : ሴት : በኋላው : መጣች : የልብሱንም : ጫፍ : ደሰሰች :: በልብዋ : ብላለችና : ልብሱን : ብቻ : ብነካው : እድናለሁ :: የሱስም : ተመልሶ : አያት : አላትም :: አይዞሽ : ልጄ : ሆይ :: ሃይማኖትሽ : አደነሽ :: ሴቲቱም : ደነች : ከዚያች : ሰዓት : ጀምሬ :: የሱስም : ወደ : መኰንኑ : ቤት : በመጣ : ጊዜ : አልቃሾች : የተሰበሰቡትም : ሲባሉ : አየ : አላቸውም :: ራቁ : ብላቴናዪቱ : አልሞተችም : ተኝታለች : እንጂ :: ከነገሩም : የተነሣ : ሳቁ :: ሕዝቡም : በወጡ : ጊዜ : ገባ : እጅዋንም : ያዛት :: ብላቴናዪቱም : ተነሣች :: ይህ : ወሬም : ወጣ : በዚያች : አገር : ሁሉ ::

---

ህያ : አምስተኛ : እሁድ : ከሥላሴ : በኋላ ።

ጸሎት ::

ያመኑብህን : የሕዝብህን : ፈቃድ : እንድታነቃ : እንለምንሃለን : አቤቱ : እርሳቸው : የበጎ : ስራውን : ፍሬ : ብዛት : አፍርተው : የደመወዜህን : ብዛት : ያገኙ : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

በመልእክት : ፈንታ :: ኤርምያስ : ፳፫፤ ፭—፰።

እነሆ : ዘመን : ትመጣለች : ይላል : እግዚአብሔር : ለዳዊት : ጻድቁን : ጫፍ : የማስነሣባት : ንጉሥም : ይነግሣል : ይከናወንማል : በምድርም : ፍርድና : ጽድቅን : ይሰራል ። በዘመኑ : ይሁዳ : ይድናል : እሥራኤልም : ምናለብኝ : ብሎ : ይቀመጣል ። የሚጸሩትም : ስም : ይኸ : ይሆናል : እግዚአብሔር : ጽድቃችን ። ስለዚኽ : እነሆ : ዘመን : ትመጣለች : ይላል : እግዚአብሔር : ደግሞም : የእሥራኤልን : ልጆች : ከምሥር : ምድር : ያወጣ : እግዚአብሔር : ሕያው : ነው : የማይሉባት :: ነገር : ግን : ከሰሜን : ምድር : ከጣልኋቸውም : አገር : ሁሉ : የእሥራኤልን : ቤት : ዘር : ያወጣ : ያገባቸውም : እግዚአብሔር : ሕያው : ነው : ይላሉ : እንጂ : ባገራቸውም : ይኖራሉ ::

የወንጌል : ክፍል ። ዮሐንስ : ፮፤ ፭—፲፬።

የሱስም : ዓይኑን : አንሣ : ብዙ : ሰዎችም : ወደርሱ : ሲመጡ : አየ :: ፊልጶስንም : አለው :: ከወዴት : እንጀራ : እንገዛለን : እሌኽ : ይበሉ : ዘንድ :: ይኽነንም : ማለቱ : ይፈትነው : ዘንድ : ነበረ :: እርሱ : የሚያደርገውን : ያውቅ : ነበረና :: ፊልጶስም : መለሰለት : አለውም ። በሁለት : መቶ : ዲናር : የሚገዛ : እንጀራ : አይበቃቸውም : ከርሳቸው : ኢያንዳንዱ : ጥቂት : ይወስድ : ዘንድ ። ከደቀ : መዛሙርቱም : አንዱ : እርሱም : እንድርያስ : የሲሞን : ጴጥሮስ : ወንድም : አለው :: ከዚኽ : አሽከር : አለ : አምስት : የገብስ : እንጀራ : ያያዘ : ሁለትም : ዓሣ :: ነገር : ግን : ምን : ይበቃል : ይኽ : እሌኽን : ለሚያኽሉ :: የሱስም : አለ :: ሰዎችን : እንዲቀመጡ : አድርጉ ። በዚያም : ስፍራ : እጅግ : መስክ : ነበረ :: ሰዎችም : ተቀመጡ : ቍጥራቸውም : አምስት : ሽህ : ያህላል :: የሱስም : እንጀሮችን : ወሰደ : አመሰገነም : ለደቀ : መዛሙርቱም : ሰጠ ። ደቀ : መዛሙርትም : ለተቀመጡት : ሰጡ :: እንደሁም : ከሁለቱ : ዓሦች : በወደዱት : መጠን ። በጸገቡም : ጊዜ : ደቀ : መዛሙርቱን : አለ ። የቀረውን : ቍራሽ : አከማቹ : አንዳች : እንዳይጠፋ :: አከማቹም : አሥራ : ሁለትም : ቅርጫት : ቍራሽን : መሉ : ካምስቱ : ገብስ : እንጀራ : ለበዮች : የቀረ ። ሰዎችም : የሱስ : ያደረገውን : ተአምራት : ባዩ : ጊዜ : አሉ :: በውነት : ይኽ : ወደ : ዓለም : የሚመጣ : ነቢይ : ነው ::

* ከመምጣት ፡ እሁድ ፡ በፊት ፡ ሌላ ፡ እሁድም ፡ እንደለ ፡ ከኤጲፋንያስ ፡ በኋላ ፡ የቀርውን ፡ የእሁድን ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ይጨምሩ ። እንደችም ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ቢተርፍ ፡ ትርፉ ፡ ይቅር ፡ የሀያ ፡ አምስተኛ ፡ እሁድ ፡ ነገር ፡ እንጅ ፡ እርሱ ፡ ወትሮ ፡ የመምጣትን ፡ እሁድ ፡ ሊቀድም ፡ ነውና ።

## የቅዱስ ፡ እንድርያስ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ለእንድርያስ ፡ ለቅዱስ ፡ ሐዋርያህ ፡ ጸጋ ፡ ሰጥተሃልና ፡ ልጅህ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጸራው ፡ ጊዜ ፡ በደስታ ፡ እንደ ፡ ታዘዘ ፡ እሺ ፡ ብሎም ፡ ሳይዘግይም ፡ እንደ ፡ ተከተለው ። ለሁላችንም ፡ ጸጋህን ፡ ስጥ ፡ እኛ ፡ በቅዱስ ፡ ቃልህ ፡ ተጸርተን ፡ ራሳችነን ፡ እንደ ፡ ያው ፡ እንሰጥ ፡ ዘንድ ፡ የተቀደሱትን ፡ ትእዛዛትህ ፡ ለመከተል ፡ በርሱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ሮሜ ፡ ፲፤ ፱፤—፳፩፤፤

ባፍኽ ፡ ተናግረህ ፡ የሱስ ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በትገልጽ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከሙታን ፡ እንደስነሣው ፡ በልብኽ ፡ ብታምን ፡ ትድናለኽ ። ሰው ፡ በልቡ ፡ ይጸደቅ ፡ ዘንድ ፡ ያምናልና ። በአፉም ፡ ይድን ፡ ዘንድ ፡ ገልጾ ፡ ይነግራል ። መጽሐፉ ፡ የሚያምንበት ፡ ሁሉ ፡ አያፍርም ፡ ይላልና ። በአይሁደዊና ፡ በአረማዊ ፡ መኻከል ፡ መለየት ፡ የለምና ። የሁላቸው ፡ ጌታ ፡ አንድ ፡ ነውና ። እርሱም ፡ ለሚጸሩበት ፡ ሁሉ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ነው ። በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚጸራ ፡ ሁሉ ፡ ይድናልና ። ነገር ፡ ግን ፡ እንዴት ፡ ይጸሩበታል ፡ የማያምኑበት ። ወይስ ፡ እንዴት ፡ ባልሰሙት ፡ ያምናሉ ። ወይስ ፡ እንዴት ፡ ይሰማሉ ፡ ሰባኪ ፡ የሌላቸው ። እንዴትስ ፡ ይሰብካሉ ፡ ባይላኩ ። እንደ ፡ ተጻፈ ። በሰላም ፡ የምስራች ፡ የሚነግሩ ፡ በመልካም ፡ የምስረች ፡ የሚነግሩ ፡ እግራቸው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያመረል ። ነገር ፡ ግን ፡ ሁላቸው ፡ ለወንጌል ፡ አልታ



ዘዙም ። ኢሳይያስ ፡ ይላልና ። አቤቱ ፡ ማን ፡ ያምናል ፡ መሰማታችነን ። እንጊዴህ ፡ ሃይማኖት ፡ ከመሰማት ፡ ነው ። መሰማትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ በውኑ ፡ አልሰሙምን ፡ እላለሁ ። እንዴታ ። በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ድምጻቸው ። ወጥተዋልና ። ቃላቸውም ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ድርቻ ፡ ደረሰ ። ነገር ፡ ግን ፡ እንዴህ ፡ እላለሁ ። እሥራኤል ፡ በውኑ ፡ አላወቀምን ። አስቀድሞ ፡ ሙሴ ፡ ይላል ። ሕዝብ ፡ ባይደለ ፡ አስቀናችኋለሁ ፡ በማያስተውልም ፡ ሕዝብ ፡ አስቈጣችኋለሁ ። ኢሳይያስ ፡ ግን ፡ በነገር ፡ ደፈረ ፡ አለም ። ባልሹኝ ፡ ተገኘሁ ። ላልጠየቁኝም ፡ ተገለጥሁ ። ስለ ፡ እሥራኤል ፡ ግን ፡ አለ ። ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እጀን ፡ ባመፀኛና ፡ በምቢተኛ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ዘረጋሁ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፬፤ ፲፰፤—፳፪፤፤

የሱስም ፡ በገሊላ ፡ ባሕር ፡ በኩል ፡ ሲመላለስ ፡ ሁለት ፡ ወንድማማችን ፡ አየ ። ሲሞንን ፡ ጴጥሮስ ፡ የሚሉትን ፡ እንድርያስንም ፡ ወንድሙን ፡ መረባቸውን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ሲጥሉ ። አዕማጀች ፡ ነበሩና ። አላቸውም ፡ በኋላዬ ፡ ኑ ፡ ሰው ፡ አዕማጀችንም ፡ አደርጋችኋለሁ ። እርሳቸውም ፡ የዚያን ፡ ጊዜውን ፡ መረባቸውን ፡ ትተው ፡ ተከተሉት ። ከዚያም ፡ ጥቂት ፡ አልፎ ፡ ሌሎችን ፡ ሁለት ፡ ወንድማማች ፡ አየ ። ያዕቆብን ፡ የዘብደዎስን ፡ ልጅ ፡ ዮሐንስንም ፡ ወንድሙን ፡ በሳምቡቅ ፡ ሁነው ፡ ካባታቸው ፡ ከዘብደዎስ ፡ ጋራ ፡ መረባቸውን ፡ ሲጠቅሙ ። ጸራቸውም ። እርሳቸውም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሳምቡቃቸውንና ፡ አባታቸውን ፡ ትተው ፡ ተከተሉት ።

## የቅዱስ ፡ ቶማስ ፡ የሐዋርያ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ ለዘላለምም ፡ የምትኖር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ ሃይማኖትን ፡ ለማጽናት ፡ ቅዱስ ፡ ሐዋርያህን ፡ ቶማስን ፡ በልጅህ ፡ ትንሣኤ ፡ ይጠራጠር ፡ ዘንድ ፡ ትተህዋ

ልና ። እኛን ፡ በጣም ፡ ያለ ፡ መጠራጠርም ፡ በልጅህ ፡ በየ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አስመንን ፡ ሣይማኖታችን ፡ በፊትህ ፡ ከቶ ፡
እንደይዘለፍ ። ስማኔ ፡ አቤቱ ፡ በርሱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡
ለርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ክብርና ፡ ም
ስጋና ፡ ሁሉ ፡ ይሁን ፡ አሁንና ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

## የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፪፤ ፲፱—፳፪፡፡

እንግዲህም ፡ እንግደችና ፡ መጻተኞች ፡ አይደላችሁም ፡፡
እላንት ፡ የቅዱሳን ፡ ባላገሮችና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ሰ
ቦች ፡ ናችሁ ፡ እንጅ ፡፡ በሐዋርያትና ፡ በነቢያትም ፡ መሠረ
ት ፡ ላይ ፡ ተሠራችሁ ፡፡ የማዝኑ ፡ ራስ ፡ ደንጊያ ፡ እርሱ ፡ የ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ያለ ። በርሱ ፡ ላይ ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ ተሰማ
ምቶበት ፡ ለቅዱስ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ በጌታ ፡ የሚያድግ ። በ
ርሱም ፡ እላንት ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሁናችሁ ፡ የምትሠሩበ
ት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ማደርያ ፡ በመንፈስ ፡፡

## የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፳፤ ፳፬—፴፩፡፡

ቶማስ ፡ ግን ፡ ዲዲሞስ ፡ የሚሉት ፡ ካሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አን
ዱ ፡፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ አልነበረም ፡ የሱስ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡፡
የቀሩትም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጌታን ፡ አየነ ፡ አሉት ፡፡ እ
ርሱም ፡ አላቸው ፡፡ የችንካሩን ፡ ምልክት ፡ በጁ ፡ ካላየሁ ፡፡
ጣቴንም ፡ ወደ ፡ ችንካሩ ፡ ምልክት ፡ ካላገባሁ ፡፡ እጄንም ፡
በጐኑ ፡ ካላኖርሁ ፡ አላምንም ፡፡ ከስምንት ፡ ቀንም ፡ በኋ
ላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ደግሞ ፡ በውሥጥ ፡ ነበሩ ፡ ቶማስ
ም ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡፡ የሱስም ፡ መጣ ፡ ደጁ ፡ ተቈልፎ ፡
ሳለ ፡፡ በማኸልም ፡ ቆመ ፡ ሰላም ፡ ይሁንላችሁም ፡ አለ ፡፡
ቶማስንም ፡ አለው ፡፡ ጣትኽን ፡ ወደዚኽ ፡ አምጣ ፡ እጄን
ም ፡ እይ ፡፡ እጅኽንም ፡ አምጣና ፡ ወደ ፡ ጐኔ ፡ አግባት ፡፡ የ
ማታምንም ፡ አትሁን ፡ አማኝ ፡ እንጅ ፡፡ ቶማስም ፡ መለ
ሰ ፡ አለም ፡፡ ጌታዬ ፡ አምላኪም ፡፡ የሱስም ፡ አለው ፡፡ ቶ
ማስ ፡ ሆይ ፡ ስላየኸኝ ፡ አመንኽ ፡፡ ሳያዩ ፡ የሚያምኑ ፡ ተ
መሰገኑ ፡፡ የሱስም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ሌላ ፡ ተአምራት ፡ አደ
ረገ ፡ በደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ፊት ፡ በዚኽ ፡ መጽሐፍ ፡ ያልተጻ



ፈ ፡፡ ይኽም ፡ ተጻፈ ፡ ታምኑ ፡ ዘንድ ፡ የሱስ ፡ እርሱ ፡ ክርስ
ቶስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡ ስታምኑም ፡ ሕ
ይወት ፡ ትሆንላችሁ ፡ ዘንድ ፡ በስሙ ፡፡

## የቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ የመመለሱ ፡ በዓል ።

## ጸሎት ።

አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በተባረከ ፡ ሐዋርያህ ፡ በቅዱስ ፡
ጳውሎስ ፡ ስብከት ፡ የወንጌልን ፡ ብርሃን ፡ ባለም ፡ ሁሉ ፡
አስበርተሃልና ። ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ የርሱን ፡ በተአምራት ፡ የሆ
ነውን ፡ መመለስ ፡ አስበን ፡ እኛ ፡ እናመሰግንህበት ፡ ዘን
ድ ፡፡ እርሱም ፡ ያስተማረባቱን ፡ ትምህርት ፡ እንከተል ፡
ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

## በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፱፤ ፩—፳፪፡፡

ሳውል ፡ ግን ፡ ገና ፡ ቅያሜንና ፡ መግደልን ፡ በጌታ ፡ ደቀ ፡
መዛሙርት ፡ ላይ ፡ አስተንፍሶ ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቃ ፡ ደ
ረሰ ፡፡ ከርሱም ፡ ጽፈትን ፡ ለመነ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ለመስጊ
ድ ፡ ሁሉ ፡፡ በዚኽ ፡ መንገድ ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ቢያገ
ኝ ፡ ወንዶችን ፡ ሴቶችንም ፡ አሥሮ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ያ
መጣቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ሲሔድም ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ቀረበ ፡፡
ድንገትም ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ብርሃን ፡ ከሰማይ ፡ በራ ፡፡ በምድ
ር ፡ ላይም ፡ ወደቀ ፡ ድምፅንም ፡ ሰማ ፡ የሚል ። ሳውል ፡ ሳው
ል ፡ ለምን ፡ ታሳድደኛለኽ ። አለውም ። አንተ ፡ ማነኽ ፡ አቤቱ ፡፡
ጌታም ፡ አለው ። እኔ ፡ የሱስ ፡ ነኝ ፡ አንተ ፡ የምታሳድደኝ ። የሾ
ለውን ፡ ብረት ፡ ብትረግጥ ፡ ይብስኻል ። ኢየተንቀጠቀጠም ፡
ኢየደነገጠም ፡ አለ ፡፡ አቤቱ ፡ ምን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ትሻ
ለኽ ፡፡ ጌታም ፡ አለው ፡ ተነሣና ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሒድ ፡፡ ከዚ
ያም ፡ ይነግሩኻል ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ የሚገባኽን ። ከርሱ ፡
ጋራ ፡ ባንድ ፡ የነበሩት ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ተደንቀው ፡ ቆሙ ፡ ድ
ምፅን ፡ ኢየሰሙ ፡ ማነንም ፡ ሳያዩ ፡፡ ሳውልም ፡ ከምድር ፡
ተነሣ ። ዓይኖቹም ፡ በተከፈቱ ፡ ጊዜ ፡ ማንንም ፡ አላየም ።
በጁም ፡ አድላድለው ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ አገቡት ፡፡ ሶስት ፡

ቀንም ፡ ሳያይ ፡ ሳይበላም ፡ ሳይጠጣም ፡ ተቀመጠ ፡፡ በደማስቀም ፡ አንድ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነበረ ፡ ስሙን ፡ ሐናንያ ፡ የሚሉት ፡፡ ጌታም ፡ በራእይ ፡ አለው ፡፡ ሐናንያ ፡ ሆይ ፡፡ እርሱም ፡ አለ ፡፡ እነሆኝ ፡ አቤቱ ፡፡ ጌታም ፡ አለው ፡፡ ተነሥተኽ ፡ ሒድ ፡ ቅን ፡ መንገድ ፡ በምትባል ፡ መንገድ ፡፡ በይሁዳ ፡ ቤትም ፡ አንድ ፡ ስሙን ፡ ሳውል ፡ የሚሉትን ፡ አገሩም ፡ ጠርሴስ ፡ ያለችውን ፡ ሰው ፡ እሻ ፡ እነሆ ፡ ይጸልያልና ፡፡ በራእይም ፡ አንድ ፡ ስሙን ፡ ሐናንያ ፡ የሚሉትን ፡ ሰው ፡ አየ ፡ ሲገባ ፡ እጁንም ፡ በላዩ ፡ ሲጭንበት ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡፡ ሐናንያም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡፡ አቤቱ ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ የዚኽን ፡ ሰው ፡ ነገር ፡ ፈጽሜ ፡ ሰማሁ ፡ ስንት ፡ ክፉ ፡ እንደደረገ ፡ በየሩሳሌም ፡ ባሉ ፡ በቅዱሳንኽ ፡ ላይ ፡፡ ከዚኽም ፡ ከካህናት ፡ አለቆች ፡ ሥልጣን ፡ አለው ፡ ስምኽን ፡ የሚጸሩትን ፡ ሁሉ ፡ ያሥር ፡ ዘንድ ፡፡ ጌታም ፡ አለው ፡፡ ሒድ ፡ ይኽ ፡ ለኔ ፡ የተመረጸ ፡ እቃ ፡ ነውና ፡ በአሕዛብ ፡ በነገሥታትም ፡ በእሥራኤል ፡ ልጆችም ፡ ፊት ፡ ስሜን ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡፡ እኔም ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡ የሚቀበለውን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አስታውቀዋለሁ ፡፡ ሐናንያም ፡ ሔደ ፡ ወደ ፡ ቤትም ፡ ገባ ፡፡ እጁንም ፡ ጫነበት ፡ አለም ፡፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ሳውል ፡፡ ጌታ ፡ የሱስ ፡ በመንገድ ፡ ስትመጣ ፡ የታየኽው ፡ ወደንተ ፡ ላከኝ ፡፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ይመላብኽ ፡ ዘንድ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንደ ፡ ቅርፊት ፡ ያለ ፡ ካይኑ ፡ ወደቀ ፡፡ አየም ፡ ተነሥቶም ፡ ተጠመቀ ፡፡ መብልም ፡ በተቀበለ ፡ ጊዜ ፡ በረታ ፡፡ ሳውልም ፡ በደማስቀ ፡ ካሉ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጋራ ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ተቀመጠ ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜውም ፡ በመስጊዶች ፡ ሰበከ ፡ በክርስቶስ ፡ እርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡ የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ ተደነቁ ፡፡ አሉም ፡፡ ይኽ ፡ በየሩሳሌም ፡ ይህነን ፡ ስም ፡ የሚጸሩትን ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋ ፡ አይደለምን ፡፡ ስለዚኽም ፡ ወደዚኽ ፡ መጣ ፡ አሥሮ ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቆች ፡ ሊወስደቸው ፡፡ ሳውልም ፡ ኃይል ፡ ተጨመረችለት ፡ በደማስቀም ፡ የተቀመጡትን ፡ አይሁድ ፡ አስጨነቀ ፡ ይኽ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሲገልጥ ፡፡



የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፲፱፡ ፳፯፡—፴፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ መለሰ ፡ ጴጥሮስ ፡ እንደዚህም ፡ አለው ፡፡ እነሆን ፡ እኛ ፡ ሁሉን ፡ ትተን ፡ ተከተልነኽ ፡፡ ምን ፡ እናገኝበታለን ፡፡ የሱስም ፡ አላቸው ፡፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ እላንትስ ፡ የተከተላችሁኝ ፡ በሐዲስ ፡ ልደት ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በምስጋናው ፡ ዙፋን ፡ሲቀመጥ ፡ ጊዜ ፡፡ እላንትም ፡ ባሥራ ፡ ሁለት ፡ ዙፋኖች ፡ ትቀመጣላችሁ ፡ ባሥራ ፡ ሁለቱም ፡ በእሥራኤል ፡ ነገዶች ፡ ትፈርዳላችሁ ፡፡ ቤትንም ፡ የተወ ፡ ሁሉ ፡ ወንድሞችንም ፡ እኅቶችንም ፡ አባትንም ፡ እናትንም ፡ ምሽትንም ፡ ልጆችንም ፡ እርሻንም ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡፡ መቶ ፡ ዕጽፍ ፡ ይወስዳል ፡ የዘላለሙንም ፡ ሕይወት ፡ ይወርሳል ፡፡ ብዙ ፡ ግን ፡ ፊተኞች ፡ ኋለኞች ፡ ይሆናሉ ፡ ኋለኞችም ፡ ፊተኞች ፡፡

የክርስቶስ ፡ መቅረብ ፡ በመቅደስ ፡
የማርያም ፡ ድንግል ፡ የመንጻትዋ ፡
በዓል ፡፡

ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡፡ እኛ ፡ በትሕትና ፡ ምስጋናህን ፡ እንለምናለን ፡ አንድ ፡ ልጅህ ፡ በዚህ ፡ ቀን ፡ በመቅደስ ፡ በሥጋችን ፡ ኑሮ ፡ እንደ ፡ ተሰጠልህ ፡ እኛም ፡ በንጹሕ ፡ ልብ ፡ የተሰጠነልህ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ በርሱ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

በመልእክት ፡ ፊንታ ፡ መልክያስ ፡ ፫፡ ፩፡—፫፡፡

እነሆ ፡ መልክተኛዬን ፡ እልካለሁ ፡ መንገድንም ፡ በፊቴ ፡ ያበጃል ፡፡ ድንገትም ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ ይመጣል ፡ ጌታው ፡ እላንት ፡ የምትሹት ፡ የቃል ፡ ኪደንም ፡ መልአክ ፡ እላንት ፡ የምትወዱት ፡፡ እነሆ ፡ ይመጣል ፡ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ፡፡ የሚመጣበትን ፡ ቀን ፡ ግን ፡ መታገሥ ፡ የሚችል ፡ ማነው ፡፡ እርሶስ ፡ ሲታይ ፡ ጊዜ ፡ የሚቆም ፡

ማነው ። እንደምታነጻ ፡ እሳት ፡ነውና ፡ እንደ ፡ አጻቦችም ፡ ሳቡና ፡ ነውና ። ብሯንም ፡ እንጥሮና ፡ አጽርቶ ፡ ይቀመጣል ። የሌዊንም ፡ ልጆች ፡ ያጸራል ፡ እንደ ፡ ወርቅና ፡ እንደ ፡ ብርም ፡ ያነጽራቸዋል ። በጽድቅም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባንን ፡ የሚያቀርቡ ፡ ይሆናሉ ። እግዚአብሔርም ፡ በይሁደና ፡ በየሩሳሌም ፡ መሥዋዕት ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ እንደ ፡ ድሮ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ቀደሙ ፡ አመታትም ። ለፍርድም ፡ ወደላንት ፡ እቀርባለሁ ፡ ፈጣኝ ፡ ምስክርም ፡ እሆናለሁ ፡ ባስማተኞችና ፡ ባመንዝሮች ፡ በሐሰትም ፡ በሚምሉ ፡ በብንደኛም ፡ ላይ ፡ በደመወዜው ፡ ግፍ ፡ በሚሰሩ ፡ ባላቸውም ፡ በሞታቸው ፡ ላይ ፡ አባትና ፡ እናትም ፡ በሌላቸው ፡ ላይ ። እንግደውንም ፡ በሚጋፉ ፡ እኔንም ፡ በማደፈሩ ፡ አለ ፡ የሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፪፡ ፳፪፡—፵፡፡

የመንጻትዋም ፡ ወራት ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሙሴ ፡ ሕግ ። ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ይዘውት ፡ ወጡ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቆሙት ፡ ዘንድ ። (በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ። የናቱን ፡ ማሕፀን ፡ የከፈተ ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ይባል ።) መሥዋዕትም ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተባለ ። ሁለት ፡ ዋልያ ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ልጆች ። እነሆም ፡ ሰው ፡ በየሩሳሌም ፡ነበረ ፡ ስሙን ፡ ስምዖን ፡ የሚሉት ። ይኸም ፡ ሰው ፡ ጻድቅ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ፈሪ ፡ ነበረ ፡ የእሥራኤልንም ፡ መጸናናት ፡ ደጅን ፡ ጸና ። መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ነበረበት ። ከመንፈስ ፡ ቅዱሰም ፡ ተገልጾለት ፡ ነበረ ፡ ሞትን ፡ እንደያይ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክርስቶስ ፡ ሳያይ ። በመንፈስም ፡ ተደዞ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ደረሰ ። አባት ፡ እናቱም ፡ ብላቴናውን ፡ የሱስን ፡ ይዘው ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ልማድ ፡ ያደርጉለት ፡ ዘንድ ። እርሱም ፡ በክንዱ ፡ ተሸከመው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ባረከ ፡ አለም ። ዛሬ ፡ አቤቱ ፡ ባርያኽን ፡ በሰላም ፡ ታሰነብታለህ ፡ እንደ ፡ ነገርኽ ። ዓይኖቼ ፡ መድኃኒት



ኽን ፡ አይተዋልና ። በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ያዘጋጀኸውን ። ብርሃን ፡ ሁኖ ፡ ለአሕዛብ ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ። ለወገንኽም ፡ ለእሥራኤል ፡ ክብር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ዮሴፍም ፡ እናቱም ፡ ስለርሱ ፡ ስለሚባለው ፡ ተደነቁ ። ስምዖንም ፡ ባረካቸው ። እናቱንም ፡ ማርያምን ፡ አላት ። እነሆ ፡ ይኸ ፡ ለብዙ ፡ ሰዎች ፡ ከእሥራኤል ፡ ወገን ፡ ለመውደቅ ፡ ለመነሣትም ፡ የተቀመጠ ፡ ነው ። ለምትከራከርባትም ፡ ምልክት ። አንቺም ፡ ደግሞ ፡ ሰይፍ ፡ ነፍስሽን ፡ ወግቶ ፡ ያልፋል ። በብዙ ፡ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ያለ ፡ አሳብ ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ። ሐናም ፡ ነቢዪቱ ፡ የፋኑኤል ፡ ልጅ ፡ ከአሴር ፡ ወገን ፡ የምትሆን ፡ ነበረች ። ይህችም ፡ አርጅታ ፡ ነበረች ፡ በብዙ ፡ ዘመን ። ከባልዋም ፡ ጋራ ፡ ተቀመጠች ፡ ከድንግልናዋ ፡ በኋላ ፡ ሰባት ፡ አመት ። እርስዋም ፡ የሰማንያ ፡ አራት ፡ አመት ፡ መበለት ፡ ነበረች ። ከቤተ ፡ መቅደስም ፡ ሳትለይ ፡ በጾም ፡ በጸሎትም ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ ታገለግል ፡ ነበረች ። እርስዋም ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ መጻች ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ባረከች ። ስለርሱም ፡ ተናገረች ፡ በየሩሳሌም ፡ኑረው ፡ የመድኃኒትን ፡ ተስፋ ፡ ለሚጠብቁ ፡ ሁሉ ። ሁሉንም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ በጨረሱ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ወደ ፡ አገራቸው ፡ ወደ ፡ ናዝሬት ፡ ተመለሱ ። ሕፃኑ ፡ ግን ፡ አደገ ፡ በመንፈስም ፡ በረታ ፡ ጥበብ ፡ መልቶበት ። የእግዚአብሔርም ፡ ጸጋ ፡ በርሱ ፡ ነበረች ።

---

### የቅዱስ ፡ ማትያስ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ባስያዧ ፡ በይሁድ ፡ ፈንታ ፡ የታመነውን ፡ ባርያህ ፡ ማትያስን ፡ የመረጽህ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለት ፡ ሐዋርያት ፡ ቍጥር ፡ አንድ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ጸጋህን ፡ ስጥ ። ወትሮ ፡ ካሰተኞች ፡ ሐዋርያት ፡ ተጠብቃ ፡ በታመኑ ፡ በውነተኞችም ፡ ጠባቆች ፡ ትሠራና ፡ ትደላደል ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ።

በመልእክት ፡ ፈንታ ። የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፩፤ ፲፭፤—፳፮፡፡

በዚያም ፡ ወራት ፡ ጴጥሮስ ፡ በደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ማኽል ፡ ተነሣ ። (ከዚያም ፡ ሰዎች ፡ ተከማችተው ፡ ነበሩ ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ስም ፡ የሚያህሉ ።) አለም ። እላንት ፡ ወንድማማች ፡ ሰዎች ። ይኽ ፡ መጽሐፍ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ይገባ ፡ ነበረ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በዳዊት ፡ አፍ ፡ አስቀድሞ ፡ የሱስን ፡ ለያዙት ፡ መሪ ፡ ስለ ፡ ሆናቸው ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ የተናገረው ። ከኛ ፡ ጋራ ፡ ተቈጥሮ ፡ ነበረና ፡ ዕፃውም ፡ ለዚኽ ፡ ማገልገል ፡ ወድቆለት ፡ ነበረ ። ይኽ ፡ ሰውም ፡ እርሻውን ፡ ገዛ ፡ በዓመፀ ፡ ዋጋ ። በግምባሩም ፡ ወድቀ ፡ ከማኽሉም ፡ ተቀደደ ፡ አንጀቱም ፡ ሁሉ ፡ ፈሰሰ ። ወሬውም ፡ በየሩሳሌም ፡ በተቀመጡት ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ታወቀ ። ያ ፡ እርሻ ፡ በቋንቋቸው ፡ አከልደማ ፡ ማለቱ ፡ የደም ፡ እርሻ ፡ እስኪጸራ ፡ ድረስ ። በመዝሙር ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏልና ። ማደርያው ፡ ባድ ፡ ትሁን ፡ የሚኖርባትም ፡ አይኑር ። ሹመቱንም ፡ ሌላ ፡ ይውሰደት ። እንግዴህም ፡ ጌታችን ፡ የሱስ ፡ በኛ ፡ ዘንድ ፡ የገባውንና ፡ የወጣውን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ከዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ጀምሮ ፡ ከኛ ፡ ዘንድ ፡ ተይዞ ፡ እስከሚወጣበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ከሔዱ ፡ ሰዎች ፡ አንዱ ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ለትንሣኤው ፡ ምስክር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። ሁለትንም ፡ ከዚያ ፡ አቆሙ ። ዮሴፍን ፡ በርሰባ ፡ የሚባለውን ፡ ዮስጦስም ፡ የተጸራውን ። ማትያስንም ። ጸለዩም ፡ እንደህ ፡ ሲሉ ። አንተ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ የሁሉን ፡ ልብ ፡ የምታውቅ ። ከለዚኽ ፡ ከሁለቱ ፡ አንዱን ፡ ግለጥ ፡ የመረጥኸውን ። የዚቺን ፡ ማገልገልና ፡ የመልእክትን ፡ ጕልት ፡ ይሁዳ ፡ የተዋትን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ስፍራውም ፡ ይሔድ ፡ ዘንድ ። ዕፃም ፡ ተጣጣሉ ። ዕፃውም ፡ በማትያስ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ። ካሥራ ፡ አንዱ ፡ ሐዋርያት ፡ ጋራም ፡ ተቈጠረ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፲፩፤ ፳፭፤—፴፡፡

በዚያን ፡ ጊዜም ፡ መለሰ ፡ የሱስ ፡ አለም ። አመሰግንኻለሁ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ጌታ ። ይኽነን ፡ ከብልሀተኞችና ፡ ካዋቆች ፡ ሠውረኸልና ፡ ለሕፃናትም ፡



ገለጥሀው ። አወን ፡ አባት ፡ ሆይ ። እንደህ ፡ ፈቃድኽ ፡ ነበረችና ፡ በፊትኽ ። ሁሉ ፡ ተሰጠኝ ፡ ካባቴ ፡ ዘንድ ። አንድም ፡ ልጅን ፡ አያውቀውም ፡ ከአብ ፡ በቀር ። አብንም ፡ ማንም ፡ አያውቀውም ፡ ከልጅ ፡ በቀር ፡ ልጅም ፡ ይገልጽለት ፡ ዘንድ ፡ ከሚሻው ። ወደኔ ፡ ኑ ፡ እላንት ፡ ደካሞች ፡ ሁሉ ፡ ሸክማችሁም ፡ የከበደ ፡ እኔም ፡ አሳርፋችኋለሁ ። ቀምበሬን ፡ በላያችሁ ፡ ተሸከሙ ፡ ከኔም ፡ ተማሩ ። እኔ ፡ ገር ፡ ነኝና ፡ በልቤም ፡ ትሑት ፡ ነኝ ። ዕረፍትም ፡ ለነፍሳችሁ ፡ ታገኛላችሁ ። ቀምበሬ ፡ መልካም ፡ ነውና ፡ ሸክሜም ፡ ቀሊል ፡ ነውና ።

---

የማርያም ፡ የቅድስት ፡ ድንግል ፡ መወራት ።

ጸሎት ።

እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ አቤቱ ፡ ጸጋህን ፡ በልባችን ፡ ታፈስ ፡ ዘንድ ፡ እኛ ፡ የልጅህ ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥጋ ፡ መልበሱን ፡ በመልአክ ፡ መልእክት ፡ እንደ ፡ አወቅነው ፡ እንደሁም ፡ በስቅለቱና ፡ በሕማማቱ ፡ ወደ ፡ ትንሣኤው ፡ ክብር ፡ እንደርስ ፡ ዘንድ ፡ በርሱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

በመልእክት ፡ ፈንታ ። ኢሳይያስ ፡ ፯፤ ፲፤—፲፭፡፡

ደግሞም ፡ ጨመረ ፡ እግዚአብሔር ፡ አካዝንም ፡ አለው ። ከእግዚአብሔር ፡ ከአምላክኽ ፡ ምልክት ፡ ለምንልኽ ፡ ወደ ፡ ሢኦል ፡ ጠልቆ ፡ የሚወርድ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ከፍታ ፡ የሚወጣ ። አካዝም ፡ አለ ፡ አልለምንም ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አልፈታተንም ። አለም ፡ እላንት ፡ የዳዊት ፡ ቤት ፡ ስሙ ። በውኑ ፡ በላንት ፡ ዘንድ ፡ ሰውን ፡ ታስቸግሩ ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ ይሆናልን ፡ አምላኬን ፡ ደግማችሁ ፡ ታስቸግራላችሁና ። ስለዚኽም ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምልክትን ፡ ይሰጣችኋል ። እነኋት ፡ ቈንጃ ፡ ትፀንሳለች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ትወልዳለች ፡ ስሙንም ፡ አማኑኤል ፡ ብላ ፡ ትጸራዋለች ። ቅቤና ፡ ማር ፡ ይበላል ፡ ክፉን ፡ ለመጽላት ፡ መልካሙንም ፡ ለመምረጽ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፩፡ ፳፮—፴፰።

በስድስተኛውም ፡ ወር ፡ ገብርኤል ፡ መልአክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ናዝሬት ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ አገር ፡ ተላከ ። ላንድ ፡ ስሙን ፡ ዮሴፍ ፡ ለሚሉት ፡ ከዳዊት ፡ ወገን ፡ ሰው ፡ ወደታጩች ፡ ቆንጆ ። የቆንጆዪቱም ፡ ስም ፡ ማርያም ፡ ነው ። መልአኩም ፡ ወደርስዋ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ አለ ። ደስ ፡ ይበልሽ ፡ ጸጋ ፡ የመላብሽ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ካንች ፡ ጋራ ፡ ነው ። በሴቶች ፡ መኻከል ፡ የተባረክሽ ፡ ነሽ ። እርስዋም ፡ ባየችው ፡ ጊዜ ፡ ከነገሩ ፡ ደነገጸች ፡ አሰበችም ፡ እንደህ ፡ ስትል ። ይኽ ፡ ሰላም ፡ ምንድር ፡ ነው ። መልአኩም ፡ አላት ፡ አትፍሪ ፡ ማርያም ፡ ሆይ ። ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጸጋ ፡ አግኝተሻልና ። እነሆም ፡ በሆድ ፡ ትፀንሻለሽ ፡ ልጅም ፡ ትወልጃለሽ ። ስሙንም ፡ የሱስ ፡ ትዪዋለሽ ። ይኽም ፡ ታላቅ ፡ ይሆናል ፡ የልዑል ፡ ልጅም ፡ ይባላል ። እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ የዳዊትን ፡ ያባቱን ፡ ዙፋን ፡ ይሰጠዋል ። በያዕቆብም ፡ ወገን ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ። ለመንግሥቱም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ። ማርያምም ፡ መልአኩን ፡ አለችው ። ይኽ ፡ እንዴት ፡ ይሆናል ፡ ወንድ ፡ ሳላውቅ ። መልአኩም ፡ መለሰ ፡ አላትም ። መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በላይሽ ፡ ይመጣል ፡ የልዑል ፡ ኃይልም ፡ ያጸልልሻል ። ስለዚኽም ፡ ካንች ፡ የሚወለደው ፡ ቅዱሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ይባላል ። እነሆችም ፡ ኤልሳቤጥ ፡ ዘመድሽ ፡ እርስዋም ፡ ልጅ ፡ ፀነሰች ፡ በርጅናዋ ። ይኽም ፡ ወር ፡ ስድስተኛ ፡ ነው ፡ ለዚያች ፡ መካን ፡ ለምትባለው ። ነገር ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አይሳነምና ። ማርያምም ፡ አለች ። እነሆኝ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባርያ ። እነደ ፡ ነገርኽ ፡ ይሁንልኝ ። መልአኩም ፡ ከርስዋ ፡ ተመለሰ ።

## የቅዱስ ፡ ማርቆስ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ ቅድስት ፡



ቤተ ፡ ክርስቲያንህን ፡ በወንጌላዊህ ፡ በቅዱስ ፡ ማርቆስ ፡ በሰማያዊት ፡ ትምህርቱ ፡ እንደ ፡ አስተማርሃት ፡ ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ እኛ ፡ በከንቱ ፡ ትምርት ፡ ንፋስ ፡ ሁሉ ፡ ሕፃናትን ፡ መስለን ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ እንደንወዘወዝ ፡ በቅዱስ ፡ ወንጌልህ ፡ እውነት ፡ እንድንጸና ፡ እንጅ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ኤፌሶን ፡ ፬፡ ፯—፲፮።

ከኛ ፡ ግን ፡ ለያንዳንዱ ፡ በክርስቶስ ፡ ስጦታ ፡ መጠን ፡ ጸጋ ፡ ተሰጠችነ ። ስለዚኽ ፡ ይላል ። ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጣ ፡ ምርኮንም ፡ ማረከ ። ለሰዎችም ፡ ስጦታ ፡ ሰጠ ። መውጣቱስ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ በፊት ፡ ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ምድር ፡ ስለ ፡ ወረደ ፡ ነው ፡ እንጅ ። የወረደው ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ ከሰማያት ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ የወጣው ፡ ሁሉን ፡ ይመላ ፡ ዘንድ ። እርሱም ፡ ሰጠ ፡ እኩሌቶች ፡ ሐዋርያት ፡ እኩሌቶችም ፡ ነቢያት ። ሌሎችም ፡ ሰባኮች ። ሌሎችም ፡ ጠባቆች ፡ አስተማሮችም ። ቅዱሳን ፡ እንዲፈጸሙ ፡ ለማገልገል ፡ ስራ ። የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ ለመስራት ። ሁላችን ፡ እስክንደርስ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ሃይማኖት ፡ አንድነት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጅም ፡ ዕውቀት ። እስከ ፡ ፍጹም ፡ ሰው ፡ ድረስ ። እስከ ፡ ክርስቶስ ፡ አካል ፡ እስከ ፡ ፍጻሜው ፡ ልክ ፡ ድረስ ። ሕፃናት ፡ እንደንሆን ፡ ሞገድ ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ የሚያደርግነ ፡ ከትምህርት ፡ ንፋስም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ የምንሔድ ፡ በሰዎች ፡ ትንኰል ፡ በምክራቸው ፡ የሚያታሉ ፡ ሊያጠፉ ። በፍቅር ፡ ግን ፡ እውነተኞች ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ። ወደርሱ ፡ ራስ ፡ ወደሚሆን ፡ እንድናድግ ፡ እርሱም ፡ ክርስቶስ ። ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ የሚዋደድበት ፡ በጅማትም ፡ ሁሉ ፡ የሚሰማማበት ፡ የሚታሠርም ፡ ኢያንዳንዱ ፡ በየክፍሉ ፡ የሰጠውን ፡ ያህል ። ሥጋ ፡ እንዲያድግበት ፡ በፍቅር ፡ ይሠራ ። ዘንድ ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፲፭፡ ፩—፲፮።

እኔ ፡ በውነት ፡ የወይን ፡ ጕንድ ፡ ነኝ ። ተካዩም ፡ አባቴ ፡ ነው ። በኔ ፡ ያለውና ፡ የማያፈራውን ፡ ጫፉን ፡ ሁሉ ፡ ያስወ

ግድዋል ። የሚያፈራውን ፡ ጫፍ ፡ ግን ፡ ያጸራዋል ፡ እጅግ ፡ ያፈራ ፡ ዘንድ ። እላንት ፡ አሁን ፡ ንጹሓን ፡ ናችሁ ፡ ስለ ፡ ነገርኋችሁ ፡ ነገር ። በኔ ፡ ኑሩ ፡ እኔም ፡ በላንት ። ጫፍም ፡ ብቻውን ፡ ሁኖ ፡ እንደማይችል ፡ ያፈራ ፡ ዘንድ ፡ በወይኑ ፡ ጕንድ ፡ ከሌለ ። እንደሁም ፡ እላንት ፡ በኔ ፡ ባትኖሩ ። እኔ ፡ የወይን ፡ ጕንድ ፡ ነኝ ፡ እላንትም ፡ ጫፎች ፡ ናችሁ ። በኔ ፡ የሚኖር ፡ እኔም ፡ በርሱ ፡ እርሱ ፡ እጅግ ፡ ፍሬ ፡ ያፈራል ። ያለኔ ፡ አንዳች ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አትችሉምና ። ማንም ፡ በኔ ፡ ባይኖር ፡ እንደ ፡ ጫፍ ፡ ወደ ፡ሜዳ ፡ ይጣላል ፡ ይደርቅማል ። ይሰበስቡታልም ፡ ወደሳትም ፡ ይጥሉታል ፡ ይቃጠልማል ። በኔ ፡ ብትኖሩ ፡ ቃሌም ፡ በላንት ፡ ቢኖር ። የምትሹትን ፡ ሁሉ ፡ ትለምኑላችሁ ፡ ይሆንላችሁማል ። በዚኽ ፡ ይመሰገናል ፡ አባቴ ፡ እጅግ ፡ ፍሬ ፡ ታፈሩ ፡ ዘንድ ። ደቀ ፡ መዛሙርቴም ፡ ትሆናላችሁ ። አብ ፡ እንደ ፡ ወደደኝ ፡ እንዲሁም ፡ እኔ ፡ ወደድኋችሁ ። በውዴ ፡ ኑሩ ። ትእዛዜን ፡ የጠበቃችሁ ፡ እንደሆን ፡ በውዴ ፡ ትኖራላችሁ ። እኔም ፡ ያባቴን ፡ ትእዛዝ ፡ እንደ ፡ ጠበቅሁ ፡ በውዴም ፡ እንደምኖር ። ይህችን ፡ ነገርኋችሁ ፡ ደስታዬ ፡ በላንት ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡ ደስታችሁም ፡ ትፈጸም ፡ ዘንድ ።

---

## የቅዱስ ፡ ፊልጶስና ፡ የቅዱስ ፡ ያዕቆብ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተን ፡ በውነት ፡ ማወቅ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ነውና ። ልጅህን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ እርሱ ፡ መንገድ ፡ እውነትም ፡ ሕይወትም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፈጽመን ፡ እናወቅ ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠን ፡ የቅዱሳን ፡ ሐዋርያትህ ፡ የቅዱስ ፡ ፊልጶስና ፡ የቅዱስ ፡ ያዕቆብ ፡ ፈለጋቸውን ፡ ተከትለን ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ሕይወት ፡ የሚወስደውን ፡ መንገድ ፡ ጸንተን ፡ እንድንመላለስ ፡ በርሱ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### የመልእክት ፡ ክፍል ። ያዕቆብ ፡ ፩፤ ፩፤—፲፪።

ያዕቆብ ፡ የእግዚአብሔርና ፡ የጌታ ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡



ባርያ ። ለተበተኑ ፡ ላሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገድ ። ደስ ፡ ይበላችሁ ። ልዩ ፡ ልዩ ፡ ፈተና ፡ ሲደረስባችሁ ፡ ጊዜ ፡ በደስታ ፡ ሁሉ ፡ ቍጠሩት ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ። አውቃችሁ ፡ የሃይማኖታችሁ ፡ መፈተን ፡ ትዕግሥት ፡ እንዲያደርግላችሁ ። ለትዕግሥትም ፡ ፍጹም ፡ ስራ ፡ ይሆንላታል ። ፍጹማን ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ምሉአንም ፡ ከማናቸውም ፡ ሳትጐሉ ። ማንም ፡ ከላንት ፡ ጥበብ ፡ ቢጐድለው ፡ ለሁሉ ፡ ሳይለይ ፡ የሚሰጠውን ፡ የማይላገድንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይለምን ። በሃይማኖት ፡ ግን ፡ ይለምን ፡ ሳይጠራጠርም ። ተጠራጥሮ ፡ የሚለምን ፡ ንፋስ ፡ የምትመታውን ፡ የምትመልሰውም ፡ የባሕርን ፡ ሞገድ ፡ ይመስላልና ። ለዚያም ፡ ሰው ፡ ከእግአዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አንዳችን ፡ የሚወስድ ፡ አይምሰለው ። ሁለት ፡ ልብ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ የጸና ፡ አይደለውም ። የተዋረደውም ፡ ወንድም ፡ በከፍታው ፡ ይመካ ። ባለጠጋ ፡ ግን ፡ በትሕትናው ። እንደ ፡ ሣዕር ፡ አበባ ፡ ያልፈልና ። ፀሐይ ፡ ትወጣለችና ፡ ከትኩሳት ፡ ጋራ ። ሣዕሩም ፡ ይደርቃል ፡ አበባውም ፡ ይረግፋል ። የመልኩም ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ይጠፋል ። እንዲሁም ፡ ይረግፋል ፡ ባለጠጋው ፡ በመንገዱ ። በመከራ ፡ የሚታገሥ ፡ ሰው ፡ ብፁዕ ፡ ነው ። ከተፈተነ ፡ በኋላ ፡ የሕይወትን ፡ አክሊል ፡ ይወስዳልና ። እግዚአብሔር ፡ ለሚወዱት ፡ ተስፋ ፡ ያስደረገበቱን ።

### የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፲፬፤ ፩፤—፲፬።

ልባችሁ ፡ አይደንግጥ ። በእግዚአብሔር ፡ ታምናላችሁ ፡ በኔም ፡ እመኑ ። ባባቴ ፡ ቤት ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ማደርያ ፡ አለ ። ያስ ፡ ባይሆን ፡ ባልኋችሁ ፡ ነበርሁ ። ቦታውን ፡ አዘጋጅላችሁ ፡ ዘንድ ፡ እሔዳለሁ ። በሔድሁም ፡ ቦታም ፡ ባዘጋጀሁላችሁ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ እመጣለሁ ፡ ወደኔም ፡ እወስዳችኋለሁ ። እኔ ፡ ወደለሁበት ፡ እላንትም ፡ ደግሞ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ። እኔም ፡ ወዴት ፡ እንድሔድ ፡ ታውቃላችሁ ፡ መንገዱንም ፡ ታውቃላችሁ ። ቶማስ ፡ አለው ። ጌታ ፡ ሆይ ፡ ወዴት ፡ እንድትሔድ ፡ አናውቅም ። እንዴት ፡ እንችላለን ፡

መንገዱን : እናውቅ : ዘንድ :: የሱስም : አለው :: እኔ : መንገድ : ነኝ : እውነትመ : ሕይወትም :: ማንም : ወደ : አብ : አይመጣም : በኔ : እንጂ :: እኔን : ብታውቁኝስ : አባቴንም : ደግሞ : ባወቃችሁ :: ከንግዲህ : ወዲኽም : ታውቁታላችሁ : ፈጽማችሁም : አያችሁት :: አለው : ፊልጶስ :: ጌታ : ሆይ : አብን : አስየንና : ይበቃናል :: አለው : የሱስ :: እኔ : ይህነን : ያህል : ዘመን : ከላንት : ጋራ : ነኝ : አታውቀኝምን : ፊልጶስ : ሆይ :: እኔን : ያየ : አብን : ፈጽሞ : አየ :: እንዴትም : ትላለኽ : አንተ :: አብን : አስየኝ :: እኔ : በአብ : እንደለሁ : አብም : በኔ : አታምንምን :: ለላንት : የምነግራችሁትን : ነገር : ከኔ : ዘንድ : አውጥቼ : አልናገርም : በኔም : ያደረብኝ : አብ : እርሱ : ስራውን : ደግሞ : ይሰራል : እንጂ :: በኔ : እመኑ : እኔ : በአብ : እንደለሁ : አብም : በኔ :: ባይሆን : ስለ : ስራዬ : በኔ : እመኑ :: እውነት : እውነት : እላችኋለሁ :: የሚያምንብኝ : እኔ : የምሰራትን : ስራ : እርሱ : ደግሞ : ያደርጋል :: ከርስዋም : የበለጠቸውን : ያደርጋል :: እኔ : ወደባቴ : እሔዳለሁና :: በስሜም : የለመናችሁትን : ሁሉ : እርሱን : አደርገዋለሁ :: አባት : በልጅ : ይመሰገን : ዘንድ :: ምንም : በስሜ : ብትለምኑ : እኔ : አደርገዋለሁ ::

### የቅዱስ : በርናበስ : የሐዋርያ : በዓል ::

#### ጸሎት ::

ሁሉን : የምትችል : እግዚአብሔር : አምላክ : ሆይ :: አንተ : ቅዱስ : ሐዋርያህን : በርናበስን : በመንፈስ : ቅዱስ : በልዩ : ልዩ : ስጥወታው : እንደ : ለበስህው : እንዴሁም : እኛ : እንለምንሃለን : ከተለያየው : ስጥወታህ : ባድ : ኑረን : አታሳድረን : ጸጋም : ጨምርልን : ለክብርህና : ለምስጋናህ : ወትሮ : እንረባው : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::



#### በመልእክት : ፈንታ :: የሐዋርያት : ስራ : ፲፩፥ ፳፪—፴፡፡

ወሬውም : ስለርሳቸው : ተሰማ : በየሩሳሌም : ባለች : በቤት : ክርስቲያን : ጆሮ : ሁሉ :: በርናባስንም : ሰደዱት : ወደ : አንጾኪያ : ይሔድ : ዘንድ :: እርሱም : በመጣ : ጊዜ : የእግዚአብሔርንም : ጸጋ : ባየ : ጊዜ : ደስ : አለው :: ሁሉንም : መከራቸው : በልባቸው : ፈቃድ : በጌታ : ይኖሩ : ዘንድ :: እርሱ : ደህና : ሰው : ነበረና : መንፈስ : ቅዱስም : የመላበት : ሃይምኖትም :: እጅግ : ሰዎችም : ለጌታ : ተጨመሩ :: በርናባስም : ወደ : ጠርሴስ : ወጣ : ሳውልን : ሊሻ :: ባገኘውም : ጊዜ : ወደ : አንጾኪያ : ይዞት : መጣ :: እርሳቸውም : አንድ : አመት : በቤት : ክርስቲያን : ተሰበሰቡ : እጅግ : ሰዎችንም : አስተማሩ :: በአንጾኪያም : አስቀድሞ : ደቀ : መዛሙርት : ክርስቲያን : ተባሉ :: በዚያችም : ወራት : ነቢያት : ከየሩሳሌም : ወደ : አንጾኪያ : ወረዱ :: ከርሳቸውም : አንዱ : ተነሣ : ስሙን : አጋቦስ : የሚሉት :: በመንፈስ : ቅዱስም : ተናገረ : ታላቅ : ራብ : እንዲሆን : በዓለም : ሁሉ :: እርሱም : የሆነ : በአቅሎድዮስ : በቄሣር : ዘመን :: ደቀ : መዛሙርትም : የተቻላቸውን : ከርሳቸው : ኢያንዳንዱ : ሰሩ : ማገልገል : ይሰዱ : ዘንድ : በይሁዳ : ላሉት : ወንድሞች :: ይህነንም : አደረጉ :: ወደ : ሽማግሎችም : ሰደዱት : በበርናባስና : በሳውል : እጅ ::

#### የወንጌል : ክፍል :: ዮሐንስ : ፲፭፥ ፲፪—፲፯፡፡

ይህች : ትእዛዜ : ናት : እርሱ : በርሳችሁ : ትወዱ : ዘንድ : እኔ : እንደ : ወደድኋችሁ :: ከዚህ : የበለጠ : ፍቅር : የለም : ማንም : ነፍሱን : ይለውጥ : ዘንድ : ስለ : ወዳጆቹ :: እላንት : ወዳጆቼ : ናችሁ : ያዘዝኋችሁን : ሁሉ : ብታደርጉ :: እንግዲህም : ባሮች : አልላችሁም :: ባርያ : ጌታው : የሚያደርገውን : አያውቅምና :: እላንትን : ግን : ወዳጆቼ : አልኋችሁ :: ካባቴ : የሰማሁትን : ሁሉ : አስታውቅያችኋለሁና :: እላንት : አልመረጣችሁኝም :: እኔ : እላንትን : መረጥኋችሁ : እንጂ :: አኖርኋችሁም : ትሔዱ : ዘንድ :

ፍሬም ፡ ታፈራ ፡ ዘንድ ፡ ፍርያቸሁም ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ። በስሜም ፡ የምትለምኑትን ፡ ሁሉ ፡ አብ ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ።

---

## የቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ የመጥመቅ ፡ በዓል ።

### ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ዮሐንስ ፡ መጥመቅ ፡ ባርያህ ፡ እንደ ፡ ዘላለም ፡ ምክርህ ፡ ተአምራት ፡ ሁኖ ፡ ተወለደ ፡ ንስሐ ፡ መግባትንም ፡ ሰብኮ ፡ ለልጅህ ፡ ለመድኃኒታችን ፡ መንገዱን ፡ ያበጅ ፡ ዘንድ ፡ ተላከ ። እኛንም ፡ ትምህርቱንና ፡ ቅዱስ ፡ አካሔዱን ፡ እንዲህ ፡ አስከተልን ፡ እንደ ፡ ስብከቱ ፡ በውነት ፡ ንስሐ ፡ እንድንገባ ፡ እንደ ፡ ምሳሌውም ፡ ወትሮ ፡ እውነትን ፡ በመናገር ፡ እንድንጸና ፡ ኃጢአትንም ፡ በድፍረት ፡ እንድንገሥጽ ፡ በውነት ፡ መክንያትም ፡ በሚመጣብን ፡ በመከራ ፡ እንድንታገሥ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

### በመልእክት ፡ ፈንታ ። ኢሳይያስ ፡ ፵፥ ፩—፲፩።

አጽናኑ ፡ ሕዝቤን ፡ አጽናኑ ፡ ይላል ፡ አምላካችሁ ። ለየሩሳሌም ፡ ልብ ፡ ተናገሩ ፡ ጽሩባትም ፡ የጦር ፡ ዘመንዋ ፡ እንደ ፡ ተፈጸመ ፡ ኃጢአትዋም ፡ እንደ ፡ ቀረችላት ። ከእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ስለ ፡ ኃጢአትዋ ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ ዕጽፍ ፡ ተቀብላለችና ። ያዋጅ ፡ ነጋሪ ፡ ቃል ፡ በምድረ ፡ በዳ ። የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ አብጁ ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ ላምላካችን ፡ የንጉሥን ፡ መንገድ ፡ አስተካክሉ ። ቆላ ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ትበል ፡ ተራራውና ፡ ኮረፍታውም ፡ ሁሉ ፡ ዝቅ ፡ ይበል ፡ አቀበትም ፡ ይቅና ፡ ደጋም ፡ ሜዳ ፡ ይሁን ። የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ትገለጣለችና ፡ ሥጋም ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ ያዩታል ፡ የእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ይኸነን ፡ ተናግርዋልና ። የሚል ፡ ቃል ፡ ጽራ ፡ ይላል ። አለም ፡ በምን ፡ እጸራለሁ ። ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ሣር ፡ ነው ፡ መልካምነቱም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ በረኻ ፡ አበባ ። ሣርስ ፡ ደረቀ ፡ አበባውም ፡ ረገፈ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ነፍሶበታልና ። በውነት ፡ ሕዝቡ ፡ ሣዕር ፡ ነው ። ሣዕር ፡ ደረቀ ፡ አበባውም ፡ ረገፈ ፡ ያምላካችነም ፡ ነገር ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለች ። ጽዮን ፡ ሆይ ፡ በጎ ፡ የምስራችን ፡ የምትነግሪ ፡ ከፍ ፡ ባለው ፡ ተራራ ፡ ውጭ ። ድምፅሽንም ፡ በኃይል ፡ አንሺ ። የሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ በጎ ፡ የምስራችን ፡ የምትነግሪ ። አንሺ ፡ አትፍሪ ፡ ለይሁዳም ፡ አገር ፡ እነሆ ፡ አምላካችሁ ፡ በዪ ። እነሆ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ በኃይል ፡ ይመጣል ፡ ክንዱም ፡ ይገዛለታል ። እነሆ ፡ ደመወዜው ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡ ምግባሩም ፡ በፊቱ ፡ ነው ። እንደ ፡ እረኛ ፡ በጎቹን ፡ ይጠብቃል ። በክንዱ ፡ ጥቦቶቹን ፡ ይሰበስባል ፡ በብብቱም ፡ ይሸከማቸዋል ። እርጉዞችንም ፡ እርሱ ፡ ይመራል ።



### የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፩፥ ፶፯—፹።

ኤልሳቤጥ ፡ ግን ፡ ወራትዋ ፡ ልትወልድ ፡ ደረሰ ። ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ። ጎረቤቶችዋም ፡ ዘመዶችዋም ፡ ሰሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሕረቱን ፡ እንደገነነላት ። ከርስዋ ፡ ጋራም ፡ ደስ ፡ አላቸው ። በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ሕፃኑን ፡ ሊገዝሩት ፡ መጡ ። ባባቱ ፡ ስምም ፡ ዘካርያስ ፡ አሉት ። እናቱም ፡ መለሰች ፡ አለችም ፡ አይደለም ። ነገር ፡ ግን ፡ ዮሐንስ ፡ ይባላል ። አልዋትም ። ከዝምድናሽ ፡ ማንም ፡ በዚኸ ፡ ስም ፡ የሚባል ፡ አይገኝም ። አባቱንም ፡ ጠቀሱት ፡ ምን ፡ ይወደል ፡ ይጸሩት ፡ ዘንድ ፡ ብለው ። የሚጻፍበትንም ፡ ጽላ ፡ እሻ ፡ ጻፈም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ። ስሙ ፡ ዮሐንስ ፡ ነው ። ሁሉም ፡ አደነቁ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አፉ ፡ ተከፈተ ፡ መላሱም ፡ ተፈታ ። እግዚአብሔርንም ፡ ኢያመሰገነ ፡ ተናገረ ። ፍርሃትም ፡ በጎረቤቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ሆነ ። በይሁዳም ፡ ደጋ ፡ ሁሉ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ወጣ ። የሰሙትም ፡ በልባቸው ፡ አሰቡ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ። እንጃ ፡ ይህ ፡ ሕፃን ፡ ምን ፡ ይሆናል ። የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበረችና ። ዘካርያስም ፡ አባቱ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ መላ ፡ እንዲህ ፡ ሲልም ፡ ተናገረ ። የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ። ወገኑን ፡ ጕብኝትዋልና ፡ ለርሳቸውም ፡ መድኃኒት ፡ አድርጓልና ። የመድኃኒትንም ፡ ቀንድ ፡ አስነሣልን ፡ በባርያው ፡ በዳዊት ፡

ቤት ፡፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በነበረት ፡ በቅዱሳን ፡ ነቢያቱ ፡ ባፋቸው ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡፡ ከጸላቶቻችን ፡ ያድነን ፡ ዘንድ ፡ ከሚጸሉነም ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡፡ ምሕረቱን ፡ ካባቶቻችን ፡ ጋራ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡፡ የተቀደሰውንም ፡ ኪዳኑን ፡ ያስብ ፡ ዘንድ ፡፡ ለአብርሃምም ፡ ላባታችን ፡ የማለለቱን ፡ መሐላውን ፡፡ ከጸላቶቻችን ፡ እጅ ፡ በደነ ፡ ጊዜ ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡፡ ያለ ፡ ፍርሃት ፡ እናገለግለው ፡ ዘንድ ፡ በውነት ፡ በጽድቅም ፡ በፊቱ ፡ የድሚያችነን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡፡ አንተም ፡ ሕፃን ፡ ሆይ ፡ የልዑል ፡ ነቢይ ፡ ትባላለኽ ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትሔደለኽና ፡ መንገዱን ፡ ልታበጅለት ፡፡ የመድኃኒቱንም ፡ እውቀት ፡ ለወገኑ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ በኃጢአታቸው ፡ ስርየት ፡፡ ባምላካችን ፡ መራራት ፡ በምሕረቱም ፡ እኛን ፡ በርስዋ ፡ የጐበኘን ፡ ከላይ ፡ የወጣልን ፡ ብርሃን ፡፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፡ በጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጽላ ፡ ለተቀመጡት ፡፡ እግሮቻችነንም ፡ በሰላም ፡ መንገድ ፡ ያቀና ፡ ዘንድ ፡፡ ሕፃኑም ፡ ያድግ ፡ ነበረ ፡ በመንፈስም ፡ ይጸናል ፡፡ በምድረ ፡ በደም ፡ ነበረ ፡ ለእሥራኤል ፡ እስኪታደበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡፡

---

## የቅዱስ ፡ ጴጥሮስ ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ለሐዋርያህ ፡ ለቅዱስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩን ፡ የጸጋህን ፡ ስጥወታ ፡ ሰጥተህ ፡ መንጋህን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ በብርቱ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ አዘዝሀው ፡ እንደ ሁም ፡ እንለምንሃለን ፡ ኤጲቆጶሳትንና ፡ ቀሳውስትን ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ቃልህን ፡ አስብካቸው ፡ ሕዝብንም ፡ በጣም ፡ ይከተሉት ፡ ዘንድ ፡ እሺ ፡ አሰኛቸው ፡ ሁላቸው ፡ የዘላለምን ፡ ክብር ፡ አክሊል ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፲፪፥ ፩—፲፩፡፡

በዚያም ፡ ዘመን ፡ ሄሮድስ ፡ ንጉሥ ፡ እጁን ፡ ጫነ ፡ በቤት ፡



ክርስቲያን ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡፡ ያዕቆብንም ፡ የዮሐንስን ፡ ወንድም ፡ በሰይፍ ፡ ገደለ ፡፡ ያም ፡ አይሁድን ፡ ደስ ፡ እንደ ፡ አሰኛቸው ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ጨመረበት ፡ ጴጥሮስን ፡ ሊይዝ ፡ ደግሞ ፡፡ የበዓለ ፡ ፋእትም ፡ ወራት ፡ ነበረ ፡፡ በያዘውም ፡ ጊዜ ፡ በግዞት ፡ አስቀመጠው ፡፡ ላራት ፡ ጭፍሮችም ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ፡ ይጠብቁት ፡ ዘንድ ፡ ከፋሲካ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ ያወጣው ፡ ዘንድ ፡ ፈቃዱ ፡ ነበረና ፡፡ ጴጥሮስም ፡ በግዞት ፡ ይጠበቅ ፡ ነበረ ፡፡ ጸሎትም ፡ ሁለግዜ ፡ ስለርሱ ፡ በቤት ፡ ክርስቲያን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆነች ፡፡ ሄሮድስም ፡ ወደርሳቸው ፡ ያወጣው ፡ ዘንድ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ጴጥሮስ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፡ በሁለት ፡ ወታደሮች ፡ መኻከል ፡ በሁለት ፡ ሰንሰለት ፡ ታሥሮ ፡፡ ጠባቆችም ፡ በደጁ ፡ ፊት ፡ የግዞቱን ፡ ቤት ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፡፡ እነሆም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ወደርሱ ፡ መጣ ፡ ብርሃንም ፡ በስፍራው ፡ በራ ፡፡ የጴጥሮስንም ፡ ጎን ፡ መታ ፡ አስነሣውም ፡፡ እንደዬህ ፡ ሲል ፡፡ ፈጥነኽ ፡ ተነሣ ፡፡ ሰንሰለቶቹም ፡ ከጁ ፡ ወደቁ ፡፡ መልአክም ፡ አለው ፡፡ ታጠቅ ፡ ጫማኽንም ፡ ልበስ ፡፡ እንዲሁም ፡ አደረገ ፡፡ አለውም ፡፡ ልብስኽን ፡ ልበስና ፡ ተከተለኝ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ ተከትሎት ፡ ወጣ ፡፡ በመልአኩም ፡ የሚደረገው ፡ ነገር ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቀም ፡፡ ራእይን ፡ የሚያይ ፡ ይመስለው ፡ ነበረ ፡ እንጅ ፡፡ መጀመርያውንም ፡ መጥበቅያ ፡ ባለፉ ፡ ጊዜ ፡ ሁለተኛውንም ፡ ወደገር ፡ ወደሚወስደው ፡ ወደ ፡ ብረቱ ፡ ደጅ ፡ ደረሱ ፡፡ እርሱም ፡ በገዛጁ ፡ ተከፈተላቸው ፡፡ በወጡም ፡ ጊዜ ፡ አንዲንም ፡ መንገድ ፡ በሔዱ ፡ ጊዜ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ መልአኩ ፡ ከርሱ ፡ ራቀ ፡፡ ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡ ልቡ ፡ ተመለሰ ፡፡ አለም ፡፡ አሁን ፡ በውነት ፡ አወቅሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ መልአኩን ፡ እንደ ፡ ላከ ፡ ከሄሮድስም ፡ እጅ ፡ የአይሁድ ፡ ወገንም ፡ ካሰቡት ፡ ሁሉ ፡ እንደዳነኝ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፲፮፥ ፲፫—፲፱፡፡

የሱስም ፡ ወደ ፡ ቂሳርያ ፡ ወደ ፡ ፊልጶስ ፡ አገር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ጠየቀ ፡ እንደዬህ ፡ ብሎ ፡፡ ማነ

ው ፡ ይላሉ ፡ ሰዎች ፡ እኔን ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡፡ እርሳቸውም ፡
አሉ ፡፡ መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ ነው ፡ የሚሉኽ ፡ አሉ ፡፡ እኵሉ
ም ፡ ኤልያስ ፡፡ እኵሉም ፡ ኤርምያስ ፡ ወይም ፡ አንዱን ፡
ከነቢያት ፡፡ አላቸውም ፡ እላንተስ ፡ ምን ፡ ትላላችሁ ፡ እ
ኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡፡ ሲሞን ፡ ጴጥሮስም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡፡
አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ነኽ ፡ የሕያው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡፡
የሱስም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለው ፡፡ ምስጉን ፡ ነኽ ፡ ሲ
ሞን ፡ ሆይ ፡ የዮና ፡ ልጅ ፡፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ ይህነን ፡ አልገለጸ
ልኽምና ፡፡ የሰማዩ ፡ አባቴ ፡ እንጂ ፡፡ እኔም ፡ እልኻለሁ ፡፡
አንተ ፡ የደንጊያ ፡ ሰው ፡ ነኽ ፡፡ በዚቺም ፡ ደንጊያ ፡ ላይ ፡ ቤ
ተ ፡ ክርስቲያኔን ፡ እሠራለሁ ፡፡ የገሃነምም ፡ ደጆች ፡ አይበ
ርቱባትም ፡፡ የመንግሥተ ፡ ሰማያትንም ፡ መክፈቻ ፡ እሰ
ጥኻለሁ ፡፡ በምድርም ፡ የምታሥረው ፡ ሁሉ ፡ በሰማያት
ም ፡ የታሠረ ፡ ይሆናል ፡፡ በምድርም ፡ የምትፈታው ፡ ሁሉ ፡
በሰማያትም ፡ የተፈታ ፡ ይሆናል ፡፡

## የቅዱስ ፡ ያዕቆብ ፡ የሐዋርያ ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ቅዱስ ፡ ሐዋርያህ ፡ ያዕቆብ ፡
አባቱንና ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉን ፡ ትቶ ፡ ሳይዘገይም ፡ ለልጅህ ፡
ለየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መጽሪት ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተከ
ተለው ፡ እንዲሁም ፡ ልባችንን ፡ አዘንብልልን ፡ እኛ ፡ የዓለ
ምን ፡ የሥጋንም ፡ መውደድ ፡ ሁሉ ፡ ትተን ፡ ወትሮ ፡ የተዘ
ጋጀነ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ የተቀደሱትን ፡ ትእዛዛትህ ፡ ለመ
ከተል ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፲፩ ፡ ፳፯—፲፪ ፡ ፫ ፡፡
በዚያችም ፡ ወራት ፡ ነቢያት ፡ ከየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ አንጾ
ኪያ ፡ ወረዱ ፡፡ ከርሳቸውም ፡ አንዱ ፡ ተነሣ ፡ ስሙን ፡ አጋ
ቦስ ፡ የሚሉት ፡፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ተናገረ ፡ ታላቅ ፡ ራ
ብ ፡ እንዲሆን ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡፡ እርሱም ፡ የሆነ ፡ በአቅ
ሎድዮስ ፡ በቄሣር ፡ ዘመን ፡፡ ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ የተቻ



ላቸውን ፡ ከርሳቸው ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰሩ ፡ ማገልገል ፡ ይሰ
ዱ ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳ ፡ ላሉት ፡ ወንድሞች ፡፡ ይህነንም ፡ አደ
ረጉ ፡፡ ወደ ፡ ሽማግሎችም ፡ ሰደዱት ፡ በበርናባስና ፡ በሳው
ል ፡ እጅ ፡፡ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ሄሮድስ ፡ ንጉሥ ፡ እጁን ፡ ጫ
ነ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡፡
ያዕቆብንም ፡ የዮሐንስን ፡ ወንድም ፡ በሰይፍ ፡ ገደለ ፡፡ ያ
ም ፡ አይሁድን ፡ ደስ ፡ እንደ ፡ አሰኛቸው ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ጨ
መረበት ፡ ጴጥሮስን ፡ ሊይዝ ፡ ደግሞ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ማቴዎስ ፡ ፳ ፡ ፳—፳፰ ፡፡
የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የዘብደዎስ ፡ የልጆቹ ፡ እናት ፡ ወደርሱ ፡
መጻች ፡ ከልጆችዋ ፡ ጋራ ፡ ስትሰግድለት ፡ ከርሱም ፡ አንድ ፡
ነገርን ፡ ስትሻ ፡፡ እርሱም ፡ አላት ፡፡ ምን ፡ ትሻለሽ ፡፡ እርስ
ዋም ፡ አለችው ፡፡ በል ፡ እሌኽ ፡ ሁለት ፡ ልጆቼ ፡ በመንግሥ
ትኽ ፡ እንዲቀመጡ ፡ አንደኛው ፡ በቀኝኽ ፡ ሁለተኛውም ፡
በግራኽ ፡፡ የሱስም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡፡ የምትለምኑትን ፡
አታውቁም ፡፡ እኔ ፡ እጠጣው ፡ ዘንድ ፡ ጊዜ ፡ ያለኝን ፡ ጽዋ
ውን ፡ ትጠጡ ፡ ዘንድ ፡ ትችላላችሁን ፡፡ እኔም ፡ የምጠመ
ቀውን ፡ ጥምቀት ፡ ትጠመቁ ፡ ዘንድ ፡፡ አሉት ፡ እንችላለ
ን ፡፡ አላቸውም ፡፡ ጽዋዬን ፡ ትጠጣላችሁ ፡ እኔም ፡ የምጠ
መቀውን ፡ ጥምቀቴን ፡ ትጠመቃላችሁ ፡፡ በቀኜና ፡ በግራዬ ፡
መቀመጥ ፡ ግን ፡ የምሰጠው ፡ የለኝም ፡፡ ካባቴ ፡ ዘንድ ፡ ለ
ተዘጋጀላቸው ፡ እንጂ ፡፡ አሥሩም ፡ ሰምተው ፡ ሁለቱን ፡ ወ
ንድማማች ፡ ተቈጥዋቸው ፡፡ የሱስም ፡ ጸራቸው ፡ አለ
ም ፡፡ የአሕዛብ ፡ ገዦች ፡ እንዲገዟቸው ፡ ታላቆቻቸው
ም ፡ እንዲሠለጥኑባቸው ፡ አወቃችሁ ፡፡ ለላንተ ፡ ግን ፡ እ
ንዲሁ ፡ አይሆንም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ በላያችሁ ፡ ታላቅ ፡ መሆን ፡
የሚወድ ፡ ሎሌ ፡ ይሁናችሁ ፡፡ በላንተም ፡ በፊት ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ የወደደ ፡ ባርያችሁ ፡ ይሁናችሁ ፡፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሊ
ያገለግሉት ፡ እንደልመጣ ፡ ሊያገለግል ፡ እንጂ ፡ ነፍሱንም ፡
አሳልፎ ፡ ሊሰጥ ፡ ለብዙ ፡ ቤዛ ፡፡

## የቅዱስ ፡ በርተሎሜዎስ ፡ የሐዋርያ ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ ለሐዋርያህ ፡ ለበርተሎሜዎስ ፡ በቃልህ ፡ በውነት ፡ ያምን ፡ ዘንድ ፡ ይሰብክበትም ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፡ እንዲሁም ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ስጥ ፡ እንለምንሃለን ፡ እርሱ ፡ ያመነበቱን ፡ ቃል ፡ ታምን ፡ ዘንድ ፡ ትሰብከውም ፡ ዘንድ ፡ ትቀበለውም ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ሥራ ፡ ፭፤ ፲፪፤—፲፯፤፤

በሐዋርያትም ፡ እጅ ፡ እጅግ ፡ ተአምራትና ፡ ድንቅ ፡ በሕዝቡ ፡ ማኸል ፡ ሆነ ፡፡ ሁሉም ፡ ባንድ ፡ ነበሩ ፡ በሰሎሞን ፡ አደራሽ ፡፡ ከቀሩትም ፡ አንድም ፡ ይቀርብላቸው ፡ ዘንድ ፡ የሚደፍር ፡ አልነበረም ፡፡ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ያከብራቸው ፡ ነበር ፡፡ በጌታም ፡ የሚያምኑ ፡ ብዙ ፡ ተጨመሩላቸው ፡ ከወንደችና ፡ ከሴቶች ፡ ታላቅ ፡ ቍጥር ፡፡ ድውያንን ፡ ባደባባይ ፡ እስኪያወጡ ፡ ድረስ ፡ ባልጋም ፡ በቃሬዛም ፡ አኖርዋቸው ፡፡ ጴጥሮስ ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ጽላው ፡ባንደንደቸው ፡ ላይ ፡ ይወድቅ ፡ ዘንድ ፡፡ እጅግም ፡ ሰዎች ፡ በዙርያ ፡ ካሉችው ፡ አገር ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፡፡ ድውያንንም ፡ ርኩስ ፡ ጋኔንም ፡ ያለባቸውን ፡ አመጡ ፡ ሁሉም ፡ ተፈወሱ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ሉቃስ ፡ ፳፪፤ ፳፬፤—፴፤፤

በመኻከላቸውም ፡ ደግሞ ፡ ክርክር ፡ ነበረ ፡ ከርሳቸው ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚመስለው ፡ ብለው ፡፡ እርሱ ፡ ግን ፡ አላቸው ፡፡ የአሕዛብ ፡ ነገሥታት ፡ እርሳቸው ፡ ይገዙዋቸዋል ፡፡ የነገሡባቸውም ፡ ቸርነት ፡ አድራጎች ፡ ይባላሉ ፡፡ እላንት ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከላንት ፡ ታላቁ ፡ እንደ ፡ ታናሽ ፡ ይሁን ፡ አለቃውም ፡ እንደ ፡ ሎሌ ፡፡ ማናቸውም ፡ ይበልጥ ፡፡ ተቀምጦ ፡ የሚበላውን ፡ ወይስ ፡ ቁሞ ፡ የሚያገለግለው ፡፡ ተቀምጦ ፡ የሚበላው ፡ አይደለምን ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ በመኻከላችሁ ፡ እንደ ፡ ሎሌ ፡ ነኝ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እላን



ት ፡ ናችሁ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ በመከራዬ ፡ የታገሣችሁ ፡፡ እኔም ፡ መንግሥትን ፡ አዘጋጅላችኋለሁ ፡ አባቴ ፡ ለኔ ፡ እንደ ዘጋጀት ፡፡ ትበሉ ፡ ትጠጡም ፡ ዘንድ ፡ በማዕዴ ፡ በመንግሥቴ ፡፡ ባሥራ ፡ ሁለትም ፡ ዙፋኖች ፡ ትቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ ባሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ነገደ ፡ እሥራኤል ፡ ትፈርዱ ፡ ዘንድ ፡፡

## የቅዱስ ፡ ማቴዎስ ፡ የሐዋርያ ፡ በዓል ፡፡

### ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ በተባረከ ፡ ልጅህ ፡ ማቴዎስን ፡ ሐዋርያና ፡ ወንጌላዊ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከቀረጥ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጸራሀው ፡ እንዲሁም ፡ ለኛ ፡ ጸጋ ፡ ስጠን ፡ የከብትን ፡ መሻት ፡ ያለ ፡ ሥርዓትም ፡ ያለውን ፡ የባለጠግነትን ፡ መውደድ ፡ ትተን ፡ ልጅህን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ እንከተል ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ የሚኖር ፡ የሚገዛም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፪፤ ቆሮንቶስ ፡ ፬፤ ፩፤—፯፤፤

ስለዚኽም ፡ ይኽች ፡ መልእክተ ፡ ተሰጥታናለችና ፡ ምህረትን ፡ እንደ ፡ ተቀበልነ ፡ አንደክምም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ የሚያሳፍረውን ፡ መሠወር ፡ ከደነ ፡፡ በተንኰልም ፡ አንሔድም ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ነገር ፡ አንሸነግልም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እውነቱን ፡ በመግለጽ ፡ ራሳችነን ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ሕሊና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንገልጣለን ፡፡ ወንጌላችን ፡ ግን ፡ የተሠወረች ፡ ብትሆን ፡ ከጠፉ ፡ ሰዎች ፡ የተሠወረች ፡ ናት ፡፡ በርሳቸውም ፡ ዘንድ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ አምላክ ፡ የማያምኑትን ፡ ልብ ፡ አሳወረ ፡፡ የክርስቶስ ፡ የክብሩ ፡ ወንጌል ፡ ብርሃን ፡ እንደያበራላቸው ፡ እርሱም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምሳሌ ፡፡ እኛ ፡ በራሳችን ፡ የምንሰብክ ፡ አይደለነምና ፡፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ እንጂ ፡፡ ራሳችነን ፡ ግን ፡ ለላንት ፡ ባሮች ፡ እናደርጋለን ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ከጨለማ ፡ ብርሃን ፡ ይወጣ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዘ ፡፡ እርሱ ፡ በልባች

ን : ብርሃን : ሰጥተልናልና : የእግዚአብሔርን : የክብሩን : ዕውቀት : ለማብራት : በየሱስ : ክርስቶስ : ፊት ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፱፥ ፱—፲፫ ::

የሱስም : ከዚያ : ባለፈ : ጊዜ : በቀረጥ : የተቀመጠውን : ሰው : አየ : ስሙን : ማቴዎስ : የሚሉት :: አለውም : ተከተለኝ :: ተነሥቶም : ተከተለው :: በቤቱም : ለምሳ : ተቀምጦ : ሳለ : እነሆ : ብዙ : ቀራጮችና : ኃጢአተኞች : መጡ : ለምሳም : ተቀመጡ : ከየሱስና : ከደቀ : መዛሙርቱ : ጋራ :: ፈሪሳውያንም : አይተው : ደቀ : መዛሙርቱን : አሉ :: ለምን : መምህራችሁ : ከቀራጮችና : ከኃጢአተኞች : ጋራ : ይበላል :: የሱስም : በሰማ : ጊዜ : አላቸው :: ባለ : ጤኖች : ባለ : መድኃኒትን : አይሹም :: ድውያን : እንጅ :: ሒዱ : ግን : ተማሩም : ይኸ : ምንድር : ነው : ምህረትን : እፈልጋለሁ : መሥዋዕትም : አይደለም :: ጻድቃንን : ለመጽራት : አልመጣሁምና : ኃጥኣንን : እንጅ : ወደ : ንስሐ ::

## የቅዱስ : ሚካኤልና : የመላእክት : ሁሉ : በዓል ::

ጸሎት ::

የዘላለም : አምላክ : ሆይ : አንተ : የመላእክትንና : የሰዎችን : ማገልገል : ድንቅ : ባለች : ሥርዓት : ሠርተሃልና :: በምህረትህ : ስጠን : ቅዱሳን : መላእክትህ : በሰማይ : ወትሮ : እንዲገዙልህ : እንዲሁም : በፈቃድህ : እኛን : በምድር : ያገዙን : ዘንድ : ይጠብቁንም : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

በመልእክት : ፈንታ :: ራእይ : ፲፪፥ ፯—፲፪ ::

በሰማይም : ሰልፍ : ሆነ :: ሚካኤልና : መላእክቱ : ዘንዶውን : ተዋጉ :: ዘንዶውም : ተዋጋ : መላእክቱም :: አላሸነፉምም :: ከዚያ : ወዲያም : በሰማይ : ስፍራ : አልተገኘላቸውም :: ታላቁም : ዘንዶ : ተጣለ :: እርሱም : የቀደመው : እባብ : ዲያብሎስ : የሚባል : ሰይጣንም :: ዓለሙን : ሁሉ : የሚያስት :: በምድር : ላይም : ተጣለ : መላእክቱም : ከር



ሱ : ጋራ : ወደቁ :: በሰማይም : ታላቅ : ቃልን : ሰማሁ : እንዲህ : ሲል :: አሁን : ያምላካችን : መድኃኒት : ችሎቱም : መንግሥቱም :: የመሢሑም : ሥልጣን : ሆነች :: ወንድሞቻችንን : የሚያሳጣቸው : ወድቋልና :: ባምላካችን : ፊት : ያሳጣቸው : የነበረ : ሌትና : ቀን :: እርሳቸውም : ድል : ነሡበት : በበጉ : ደም : በምስክርነታቸውም : ቃል :: ነፍሳቸውንም : አልወደዱም : ለሞት : እስኪደርሱ : ድረስ :: ስለዚኸ : ደስ : ይበላችሁ : እላንት : ሰማዮች : በርሳቸውም : ያላችሁ :: በምድርና : በባሕር : ለምትኖሩ : ግን : ወዮላችሁ :: ዲያብሎስ : ወርደባችኋልና : በርሱም : ታላቅ : ቍጣ : አለበት :: ጥቂት : ዘመን : እንደ : ቀረለት : ያውቃልና ::

የወንጌል : ክፍል :: ማቴዎስ : ፲፰፥ ፩—፲ ::

በዚያች : ሰዓት : ጊዜ : ደቀ : መዛሙርቱ : ወደ : የሱስ : መጡ : እንዲህ : ሲሉ :: ማነው : በመንግሥተ : ሰማያት : የሚበልጥ :: የሱስም : ሕፃን : ጸራና : በመኻከላቸው : አቆመው :: አለም : እውነት : እላችኋለሁ :: ባትመለሱ : እንደ : ሕፃናትም : ባትሆኑ : ወደ : መንግሥተ : ሰማያት : አትገቡም :: እንደዚኸም : ሕፃን : ራሱን : የሚያዋርድ : እርሱ : ነው : በመንግሥተ : ሰማያት : የሚበልጥ :: እንዲህ : ያለውንም : ሕፃን : በስሜ : የሚቀበል : እኔን : ይቀበላል :: ከለዚኸም : ከታናሾች : በኔ : ከሚያምኑ : አንዱን : የሚያሰናክል :: የወፍጮ : ደንጊያ : ባንገቱ : ታሥሮ : ወደ : ባሕር : ጥልቅ : መሥጠም : ይሻለዋል :: ወዮ : ለዓለም : ስለ : መሰናከያ :: መሰናከያስ : በግድ : ሊመጻ : አለውና :: ነገር : ግን : ወዮለት : ለዚያ : ሰው : በርሱ : ምክንያት : መሰናከያ : የምትመጻ :: እጅኸ : ግን : እግርኸም : ብታሰናክልኸ : ቍርጠኸ : ካንተ : ጣላት :: ወደ : ሕይወት : ብትገባ : አንካሳ : ሁነኸ : ወይም : ከብልቶችህ : አንድ : ጐድሎብህ : ይሻልኻልና : ሁለት : እጅ : ሁለት : እግር : ኑሮኸ : ወደ : ዘላለም : እሳት : ክትጣል :: ዓይንኸም : ብታሰናክልኸ : አውልቀኸ : ጣላት :: ሀባል : ሁነህ : ወደ : ሕይወት :

ብትገባ ፡ ይሻልኻልና ፡ ሁለት ፡ ዓይን ፡ ኑሮኽ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
እሳት ፡ ከትጣል ። እዩ ፡ ከለዚኽ ፡ ከታናሾች ፡ አንዱን ፡ እ
ንዳትንቁ ። እላችኋለሁና ፡ መላእክታቸው ፡ በሰማዮች ፡
ሁልጊዜ ፡ የሰማዩን ፡ ያባቴን ፡ ፊት ፡ ያያሉ ።

የቅዱስ ፡ ሉቃስ ፡ የወንጌላዊ ፡ በዓል ።

ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ባለ ፡ መድ
ኃኒት ፡ የነበረውን ፡ ሉቃስን ፡ በወንጌል ፡ የከበረውን ፡ ወን
ጌላዊና ፡ የነፍስ ፡ ፈዋሽ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ የጸራሀው ። በ
ርሱ ፡ በተሰጠች ፡ በትምህርት ፡ ደህና ፡ መድኃኒት ፡ የነፍሳ
ችን ፡ በሽታ ፡ ሁሉ ፡ እንዲፈወስ ፡ ውደድ ፡ በልጅህ ፡ በየ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ምግባር ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ፪፥ ጢሞቴዎስ ፡ ፬፥ ፭—፲፰።

አንተ ፡ ግን ፡ በሁሉ ፡ ንቃ ። መከራ ፡ ተቀበል ። የወንጌላ
ዊን ፡ ስራ ፡ ስራ ። መልክትኽን ፡ ፈጸም ። እኔ ፡ እነሆ ፡ እሠ
ዋለሁና ። የመሰናበቴም ፡ ጊዜ ፡ ደርሶዋል ። መልካሙን ፡
ገድል ፡ ተጋደልሁ ። ሩጫዩንም ፡ ጨረስሁ ። ሃይማኖትንም ፡
ጠበቅሁ ። እንግዲህም ፡ የጽድቅ ፡ አክሊል ፡ ተዘጋጅቶልኛ
ል ። እግዚአብሔር ፡ ያ ፡ ጻድቅ ፡ ፈራጅ ፡ እርሱን ፡ በዚያች ፡
ቀን ፡ የሚሰጠኝ ። ለኔም ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። መገለጡን ፡
ለሚወዱ ፡ ሁሉ ፡ እንጂ ፡ ደግሞ ። ቶሎ ፡ ወደኔ ፡ ትመጣ ፡
ዘንድ ፡ ፍጠን ። ዴማስ ፡ ትቶኛልና ። ይኽንም ፡ ዓለም ፡ ወ
ድዋልና ። ወደ ፡ ተሰሎንቄም ፡ ሔደ ። ቀረስኪስም ፡ ወደ ፡
ገላትያ ። ቲቶስም ፡ ወደ ፡ ደልማጥያ ። ሉቃስ ፡ ብቻ ፡ ከኔ ፡
ጋራ ፡ ነው ። ማርቆስን ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ይዘኸው ፡ ና ። ለማገ
ልገል ፡ ይረባኛልና ። ቲኪቆስን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ላክ
ሁ ። በጠራዋስ ፡ በከርጶስ ፡ ዘንድ ፡ የተውኋትን ፡ ቡርኑስ ፡
በመጣኽ ፡ ጊዜ ፡ ይዘኻት ፡ ና ። መጻሕፍቱንም ። ይልቁን
ም ፡ በራናውን ። እስክንድሮስ ፡ የናስ ፡ አንጥረኛ ፡ እጅግ ፡
ክፉ ፡ አደረገብኝ ። እግዚአብሔር ፡ ይመልስለት ፡ እንደ ፡



ስራው ። አንተም ፡ ደግሞ ፡ ከርሱ ፡ ተጠንቀቅ ። ነገራችነን ፡
እጅግ ፡ ተጠናውትዋልና ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፥ ፩—፯።

ከዚኽም ፡ በኋላ ፡ ጌታ ፡ ሌሎችን ፡ ሰብዓ ፡ ደግሞ ፡ ለየ ።
ሁለት ፡ ሁለትም ፡ አድርጎ ፡ በፊቱ ፡ ላካቸው ፡ እርሱ ፡ ወ
ደሚሔድበት ፡ አገርና ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ። አላቸውም ፡ መከ
ሩ ፡ እጅግ ፡ ነውና ። ሰራተኞች ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ናቸው ። ወደ ፡
መከሩ ፡ ጌታ ፡ ለምኑ ፡ ለመከሩ ፡ ሰራተኞችን ፡ ያወጣ ፡ ዘ
ንድ ። ሒዱ ። እነሆ ፡ እንደ ፡ በግ ፡ በተኵላ ፡ ማኸል ፡ እሰ
ደችኋለሁ ። አቆማደውን ፡ አትያዙ ፡ ከረጢትንም ፡ ጫ
ማውንም ። በመንገድም ፡ ለማንም ፡ ሰላም ፡ አትስጡ ።
ወደምትገቡበትም ፡ ቤት ፡ አስቀድማችሁ ፡ በሉ ። ሰላ
ም ፡ ለዚኽ ፡ ቤት ። ከዚያም ፡ የሰላም ፡ ልጅ ፡ ቢኖር ፡ ሰላ
ማችሁ ፡ ያድርበታል ። ያለዚያም ፡ ሰላማችሁ ፡ ይመለስ
ላችኋል ። በዚያም ፡ ቤት ፡ ተቀመጡ ፡ በርሳቸውም ፡ ዘን
ድ ፡ ካለው ፡ ብሉ ፡ ጠጡም ። ለሰራተኛ ፡ ደመወዜው ፡ ይ
ገባዋልና ።

የቅዱስ ፡ ሲሞንና ፡ የቅዱስ ፡ ይሁዳ ፡ የሐዋርያት ፡ በዓል ።

ጸሎት ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ቤት ፡ ክር
ስቲያንህን ፡ በሐዋርያትና ፡ በነቢያት ፡ መሠረት ፡ የማዝን ፡
ራሱ ፡ ደንጊያ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ራሱን ፡ ባለው ፡ ላይ ፡ መ
ሠርተሃልና ። ጸጋህን ፡ ስጠነ ፡ እኛ ፡ በርሳቸው ፡ ትምህርት ፡
በመንፈስ ፡ አንድነት ፡ እርሱ ፡ በርሳችን ፡ እንዷህ ፡ እንሰ
ማማ ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡ የምትወደት ፡ የተቀደሰችም ፡ መቅ
ደስ ፡ እንድንሆን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የመልእክት ፡ ክፍል ። ይሁዳ ፡ ፩፥—፰።

ከይሁዳ ፡ ከየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ባርያ ፡ ከያዕቆብ ፡ ወንድ
ም ። በእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ተቀደሱ ፡ በየሱስ ፡ ክር

ስቶስም ፡ ወደ ፡ ተጠበቁ ፡ ወደ ፡ ተጸሩት ፡፡ ምሕረት ፡ ሰላምም ፡ ፍቅርም ፡ ትብዛላችሁ ፡፡ ወዳጆቼ ፡ ስለ ፡ ደኅንነት ፡ አንድነት ፡ እጽፍላችሁ ፡ ዘንድ ፡፡ እጅግ ፡ ቸኵዬ ፡ ሳለሁ ፡፡ የግድ ፡ አሉብኝ ፡ ጽፌ ፡ እመክራችሁ ፡ ዘንድ ፡ ለቅዱሳን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ለተሰጠችው ፡ ሃይማኖት ፡ እንድ ፡ ትጋደሉ ፡፡ ሰዎች ፡ ቀስ ፡ ብለው ፡ ገብተዋልና ፡ አስቀድሞ ፡ ለዚኽ ፡ ፍርድ ፡ የተጻፉ ፡፡ እርሳቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የማይፈሩ ፡፡ ያምላካችነንም ፡ ጸጋ ፡ በርኵሰት ፡ የለወጡ ፡፡ አንደኛም ፡ አምላካችንና ፡ ጌታችን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ የካዱት ፡፡ አሳስባችሁም ፡ ዘንድ ፡ እወዳለሁ ፡፡ አንደግዜ ፡ ይህነን ፡ እንደወቃችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ እንደዳነ ፡፡ ሁለተኛም ፡ ያላምኑትን ፡ ፈጽሞ ፡ እንደጠፋ ፡፡ አለቅነታቸውንም ፡ ያልጠበቁትን ፡ ስፍራቸውንም ፡ የተው ፡ እንጅ ፡ መላእክት ፡፡ በጨለማ ፡ ውሥጥ ፡ ጠበቃቸው ፡ በዘላለም ፡ እሥራት ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ቀን ፡ ፍርድ ፡፡ እንደ ፡ ሰዶምና ፡ እንደ ፡ ገሞራ ፡ በዙርያቸውም ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አገሮች ፡፡ ዝሙት ፡ ያደረጉ ፡ እንደርሳቸው ፡ ከሌላ ፡ ሥጋም ፡ በኋላ ፡ የሔዱ ፡፡ እርሳቸውንም ፡ ምሳሌ ፡ አደረጋቸው ፡ ፍርድም ፡ አገኛቸው ፡ በዘላለም ፡ እሳት ፡፡ እንደሁም ፡ ደግሞ ፡ እለዚህ ፡ በሕልማቸው ፡ ሥጋቸውን ፡ ያረክሳሉ ፡፡ ጌትነትንም ፡ ያቃላሉ ፡ ክብርንም ፡ ይሰድባሉ ፡፡

## የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፲፭፡ ፲፰፡—፳፯፡፡

ይህነን ፡ አዛችኋለሁ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ ፡ ተዋደዱ ፡ ዘንድ ፡፡ ዓለም ፡ ቢጸላችሁ ፡ ከላንት ፡ በፊት ፡ እኔን ፡ እንደ ፡ ጸላኝ ፡ ታውቃላችሁ ፡፡ ከዓለምስ ፡ ብትሆኑ ፡ ዓለም ፡ ከርሱ ፡ ወገን ፡ የሆነውን ፡ ይወድ ፡ ነበረ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከዓለም ፡ አይደላችሁምና ፡ እኔ ፡ ከዓለም ፡ መረጥኋችሁ ፡ እንጅ ፡ ዓለም ፡ ይጸላችኋል ፡፡ እኔ ፡ የነገርኋችሁትን ፡ ነገር ፡ አስቡ ፡ ባርያ ፡ ከጌታው ፡ አይበልጥም ፡ ብዬ ፡፡ እኔን ፡ አሳደውኝ ፡ እንደ ሆን ፡ እላንትንም ፡ ያሳድዋችኋል ፡፡ ቃሌን ፡ ጠብቀው ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ቃላችሁንም ፡ ይጠብቃሉ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይህነን ፡



ሁሉ ፡ ያደርጉባችኋል ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡፡ የላከኝን ፡ አያውቁምና ፡፡ ካልመጣሁ ፡ ካልነገርኋቸውም ፡ ኃጢአት ፡ ባልሆነባቸው ፡፡ አሁን ፡ ግን ፡ ለኃጢአታቸው ፡ ምክንያት ፡ የላቸውም ፡፡ የሚጸላኝ ፡ አባቴን ፡ ደግሞ ፡ ይጸላል ፡፡ ከቶ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ያላደረገውን ፡ ስራ ፡ እኔ ፡ በመኻካላቸው ፡ ካላደረግሁ ፡ ኃጢአት ፡ ባይኖርባቸው ፡ ነበር ፡፡ አሁን ፡ ግን ፡ እኔን ፡ አዩኝ ፡ ጸሉኝም ፡ አባቴንም ፡ ጸሉ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይኽ ፡ ሆነ ፡ በኦሪታቸው ፡ የተጻፈው ፡ ነገር ፡ ለመፈጸም ፡ በከንቱ ፡ ጸሉኝ ፡ ተብሎ ፡፡ የሚያጸና ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ ግን ፡ ሲመጻ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ለላንት ፡ ከአብ ፡ ዘንድ ፡ የምሰደው ፡፡ ከአብ ፡ የሚወጣ ፡ የውነት ፡ መንፈስ ፡፡ እርሱ ፡ ስለኔ ፡ ይመሰክራል ፡፡ እላንትም ፡ ደግሞ ፡ ትመሰክራላችሁ ፡፡ ከመጀመርያ ፡ ጀምራችሁ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነበራችሁና ፡፡

## የቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ በዓል ፡፡

## ጸሎት ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ የመረጽሃቸውን ፡ ወገኖችህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ በመንፈሳዊት ፡ ገላኽ ፡ ላንዲት ፡ አንድነትና ፡ ጉባኤ ፡ አሰማምተሃቸዋልና ፡፡ ጸጋህን ፡ ስጠኔ ፡ በደህና ፡ ደስም ፡ በሚያሰኝህ ፡ አካሔድ ፡ ሁሉ ፡ የተፈጸሙትን ፡ ቅዱሳንህ ፡ እንዴህ ፡ እንከተላቸው ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ ግብዝነት ፡ ለሚወዱህ ፡ ወደዘጋጅህው ፡ ወደማይናገር ፡ ደስታ ፡ እስክንደርስ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

## በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ ራእይ ፡ ፯፡ ፪፡—፲፪፡፡

ሌላውንም ፡ መልአክ ፡ አየሁ ፡ ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ሲወጣ ፡፡ ለርሱም ፡ የሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ማሕተም ፡ ነበረለት ፡፡ በታላቅ ፡ ቃልም ፡ ምድርንና ፡ ባሕርን ፡ ይጉዱ ፡ ዘንድ ፡ የተሰጣቸውን ፡ አራቱን ፡ መላእክት ፡ ጸራ ፡ እንዴህ ፡ ሲል ፡፡ ምድርን ፡ አትጉዱ ፡ ባሕርንም ፡ ዛፎችንም ፡፡ የአምላካችነን ፡ ባሮች ፡ በማሕተም ፡ በግምባራቸው ፡ ላይ ፡ እስ

ክፍመለክት ፡ ድረስ ። የታተሙትንም ፡ ቍጥር ፡ ሰማሁ ። መቶ ፡ አርባ ፡ አራት ፡ ሺህ ። ከእሥራኤል ፡ ልጀች ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ የታተሙ ። ከይሁዳ ፡ ወገን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከሮቤል ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከጋድ ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከአሴር ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከንፍታሌም ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከምናሴ ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከስምዖን ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከሌዊ ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከይሳኮር ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከዛብሎን ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከዮሴፍ ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከብንያም ፡ ወገንም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ የታተሙ ። ከዚኽም ፡ በኋላ ፡ አየሁ ፡ እነሆም ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ለማንም ፡ ይቈጥሬቸው ፡ ዘንድ ፡ የማይቻለው ። ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከነገድም ፡ ከወገንም ፡ ከቋንቋችም ። በዙፋኑ ፡ ፊት ፡ ቁመው ፡ በበጉም ፡ ፊት ። ነጭ ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ። የሰሌንም ፡ ዝንጣፎች ፡ በጀቻቸው ፡ ይዘው ። በታላቅ ፡ ቃልም ፡ ጮሁ ፡ እንደዚህ ፡ ሲሉ ። መድኃኒት ፡ በዙፋን ፡ ላይ ፡ ለተቀመጠ ፡ ላምላካችንና ፡ ለበጉ ። መላእክትም ፡ ሁሉ ፡ በዙፋኑና ፡ በሽማግሎች ፡ ባራቱ ፡ እንስሶችም ፡ ዙርያ ፡ ቆሙ ። በዙፋኑም ፡ ፊት ፡ በግምባራቸው ፡ ወደቁ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ሰገዱ ፡ እንደዚህ ፡ ሲሉ ። አሜን ። በረከት ፡ ክብርም ፡ ጥበብም ፡ ምስጋናም ፡ ገናንነትም ፡ ኃይልም ፡ ችሎትም ፡ ላምላካችን ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

## የወንጌል ፡ ክፍል ። ማቴዎስ ፡ ፭ ፩—፲፪።

ብዙ ፡ የተሰበሰቡትን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ። በተቀመጠም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደርሱ ፡ መጡ ። አፉንም ፡ ከፈተ ፡ አስተማራቸውም ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ። በመንፈስ ፡ ድኆች ፡ ያሉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ለርሳቸው ፡ ናትና ። የሚያለቅሱ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። እርሳቸው ፡ ይጸናናሉና ። ገሮች ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። እርሳቸው ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉና ። ወደ ፡ ጽድቅ ፡ የሚራቡና ፡ የሚጸሙ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። እርሳቸው ፡ ይጸግባሉና ። መሐሮች ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። ምሕረትን ፡ ያገኛሉና ። ልባቸው ፡ የነጻ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። እርሳቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያያሉና ። ዕርቅን ፡ የሚያደርጉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። እርሳቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ። ስለ ፡ ጽድቅ ፡ የተሰደዱ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ። መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ለርሳቸው ፡ ናትና ። እላንት ፡ የተመሰገናችሁ ፡ ናችሁ ፡ ሲሰድቡዋችሁና ፡ ሲያሳድዋችሁ ፡ ጊዜ ። በላያችሁም ፡ ክፉውን ፡ ሁሉ ፡ ሲናገሩ ፡ ጊዜ ፡ በሐሰት ፡ ስለኔ ። ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ሐሤትም ፡ አድርጉ ። ደመወዛያችሁ ፡ በሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ነውና ። እንደዚሁም ፡ ከላንት ፡ በፊት ፡ የነበሩትን ፡ ነቢያት ፡ አሳደዋልና ።



---

## የጌታችን : እራት : የማገልገሉ : ሥርዓት : ወይስ : ቅድስት : አንድነት : ቊርባን : የምትባል።

የጌታውን : እራት : መቀበል : የሚሹ : ሁሉ : ስማቸውን : ላገልጋይ : ይንገሩ : አንድ : ወይስ : ኢያሌ : ቀን : አስቀድሞ ::

ከርሳቸውም : ማንም : ቢሆን : በግልጽ : ለኀጢአት : የሚገዛ :: ወይስ : ባልንጀራውን : በነገር : ወይስ : በስራ : የበደለው : ጉባዔ : በዚህ : እንደ : ተበደለች :: አገልጋይ : ይህነን : ዐውቀ : ይንገረው : ያስታውቀውም : ከቶ : ወደ : ጌታችን : ማዕድ : ለመቅረብ : እንዳይደፈር :: ንስሓ : እንደ : ገባ : ያለፈውንም : ክፉ : ሕይወቱን : እንደ : ለወጠ : በግልጽ : ሳይነግር :: በፊትም : የተበደለች : ጉባዔ : በዚህ : ልታርቅ :: የጐደውንም : ክፍሉን : ሊሰጥ : ወይስ : በውነት : ፍቃዴን : ሊያስታወቅ : መልካም : ሲችል : እንዲህ : ያድርግ : ዘንድ : እንዲወድ ::

አገልጋይም : በመኻከላቸው : ክፋትና : ጸላት : እንዲገዛ : ለሚያውቃቸው : ሰዎች : ደግሞ : እንዲህ : ያድርግ :: እርሳቸውን : ሳይተዋቸው : የጌታውን : እራት : ይከፈፈሉ : ዘንድ : ባይታረቁ :: ከርሳቸውም : አንድ : ክፍል : ቢሆን : ከሌላ : የተቀበለውን : በድል : ሁሉን : ከለልቡ : ሊያስቀርለት :: እርሱም : በራሱ : የበደለውን : ሊመልስ : የታዘጋጀ :: ሌላ : ክፍል : ግን : እንዲህ : ለመሆን : አንድነት : ባይሰማ :: በድፍረቱ : በክፋቱም : ደኖር : ዘንድ : የሚወድ : እንጅ :: ቄስ : ንስሓ :



የገባውን : ሰው : ለጌታ : እራት : ይቀበለው : ጸላቱን : ግን : ይከልክል ::

ቄስም : በጌታችን : እራት : ጊዜ : በሳድቃ : ወገን : ቁሞ : የጌታችን : ጸሎት : ከሚከተለው : ጸሎት : ጋራ : ይበል : ጉባዔ : ሁሉ : በጕልበታቸው : ተምበርክከው : ሲሆኑ ::

አባታችን : ሆይ : በሰማይ : የምትኖር :: ስምህ : ይቀደስ :: መንግሥትህ : ትምጸ :: ፈቃድህ : በምድር : ትሁን : እንደ : ሆነች : በሰማይ :: እንጀራችነን : የሚበቃነን : ስጠነ : ዛሬ :: ይቅር : በለነ : በኛ : ያለውን :: እኛ : ደግመን : ይቅር : እንደምንል : ልኛ : የለባቸውን :: ወደ : ፈተናም : አታግባን :: ከክፉ : አድነነ : እንጅ :: አሜን ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : ሆይ : ልብ : ሁሉ : በፊትህ : ተገልጽዋልና : መመኛትም : ሁሉ : ታውቂልና :: ምሥጢርም : ሁሉ : ካንተ : አልተሰወረችምና :: የልባችነን : ማሰብ : በመንፈስ : ቅዱስህ : በስትንፈሱ : አንጻው :: እኛ : ፈጽመን : እንወድህ : ዘንድ :: ቅዱስ : ስምህንም : እንደሚገባነ : እናመሰግን : ዘንድ : በክርስቶስ : ባጌታችን :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ፊቱን : ወደ : ሕዝብ : መልሶ : አሥር : ትእዛዛትን : ሁሉን : በጽሩ : ድምጽ : ይንገራቸው :: ሕዝብም : ሁሉ : በጕልበታቸው : ሁነው : ከኢያንዳንድ : ትእዛዝ : በኋላ : የእግዚአብሔርን : ምህረት : ይለምኑ : ስለ : መተላለፋ : ባለፈ : ዘመን :: ጸጋውንም : ይለምኑ : በሚመጣ : ዘመን : ይጠብቁት : ዘንድ :: እንዲሁም : ይሁን ::

ቄስ :: እግዚአብሔር : ይህነን : ነገር : ተናገረ : እንዲህ : ሲል :: እኔ : እግዚአብሔር : አምላክህ : ነኝ :: ሌሎች : አማልክት : በፊቴ : አይሁኑልህ ::

ሕዝብ :: ማረነ : አቤቱ :: ልባችነንም : መልስ : ይህችን : ትእዛዝ : እንጠብቅ : ዘንድ ::

ቄስ ። ሥእልን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌንም ፡ ከቶ ፡ አትስራልህ ። በላይ ፡ በሰማይ ፡ ካለው ። በታችም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ካለው ። በውኃም ፡ ከምድር ፡ በታች ፡ ካለው ። አትስገድላቸው ። አታምልካቸውም ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ቀናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነኝና ። ያባቶችን ፡ ኃጢአት ፡ የምመረምር ፡ በልጆች ፡ እስከ ፡ ሶስተኛ ፡ እስከ ፡ አራተኛም ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በሚጸሉኝ ። መሀረትንም ፡ አደርጋለሁ ፡ ለብዙ ፡ ሺህ ፡ ለሚወዱኝ ፡ ትእዛዛቴንም ፡ ለሚጠብቁ ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። የእግዚአብሔርን ፡ ያምላክህን ፡ ስም ፡ ከንቱ ፡ አታደርገው ። እግዚአብሔር ፡ ስሙን ፡ ከንቱ ፡ ያደረገውን ፡ ሳይቀስፈው ፡ አይተወውምና ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። የሰንበትን ፡ ቀን ፡ አስብ ፡ ትቀድሰው ፡ ዘንድ ። ስድስት ፡ ቀን ፡ ስራ ፡ ተግባርህንም ፡ ሁሉን ፡ አድርግ ። ሰባተኛ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ያምላክህ ፡ ሰንበት ፡ ነውና ፡ በርሱ ፡ ስራን ፡ ሁሉን ፡ አትስራ ፡ አንተ ፡ ወንድ ፡ ልጅህም ፡ ሴት ፡ ልጅህም ፡ ሎሌህም ፡ ገረድህም ፡ ከብትህም ፡ ወይስ ፡ ባገርህ ፡ ያለ ፡ እንግዳ ። በስድስት ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንም ፡ ያለባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ፈጥርዋልና ፡ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ አረፈ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ባረከ ፡ ቀደሰውም ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክብር ። ዕድሜህ ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ በሚሰጠህ ፡ ምድር ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። አትግደል ።



ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። አታምንዝር ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዝንድ ።

ቄስ ። አትስረቅ ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቀ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። ባሰት ፡ አትምሰክር ፡ በባልንጀራህ ፡ ላይ ።

ሕዝብ ። ማረነ ፡ አቤቱ ። ልባችንንም ፡ መልስ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። የባልንጀራህን ፡ ቤት ፡ አትመኝ ። የባልንጀራህንም ፡ ምሽት ፡ አትመኝ ። ባርያውንም ፡ ባርያዪቱንም ። በሬውንም ፡ አህያውንም ፡ ማናቸውንም ፡ ከባልንጀራህ ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ።

ሕዝብ ። አቤቱ ፡ እንለመንሃለን ፡ ትምረን ፡ ዘንድ ። እለዚህንም ፡ ትእዛዛትህን ፡ በልባችን ፡ ትጽፍ ፡ ዘንድ ።

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ አንዲት ፡ ከለዚህ ፡ ሁለት ፡ ልመኖች ፡ ትከተል ፡ ስለ ፡ ንግሥት ። ቄስም ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ሲቆም ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።

እንጸልይ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ መንግሥትህ ፡ የዘላለም ፡ ናትና ። ኃይልህም ፡ አልተወሰነችም ። ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሁሉን ፡ ማራት ። የመረጽሃትንም ፡ የባርያህን ፡ የቢክቶርያን ፡ የንግሥታችንን ፡ ልብ ፡ እንዲህ ፡ ግዛ ፡ እርስዋ ፡ የማን ፡ አገልጋይ ፡ እንድትሆን ፡ ዐውቃ ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ያንተን ፡ ክብርና ፡ መስጋናውን ፡ እንድትሻ ። እኛም ፡ ለርስዋም ፡ የሚገዙ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የማን ፡ ሥልጣን ፡ ያለቻት ፡ በጣም ፡ ስናስብ ፡ ታመነን ፡ እንድንገዛላት ፡ እንድናከብራትም ፡ በትሕትናም ፡ እንድንታዘዝላት ፡ ባንተ ፡ ስላንተም ። እንደ ፡ ተባረከ ፡ ቃልህና ፡ ሥርዓትህ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ካን

ቲና : ከመንፈስ : ቅዱስ : ጋራ : በሚኖር : በሚገዛም : አንድ : አምላክ : ለዘላለም :: አሜን ::

ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ : ሆይ :: የነገሥታት : ልብ : በጅህ : በመግዛትህም : እንዳለ :: አንተም : ለጥበብህ : መልካም : እንደ መስል : እንድታኖራቸው : እንድትመልሳቸውም : ከቅዱስ : ቃልህ : ተምረናልና :: እኛ : በትሕትና : እንለምንሃለን : የባርያህን : የቢክቶርያን : የንግሥታችነን : ልብ : እንዲህ : እንድታቀናው : እንድትገዛውም : እርስዋ : በማሰብዋ : በመናገርዋም : በስራዋም : ሁሉ : ለዘወትር : ክብርህን : መስጋናህንም : ትሻ : ዘንድ :: እርስዋም : የታመነችበትን : ሕዝብህ : በባለጠግነት : በዕርቅም : በጽድቅም : ትጠብቅ : ዘንድ :: ይህነን : ስጥ : የምህረት : አባት : ሆይ : በተወደደ : ልጅህ : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : መክንያት :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ለዚያ : ቀን : የተደረገች : ጸሎት : ትከተል :: ቄስም : ከዚያ : በኋላ : ለዚያ : ቀን : የተደረገውን : የወንጌልን : የመልእክትንም : ክፍል : ያንብብ :: ሕዝብ : ሁሉ : ወንጌል : ሲነበብ : ጊዜ : ይቁሙ :: ከዚያም : በኋላ : ሁላቸው : ከዚህ : የሚከተለውን : የሃይማኖትን : ስምቦሉን : ባንድ : ድምጽ : ይበሉ : ሁላቸው : ቁመው : ሳሉ ::

እኔ : አመናለሁ : ባንድ : አምላክ : ሁሉን : በሚችል : አብ :: የሰማይና : የምድር : የሚታይም : የማይታይም : ነገር : ሁሉ : ፈጣሪ ::

ባንድ : ጌታም : በየሱስ : ክርስቶስ : እርሱም : ብቻውን : የተወለደ : የእግዚአብሔር : ልጅ :: ከአብ : የተወለደ : ካለም : ሁሉ : አስቀድሞ :: አምላክ : ከአምላክ :: ብርሃን : ከብርሃን :: እውነተኛ : አምላክ : ከውነተኛ : አምላክ :: የተወለደም : ያልተፈጠረ :: ያንድ : ባሕሪ : ሁኖ : ከአብ : ጋራ :: ነገር : ሁሉ : በርሱ : የሆነ :: እርሱም : ስለኛ : ሰዎች : ስለ : ማድኀኒታችን : ከሰማይ : ወረደ :: ሥጋም : ለበሰ : በ



መንፈስ : ቅዱስ : ከማርያም : ድንግል :: ሰውም : ሆነ :: ደግምም : ስለኛ : ተሰቀለ : በጲላጦስ : በጴንጤናዊ : ዘመን :: እርሱም : መከራ : ተቀበለ : ተቀበረም :: በሶስተኛውም : ቀን : ተነሣ : በመጽሐፍ : ቅዱስ : እንደ : ተባለ :: ወደ : ሰማይም : ወጣ :: ወደ : አብም : ወደ : ቀኙ : ተቀመጠ :: በምስጋናም : ይመለስ : ዘንድ : ጊዜ : አለው : በሕያዋንና : በሙታን : ለመፍረድ :: መንግሥቱም : መጨረሻ : የላትም ::

አምናለሁም : በመንፈስ : ቅዱስ :: እርሱም : ጌታ : የሕይወትም : ሰጭ : የሚሆን :: ከአብና : ከወልድ : የሚወጣ :: ከአብና : ከወልድም : ጋራ : ባንድ : የሚሰግዱለት : የሚያመሰግኑትም :: እርሱም : በነቢያት : አፍ : ተናገረ :: አምናለሁም : ባንዲት : ካቶሊካዊትና : አጶስቶሊካዊት : ቤተ : ክርስቲያን :: አንዲትንም : ጠምቀት : ስለ : ኃጢአት : ስርየት : አስታውቃለሁ :: ተስፋም : አድርጋለሁ : የሙታንን : ትንሣኤ :: የሚመጣውንም : ዓለም : ሕይወት :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : አንዳች : በሚመጣ : ሳምንት : በዓል : ቢሆን : ወይስ : ቊርባን : በሚመጣ : እሁድ : መግዘትም : ቢሆን : መጋባትም : ሌላም : የቤተ : ክርስቲያን : ነገር : ቄስ : ያውራው :: ከዚያም : ወዲያ : ስብከት : የእግዚአብሔርን : ነገር : ማስታወቅ : ይከተል :: ከዚያም : በኋላ : ቄስ : በጌታ : ሳድቃ : ዘንድ : ቁሞ : ከዚህ : ከሚከተል : ከወንጌል : ነገር : ኢያሌን : ያንብብ :: ዲያቆናትም : የዚያን : ጊዜን : ምጽዋት : ስለ : ድኆች : ከተሰበሰቡ : ሰዎች : ያክማቹ ::

እንዲሁ : ብርሃናችሁ : በሰው : ፊት : ይብራ : መልካሙን : ስራችሁን : አይተው : የሰማዩን : አባታችሁ : እንዲያመሰግኑት :: ማቴዎስ : ፭።

መዝገብን : አትሰብስቡላችሁ : በምድር : ላይ :: ትል : ወደሚበላው : ነቀዝም : ወደሚያነቅዘው :: ሌቦችም : ነድለው : ወደሚሰርቁት :: ነገር : ግን : መዝገብን : ሰብስቡላ

ችሁ : በሰማይ : ትል : ወደማይበላው :: ነቀዝም : ወደ ማያነቅዘው : ሌቦችም : ነድለው : ወደማይሰርቁት :: ማቴዎስ : ፯፡፡

ሰዎች : ሊያደርጉላችሁ : እንደምትወዱት : ሁሉ : እንዲሁም : እላንት : ደግሞ : አድርጉላቸው :: ኦሪትና : ነቢያትም : ይህ : ነውና :: ማቴዎሰ : ፯፡፡

አቤቱ : አቤቱ : ብሎ : የሚለኝ : ሁሉ : መንግሥተ : ሰማያትን : የሚገባ : አይደለም :: በሰማይ : ያለውን : ያባቴን : ፈቃድ : የሚያደርግ : እንጅ :: ማቴዎስ : ፯፡፡

ዘኬዎስም : ቆመ : ጌታንም : አለው :: እነሆ : የከብቴን : እኩሌታ : ጌታ : ሆይ : ለድኆች : እሰጣለሁ :: ማንንም : ቀምቼ : እንደሆንሁ : መልሼ : አራት : እፅፍ : እከፍልለታለሁ :: ሉቃስ : ፲፱፡፡

በንፍገት : የዘራ : በንፍገትም : ያጭዷልና :: በበረከትም : የዘራ : በበረከትም : ያጭዷል :: ኢያንዳንዱ : በልቡ : እንደ : ተዘጋጀ : ያድርግ :: በልብ : አዘንም : በግድም : እንደሚሆን : አይደለም :: እግዚአብሔር : ወደ : የሚሰጠውን : ይወዷልና :: ፪ ቆሮንቶስ : ፱፡፡

አሁንም : ጊዜ : አገኘተናልና : መልካም : እናድርግ : ለሁሉ :: ይልቁንም : ለሃይማኖት : ቤተ : ሰቦች :: ገላትያን : : ፮፡፡

የኛ : ንግድ : ታላቅ : ናት :: እርሱም : አምልኮ : በቃኝ : ማለትም :: ወደ : ዓለም : አንዳች : ይዘን : አልገባንምና :: ከርሱም : አንዳች : ይዘን : መውጣት : አይቻለነምና :: ፩ ወደ : ጢሞቴዎስ : ፮፡፡

የዚህን : ዓለም : ባለጠጎች : ለመለገስና : ለመክፈል : እንዲዘጋጁ : እዘዛቸው : መልካም : መሠረትን : ለሚመጣው : ዘመን : ለራሳቸው : እንዲያከማቹ : የዘላለምንም : ሕይወት : ይወስዱ : ዘንድ :: ፩ ወደ : ጢሞቴዎስ : ፮፡፡

እግዚአብሔር : ግፈኛ : አይደለምና : ስራችሁን : ከፍቅርም : የሆነውን : ድካማችሁን : ይረሳ : ዘንድ : በስሙ : የገ



ለጣችሁትን : ባለፈው : ማገልገላችሁ : ለቅዱሳን :: አሁንም : ታገለግልዋቸዋላችሁ :: ወደ : ዕብራውያን : ፮፡፡

መምጸወትንና : መክፈልን : አትርሱ :: እንዲህ : ያለውን : መሥዋዕት : እግዚአብሔር : ይወዷልና :: ዕብራውያን : ፲፫፡፡

የዚህን : ዓለም : ገንዘብ : ያለው : ወንድሙንም : አንዳች : ሲሻ : የሚያይ : ርኅራኄውንም : የከለከለው :: እንዴት : ይኖርበታል : የእግዚአብሔር : ፍቅር :: ፩ ዮሐንስ : ፫፡፡

ድኆችን : የሚምር : ለእግዚአብሔር : ያበድራል :: እርሱም : ደግሞ : ምላሹን : ይመልስለታል :: ምሳሌ :: ፲፱፡፡

ለችጋረኛ : ለምስኪንም : የሚያስብ : መስጉን : ነው :: እግዚአብሔር : በክፉ : ቀን : ያድነዋል :: መዝሙር : ፵፩፡፡

የሚሰበስቡትንም : ምጽዋት : በወጭት : አድርገው : ለቄስ : ያምጡት : እርሱም : በጌታ : ሳድቃ : ላይ : ሊያኖረው ::

የወይን : ጸጅንም : በሳድቃ : ላይ : ያኑር :: ከዚያም : ወዲያ : ቄስ : ይበል ::

ከዚህ : በምድር : ላይ : ለምትጋደል : ለክርስቶስ : ቤተ : ክርስቲያን : ሁሉ : እንጸልይ ::

ሁሉን : የምትችል : በዘላለምም : የምትኖር : ሕያው : አምላክ :: በቅዱስ : ሐዋርያህ : አፍ : ለሰው : ሁሉ : ጸሎትን : እናድርግ : ዘንድ : እንለምንህም : ዘንድ : እናመሰግንህም : ዘንድ : አስተምረሀናልና :: እኛ : በትሕትና : እንለምንሃለን : በታላቅ : ርኅራኄህ : (* ይህችን : የምናቀርብልህ : ምጽዋታችነንና :) ይህነን : ለመለኮትህ : ምስጋና : የምናቀርበውን : ጸሎታችን : ትቀበል : ዘንድ :: ካቶሊካዊትንም : ቤተ : ክርስቲያንህ : ለዘወትር : በውነት : ባንድነትም : በሰላምም : መንፈስ : ትገዛት : ዘንድ : እንለምንሃለን :: ቅዱስ : ስምህም : ለሚጸራባቸው : ሁሉ : በቅዱስ : ቃልህ : በውነቱ : አንድ : ይሆኑ : ዘንድ :: ባንድነትም : በተቀደሰ : ፍቅርም : ይኖሩ : ዘንድ : ጸጋህን : ስጣቸ

* ምጽዋት : ሳይለቀም : ጊዜ : ይህ : ነገር : ይቅር ::

ው ። ደግመን ፡ እንለምንሃለን ፡ የክርስቲያንን ፡ ነገሥታት ፡ መኳንንትንም ፡ ሹማምትንም ፡ ሁሉን ፡ ታድናቸው ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቃቸውም ፡ ዘንድ ። ይልቁንም ፡ ባርያህን ፡ ቢክተርያ ኙ ፡ ንግሥታችንን ። ክርስዋ ፡ በታች ፡ እኛ ፡ በሥርዓትና ፡ በርቅ ፡ እንገዛ ፡ ዘንድ ። ለሸንጎዋም ፡ ሁሉ ፡ ከርስዋም ፡ በታች ፡ ለ ተሾሙ ፡ ሁሉ ፡ ጸጋህን ፡ ስጣቸው ፡ በውነት ፡ ያለ ፡ አድልዎ ፡ ገጽም ፡ ቅንን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ። ዓመፃንና ፡ ዝንግን ፡ ለመ ቅሠፍ ፡ እውነተኛ ፡ ሃይማኖትን ፡ ግን ፡ በጐነትንም ፡ ለመ ጠበቅ ። ጸጋህንም ፡ ስጥ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ ለኤ ጲስቆጶሳት ፡ ሁሉ ፡ ለቀሳውስትም ፡ ሁሉ ። እርሳቸው ፡ በሕይወታቸው ፡ በትምህርታቸውም ፡ እውነተኛውን ፡ ሕያ ውንም ፡ ቃልህ ፡ ይገልጹ ፡ ዘንድ ። የተቀደሱትንም ፡ ምሥ ጢራትህን ፡ በቅን ፡ እንደ ገባቸው ፡ ያገለግልዋቸው ፡ ዘን ድ ። ለሕዝብህም ፡ ሁሉ ፡ ሰማያዊትን ፡ ጸጋህ ፡ ስጣቸው ። ይልቁንም ፡ ከዚህ ፡ ላለች ፡ ጉባዔ ። እርሳቸው ፡ በየዋህ ፡ ልብ ፡ በሚገባውም ፡ ፍርሃት ፡ ቅዱስ ፡ ቃልህን ፡ ሰምተው ፡ ተቀብለውም ፡ በውነት ፡ በቅድስናም ፡ በጽድቅም ፡ ያገለግ ሉህ ፡ ዘንድ ፡ የሕይወታቸውን ፡ ዘመን ፡ ሁሉን ። ደግሞም ፡ በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ አቤቱ ፡ ስለ ፡ ቸርነትህ ፡ በዚ ች ፡ በምታልፍ ፡ ሕይወት ፡ በድካም ፡ በመከራም ፡ በድን ትም ፡ በሕማምም ፡ ወይስ ፡ በሌላ ፡ መጎደል ፡ ያሉትን ፡ ሁሉን ፡ ታጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ ትረዳቸውም ፡ ዘንድ ። ደግ ሞም ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እንባርካለን ፡ ከዚች ፡ ሕይወት ፡ በሃይማኖትህና ፡ በፍርሃትህ ፡ ስለ ፡ ወጡ ፡ ባሮችህ ፡ ሁሉ ። እንለምንህማለን ፡ ጸጋ ፡ ትሰጠኑ ፡ ዘንድ ፡ የርሳቸውን ፡ በጎ ፡ ምሳሌያቸውን ፡ ለመከተል ። እኛ ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ የሰማዩን ፡ መንግሥትህ ፡ እንከፈፈል ፡ ዘንድ ። ይህንን ፡ ስጥ ፡ አባት ፡ ሆይ ። ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስላንድ ፡ መ ካከለኛችንና ፡ ጰራቅሊጦሳችን ፡ መክንያት ። አሜን ።

ቄስ ፡ የጌታችንን ፡ እራት ፡ ባወራ ፡ ጊዜ ፡ ኢያሌ ፡ ቀን ፡ ወይስ ፡ አንድ ፡ ሰንበት ፡ አስቀድሞ ፡ የ



ሚሆን ። ከስብከቱ ፡ በፊት ፡ ወይስ ፡ በኋላ ፡ ይህነን ፡ ከዚህ ፡ የሚከተለውን ፡ ምክር ፡ ያን ብብ ።

ወዳጆቼ ፡ ሆይ ። እግዚአብሔር ፡ ቢወድ ፡ በሚመጣ ፡ እጅግ ፡ የሚያጸናውን ፡ የክርስቶስ ፡ የሥጋውንና ፡ የደሙን ፡ ምሥጢር ፡ በሃይማኖትና ፡ በፍርሃት ፡ ለሚ ቀበሉት ፡ ሁሉ ፡ አገለግልላቸው ፡ ዘንድ ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ። በርሱ ፡ ብቻ ፡ የኀጢአታችንን ፡ ስርየት ፡ ለምናገኝበት ፡ የ መንግሥት ፡ ሰማያትም ፡ ተከፋዮች ፡ ለምንሆንበት ፡ ለከ በረ ፡ መስቀሉና ፡ ለሕማማቱ ፡ ማስታሰቢያ ፡ ሁኖ ፡ ይቀበ ሉት ፡ ዘንድ ። ስለዚህ ፡ ሁሉን ፡ የሚችለውን ፡ የሰማዩን ፡ አባታችን ፡ በትሕትና ፡ ከለልባችንም ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ይገባናል ። ልጁን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ማድኃኒታችንን ፡ ሰ ጥትዋልና ፡ ስለኛ ፡ ለመሞት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ በዚች ም ፡ በተቀደሰች ፡ ምሥጢር ፡ መንፈሳዊ ፡ መብልና ፡ ምግ ብ ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ። ይህም ፡ ነገር ፡ እንደሚገባ ቸው ፡ ለሚቀበሉት ፡ እንደዬህ ፡ አምላካዊ ፡ በማጽናትም ፡ የመላ ፡ ነገር ፡ ሁንዋልና ፡ እንደማይገባቸውም ፡ ለሚቀበ ሉት ፡ እንደዬህ ፡ ታላቅ ፡ ኩነኔ ፡ መልቶበታልና ፡ ለኔ ፡ እመ ክራችሁ ፡ ዘንድ ፡ ይገባኛል ። የዚህችን ፡ የተቀደሰችን ፡ ምሥጢር ፡ ታላቅነት ። የፍርዷችሁንም ፡ ፍርሃት ፡ እንደማ ይገባችሁም ፡ ብትወስድዋት ፡ የምትወድቁባትን ፡ ታስቡት ፡ ዘንድ ። አቅልላችሁትም ፡ አይደለም ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ገብዛችሁ ፡ አይደለም ። በውነት ፡ እንጅ ፡ ልባችሁን ፡ ፍለጉት ፡ መርምሩትም ፡ ወደዚች ፡ ወደ ፡ ሰማያዊት ፡ እ ራት ፡ ቅዱሳንና ፡ ንጹሓን ፡ ሁናችሁ ፡ ትቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ በመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ የሚፈልገውን ፡ የሰር ግን ፡ ልብስ ፡ ተልብሳችሁ ። ለዚች ፡ ለተቀደሰች ፡ ማዕድ ፡ የተባረካችሁ ፡ ተቀማጮች ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ።

መመርመርም ፡ እንደዬህ ፡ ይደረጋል ። በመጀመርያ ፡ ሕይ ወታችሁን ፡ አካሔዳችሁንም ፡ በሥርዓት ፡ በእግዚአብሔ ር ፡ ትእዛዛት ፡ ልትመርምሩ ። በምናቸውም ፡ ነገር ፡ ታገኛላ

ችሁ ፡ እንደሆን ፡ እንደ ፡ በደላችሁ ፡ በፈቃድ ፡ ወይስ ፡ በመንገር ፡ ወይስ ፡ በስራ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ የራሳችሁን ፡ ኃጢአት ፡ ልታልቅቡት ። ይህነንም ፡ በራሳችሁ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንድታስታውቁበት ፡ በፍጹም ፡ ፈቃደችሁ ፡ ሕይወታችሁን ፡ ለበጐነት ፡ ትለውጡ ፡ ዘንድ ። መበደላችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ እንዲይሆን ፡ በባልጀሮቻችሁም ፡ እንጀ ፡ ብታገኙ ። እላንት ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ታረቁ ። የታዘጋጀችሁም ፡ ሁኒ ፡ በማንም ፡ ግፍና ፡ መጒደት ፡ ያደረጋችሁ ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ እንደ ፡ ችሎታችሁ ፡ ሁሉ ፡ ፍደውን ፡ ትከፍሉለት ፡ ዘንድ ። ወይስ ፡ ከሌላ ፡ ሰው ፡ የተበደላችሁ ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ ታስቀሩለት ፡ ዘንድ ፡ የመበደላችሁን ፡ ማስተስረያ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ እንደምትሹ ። ይህም ፡ ባይሆን ፡ ቅዱስ ፡ ቍርባንን ፡ በመቀበል ፡ ፍርዳችሁን ፡ ታበዙታላችሁ ፡ ብቻ ። ስለዚህ ፡ ማንም ፡ ከላንት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሰደቢ ፡ ቢሆን ። የቃሉንም ፡ ከልካይ ፡ ወይስ ፡ አቃላይ ። ወይስ ፡ አመንዝራ ። ወይስ ፡ ባመፃ ፡ ወይስ ፡ በቅናት ፡ ወይስ ፡ በሌላ ፡ ታላቅ ፡ ኃጢአት ፡ የሚኖር ። ስለ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ ንስሓ ፡ ባትገቡ ፡ ለዚህ ፡ ለተቀደሰ ፡ ሳድቃ ፡ አትቅረቡ ። የጌታውን ፡ እራት ፡ ከተቀበላችሁት ፡ በኋላ ፡ ሰይጣን ፡ ወደላንት ፡ እንደደገባ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ እንደ ፡ ገባ ። በዓመፃ ፡ ሁሉ ፡ እንዲይመላችሁ ፡ ወደ ፡ ሥጋም ፡ ወደ ፡ ነፍስም ፡ ጥፋት ፡ እንደይዛችሁ ።

ለሰውም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምህረት ፡ ፈጽሞ ፡ ባይታመን ። ልቡም ፡ ካልታረቀ ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ ቍርባን ፡ እንደይቀርብ ፡ ተገብትዋልና ። ማንም ፡ ቢሆን ፡ እንዲህ ፡ መርምሮ ፡ ሕሊናውን ፡ ማስታረቅ ፡ የማይችለው ፡ ሌላውን ፡ ማጽናትና ፡ ምክር ፡ ይፈልጋል ፡ እንጀ ። እርሱ ፡ ወደኔ ፡ ይምጣ ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ወደ ፡ እግዚአይሔር ፡ ቃል ፡ በጎ ፡ አገልጋይ ። አዘኑንም ፡ ይግለጽ ። በእግዚአብሔር ፡ በቅዱስ ፡ ቃሉ ፡ ኃጢአቱ ፡ ይሰረይለት ፡ ዘንድ ፡ መንፈሳዊትንም ፡ ምክር ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ሕሊናውንም ፡ ለማስታረቅ ፡ ጥርጣርዩንም ፡ ሁሉ ፡ ለማርጋት ።



ወይስ ፡ ቄስ ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ ቍርባን ፡ ለመምጣት ፡ እንዲታከቱ ፡ ቢያይ ፡ በዚያ ፡ ምክር ፡ ፈንታ ፡ ይህነን ፡ ያንብብ ።

እጅግ ፡ የተወደዳችሁ ፡ ወንድሞቼ ። በሚመጣ ፡ —— በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ የጌታን ፡ እራት ፡ አገለግል ፡ ዘንድ ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ ያላችሁትን ፡ ሁላችሁን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ወደርሱ ፡ እድማችኋለሁ ። በጌታችንም ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መክንያት ፡ እለምናችኋለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ራሱን ፡ እንዲህ ፡ በፍቅር ፡ አስጸርተዋችኋልና ፡ እምቢ ፡ አትበሉለት ። እላንትም ፡ ታውቃላችሁ ፡ እንዴት ፡ እጅግ ፡ እንዲያሳዝን ፡ እንዴት ፡ ታላቅ ፡ መበደልም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሰው ፡ ታላቅ ፡ ምሳውን ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ። ሳድቃውንም ፡ በበጎ ፡ መግብ ፡ ሁሉ ፡ በመላ ፡ ጊዜ ፡ ተቀምጦ ፡ የሚበላው ፡ ሰው ፡ እንጀ ፡ እንጀች ፡ የጐደለ ፡ እንደይኖር ፡ የታደሙትም ፡ ሰዎች ፡ በልባቸው ፡ ምቀኝነት ፡ ያለ ፡ መክንያትም ፡ ለመምጣት ፡ እምቢ ፡ ቢሉ ። ማነው ፡ ከላንት ፡ እንዲህ ፡ ቢሆንበት ፡ የማይቈጣ ። ማነው ፡ ከላንት ፡ እንዲህ ፡ ቢሆንበት ፡ ታላቅ ፡ መበደል ፡ ሆኖ ፡ የማይቈጥረው ። ስለዚህ ፡ በክርስቶስ ፡ እጅግ ፡ የተወደዳችሁ ። ትጠንቀቁ ፡ ይህነን ፡ ቅዱስ ፡ እራት ፡ ለመቀበል ፡ እምቢ ፡ በማለታችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቍጣ ፡ በላያችሁ ፡ እንደታስነሡ ። "እኔ ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ እራት ፡ አልመጣም ፡ ሌላ ፡ የሚከለክለኝ ፡ ምድራዊ ፡ ስራ ፡ አለኝና ፡" ማለት ፡ ለሰው ፡ ይቀላል ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ይህነን ፡ መንገራችሁን ፡ እንዲህ ፡ ቃሊል ፡ ሆኖ ፡ አይቈጥረውም ፡ አይቀበለውምም ። ማንም ፡ "እኔ ፡ ታላቅ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ነኝና ፡ ከመምጣት ፡ እፈራለሁ ፡" ቢል ። ለምን ፡ ንስሓ ፡ አትገቡም ። ለምንስ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አትመለሱምን ። እግዚአብሔር ፡ በጸራችሁ ፡ ጊዜ ፡ እላንት ፡ "አልመጣም ፡" ከማለታችሁ ፡ አታፍሩም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መመለስ ፡ ሲገባችሁ ፡ እላንት ፡ ራሳችሁን ፡ ታነጻላችሁን ፡ "አልተዘጋጀነም ፡" በማለት ። በውነት ፡ በልባችሁ ፡ አስቡ ። እንዲህ ፡ ያለ ፡ ከንቱ ፡ መንገ

ራችሁ ፡ ምን ፡ ደረባችኋል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ። ክርስ
ቶስ ፡ ምንድር ፡ ይላል ፡ በወንጌል ። ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አደረገ
ው ፡ ወደ ፡ ልጁ ፡ ሰርግ ፡ ለመምጣት ፡ እርሻውን ፡ ስለ ፡ ገ
ዙ ፡ ወይስ ፡ የተገዙትን ፡ ጽምድ ፡ በሮች ፡ ይፈትኑ ፡ ዘንድ ፡
ወይስ ፡ ምሽትን ፡ ስለ ፡ ማጋባት ፡ እምቢ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡
እንደህ ፡ በማለታቸው ፡ አልነጹም ፡ ሰማያዊ ፡ ምሳ ፡ የማ
ይገባቸው ፡ ሁነው ፡ ተቈጠሩ ፡ እንጂ ። እኔስ ፡ በስፍራዬ ፡ የ
ተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ። እንደ ፡ ሹመቴም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስ
ም ፡ አድማችኋለሁ ፡ በክርስቶስም ፡ ፈንታ ፡ እጸራችኋለ
ሁ ፡ እመክራችሁማለሁ ። የነፍሳችሁን ፡ መድኃኒት ፡ ብት
ወዱ ፡ ይህችን ፡ ቅድስት ፡ አንድነት ፡ እንድትካፈሉት ። የ
እግዚአብሔር ፡ ልጅም ፡ ነፍሱን ፡ በሞቱ ፡ በመስቀል ፡ ስ
ለ ፡ መድኃኒታችሁ ፡ እንደ ፡ ሰጠው ፡ እንዲሁም ፡ ይገባች
ኋል ፡ ለሞቱ ፡ መሥዋእት ፡ ለማሳሰብያው ፡ የተደረገውን ፡
እራቱን ፡ እርሱ ፡ እንደዘዘው ፡ ትቀበሉት ፡ ዘንድ ። ይህን
ን ፡ ቸል ፡ ብላችሁ ፡ ባታደርጉ ፡ በራሳችሁ ፡ አሰቡ ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ እንዴት ፡ እንድትበድሉት ። የዚህም ፡ መበደል ፡
በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ የተንጠለጠለ ፡ መቅሠፍቱ ፡ እንዴት ፡
ታላቅ ፡ ይሆናል ። ወደ ፡ ጌታው ፡ እራት ፡ ከመምጣት ፡ በፈ
ቃዳችሁ ፡ እምቢ ፡ ብላችኋልና ፡ ወደርሱም ፡ ከሚመጡ ፡
ከዚያም ፡ ከሰማያዊ ፡ ምግብ ፡ ምሳ ፡ ከሚመገቡ ፡ ከወን
ድሞቻችሁ ፡ ራሳችሁን ፡ ትለያላችሁና ። ይህነን ፡ ነገር ፡ መ
ልካም ፡ ብታስቡ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዳት ፡ ወደሚሻል ፡ ል
ብ ፡ ትለወጣላችሁ ። እኛም ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ የሰማዩ ፡ አባታችን ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ እንዲሰጣችሁ ፡
ጸሎታችነን ፡ በትሕትና ፡ እንተውም ።

ቅዱስ ፡ ቍርባንም ፡ ሲቈረብ ፡ የሚቀበሉትም ፡ በ
ስፍራቸው ፡ ሲሆኑ ፡ ጊዜ ፡ ቄስ ፡ ይህችን ፡ ምክ
ር ፡ ይበል ።

እጅግ ፡ የተወደዳችሁ ፡ በእግዚአብሔር ። እላንት ፡ ወደ ፡
ክርስቶስ ፡ ወደ ፡ መድኃኒታችን ፡ ወደ ፡ ሥጋውና ፡ ደሙ ፡ ወ



ደ ፡ ቅድስት ፡ አንድነቱ ፡ ትቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ የምትሹ ። ቅዱ
ስ ፡ ጳውሎስ ፡ ሰውን ፡ ሁሉን ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ መከረው ፡
ራሱን ፡ እጅግ ፡ ሊፈልግ ፡ ሊመረምርም ፡ ከዚያም ፡ እንጀ
ራ ፡ ይብላ ፡ ዘንድ ፡ ከዚያም ፡ ጽዋ ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ ሳይደ
ፈር ፡ በጣም ፡ ታስቡ ፡ ዘንድ ፡ ይገባችኋል ። በውነት ፡ ንስሐ ፡
በሚገባ ፡ ልብ ፡ በሕያውትም ፡ ሃይማኖት ፡ ያችን ፡ ቅድስት ፡
ምሥጢር ፡ ብንቀበል ፡ በረከቱ ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ። (እ
ንደህ ፡ አድርገን ፡ በመንፈስ ፡ የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ እንበላለ
ንና ፡ ደሙንም ፡ እንጠጣለንና ። እንዲህም ፡ አድርገን ፡ እ
ኛ ፡ በክርስቶስ ፡ እንኖራለን ፡ ክርስቶስም ፡ በኛ ፡ ይኖራል ።
እኛም ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነን ፡ እርሱም ፡ ከኛ ፡ ጋ
ራ ፡ አንድ ፡ ነው ።) እንዲሁም ፡ እንደ ፡ ይገባነ ፡ ብንቀበለው ፡
መጉዳታችን ፡ ታላቅ ፡ ነው ። እንዲህ ፡ አድርገን ፡ በክርስቶ
ስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ በሥጋውና ፡ በደሙ ፡ በደለኞች ፡ እን
ሆናለን ። የራሳችነንም ፡ ኩነኔ ፡ እንበላለን ፡ እንጠጠውማ
ለን ፡ የጌታውን ፡ ሥጋ ፡ አንለይምና ። የእግዚአብሔርንም ፡
ቍጣ ፡ በላያችን ፡ እናነደለን ። በልዩ ፡ ልዩ ፡ ሕማም ፡ በሞት
ም ፡ ይቀስፈን ፡ ዘንድ ፡ እናስመረዋለን ። ስለዚህ ፡ እላንት ፡
ወንድሞቼ ፡ በራሳችሁ ፡ ፍረዱ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ይፈር
ድባችሁ ። ስለ ፡ ሰራችሁት ፡ ኃጢአታችሁ ፡ በውነት ፡ ንስሐ ፡
ግቡ ። ሕያውትና ፡ የጸናች ፡ ሃይማኖት ፡ በክርስቶስ ፡ በመድ
ኃኒታችን ፡ ትሁንላችሁ ። ሕይወታችሁንም ፡ የተሻለውን ፡
አድርጉት ። በፍጹምም ፡ ፍቅር ፡ ኑሩ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋ
ራ ። እንዲሁም ፡ የዚያች ፡ የተቀደሰች ፡ ምሥጢር ፡ የሚገባ
ችሁ ፡ ተከፋዮቹ ፡ ትሆናላችሁ ። ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡ በትሕ
ትና ፡ ከለልባችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ አብን ፡ ወልድንም ፡
መንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ አመስግኑት ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡
ባለ ፡ በክርስቶስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ በሕማማቱና ፡ በሞቱ ፡
ዓለምን ፡ አድንዋልና ፡ ክርስቶስም ፡ ስለኛ ፡ በጨለማ ፡ በ
ሞትም ፡ ጽላ ፡ ስለ ፡ ተቀመጥነ ፡ ስለ ፡ ችጋረኞች ፡ ኃጢአተ
ኞች ፡ ራሱን ፡ ተዋረደ ፡ በመስቀል ፡ እንኳ ፡ እስኪሞት ፡
ድረስ ። እኛን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ልጆች ፡ ያደርገን ፡ ዘን

ድ : ወደ : ዘላለምም : ሕይወት : ያንሣን : ዘንድ :: ይህነን
ም : የመምህራችነን : ያንደኛውንም : መድኃኒታችን : ስ
ለኛ : የሞተውን : የየሱስ : ክርስቶስን : ጭራሽም : የሌለ
ውን : ፈቅር : ቍጥርም : የሌለውን : የከበረውን : ደሙ
ን : በማፍሰስ : ለኛ : የሰራውን : በረከት : ለዘወትር : እ
ናስብ : ዘንድ : እርሱ : የተቀደሶትን : ምሥጢራት : የፍቅሩ :
አረቡን : የሞቱም : መሳሰብያ : ይሆኑ : ዘንድ : ሰጠነ : ለታ
ላቅ : ለማያልቅም : ደስታችን :: ለርሱም : እንጊዴህ : ከአብ
ና : ከመንፈስ : ቅዱስ : ጋራ : በውነት : እንዲገባነ : ሁለግዜ :
ምስጋና : እንስጥ :: ራሳችነንም : በጣም : ለቅዱስ : ፈቃዱና :
ለመውደዱ : እንተው :: በውነተኛም : ቅድስና : በጽድቅ
ም : የሕይወታችን : ዘመን : ሁሉ : እንገዛለት : ዘንድ : እ
ንጋደል :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ወደ : ቅድስት : ቍርባን :
ለሚመጡ : እንዲህ : ይበል ::

ከላንት : በውነት : በልባችሁም : ስለ : ኃጢአታችሁ : የ
ምታዘኑ :: ከባልንጀሮቻችሁም : ጋራ : በፍቅርና : በውድ :
ያላችሁ :: አዲስም : ሕይወትን : ትሐዩ : ዘንድ : የእግዚአ
ብሔርንም : ትእዛዛት : ትከተሉ : ዘንድ : ካሁንም : ጀም
ራችሁ : በቅዱስ : መንገዱ : ትመላለሱ : ዘንድ : የምትፈ
ቅዱ :: በሃይማኖት : ቀረቡ :: ይህችንም : ቅድስትን : ምሥጢ
ር : ለመጽናታችሁ : ተቀበልዋት :: ሁሉንም : ለሚችል : ለ
እግዚአብሔር : የኃጢአታችሁን : መናዘዝ : አድርጉ : በት
ሕትና : በጕልበታችሁ : ተንበርክካችሁ : እንዲህ : ስትሉ ::

የዚያን : ጊዜም : ይህ : መናዘዝ : በሚቀረቡ : ሰ
ዎች : ስም : በቄስ : ይደረግ : እርሱ : ከሕዝብ :
ሁሉ : ጋራ : ተምበርክኮ :: ሁላቸውም : ባንድ :
ድምጽ : እንዲህ : ይበሉ ::

ሁሉን : የምትችል : እግዚአብሔር :: የጌታችን : የየሱስ :
ክርስቶስ : አባት : ያለምም : ሁሉ : ፈጣሪ :: የሰውም : ሁ
ሉ : ፈራጅ :: እኛ : ባሳብ : በነገርም : በስራም : ባምላካዊት :



ምስጋናህ : ላይ : ወትሮ : ያደረግነውን : የሚገባውንም : ቍ
ጣህና : መዓትህ : በላያችን : ያስነሣነበቱን : ብዙና : ታላ
ቅ : ኃጢአታችንና : መበደላችነን : እናውቃለን : እናዝንበት
ማለን :: እኛ : በዚህ : ኃጢአታችን : በውነት : እናዝናለን ::
ከለልባችንም : እናፈርበታለን :: ማሰቡ : እጅግ : ያሳዝነ
ናል :: መሸከሙንም : አንችለውም :: ማረነ :: የመሀረት :
አባት : ሆይ : ማረነ :: ስለ : ልጅህም : ስለ : ጌታችን : ስለ :
የሱስ : ክርስቶስ : መክንያት :: ያለፈውን : ሁሉ : ይቅር :
በለነ :: ጸጋህንም : ስጠነ :: ከንጊዴህ : ወዲህ : ለዘወትር :
ባዲስ : ሕይወት : እንገዛልህ : ዘንድ : ደስም : እናሰኝህ :
ዘንድ :: ለስምህ : መስጋናና : ክብር :: በጌታችን : በየሱስ :
ክርስቶስ :: አሜን ::

ከዚያም : ወዲያ : ቄስ : ወይስ : ኤጲስቆጶስ : ይነ
ሣ : ፊቱንም : ወደ : ሕዝብ : መልሶ : እንዲህ : ይ
በል ::

ሁሉን : የሚችል : እግዚአብሔር :: የሰማዩ : አባታችን ::
በታላቅ : ምህረቱ : በልቡ : ንስሓ : በመግባት : በውነተኛ
ም : ሃይማኖት : ወደርሱ : ለሚመለስ : ሰው : ሁሉ : ኃጢአ
ቱን : ሁሉን : ያስቀርለት : ዘንድ : ተስፋ : ያስደረገ :: እር
ሱ : ይማራችሁ : ኃጢአታችሁንም : ሁሉን : ይቅር : ይበልላ
ችሁ : ከኃጢአትም : ያድናችሁ :: በበጎ : ነገርም : ሁሉ : ያ
ጽናችሁ : ያብርታችሁም :: ወደ : ዘላለምም : ሕይወት :
ያድርሳችሁ :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ይበል ::

ክርስቶስ : መድኃኒታችን : በውነት : ወደርሱ : ለሚመለ
ሱ : እንደ : ምን : የሚያጸናውን : ነገር : ያላቸውን : ስሙ ::
ወደኔ : ኑ : እላንት : ደካሞች :: ሸክማችሁም : የከበ
ደ :: እኔም : አሳርፋችኋለሁ :: ማቴዎስ : ፲፩ ፳፰ ::
እግዚአብሔር : እንዲህ : ዓለሙን : ወደደ : አንድ : ልጁ
ን : እስኪለውጥ : ድረስ :: በርሱ : የሚያምን : ሁሉ : እን

ደይጠፋ :: የዘላለም : ሕይወት : እንድትሆንለት : እን
ጅ :: ዮሐንስ : ፫፤ ፲፮::

ቅዱስ : ጳውሎስ : የሚለውን : ነገር : ደግሞ : ስሙ ::
ነገሪቱም : እውነተኛ : ናት : እርስዋንም : ፈጽሞ : መቀበ
ል : የሚገባ : ነው :: ክርስቶስ : የሱስ : ወደ : ዓለም : እ
ንደ : መጣ : ኃጢአተኞችን : ሊያድን :: ፩፤ ጢሞቴዎስ :
፩፤ ፲፭::
ቅዱስ : ዮሐንስም : ደግሞ : የሚለውን : ነገር : ስሙ ::
ከላንት : ማንም : ኃጢአት : ቢሰራ : ከአብ : ዘንደ : ጰራ
ቅሊጦስ : አለን : የሱስ : ክርስቶስ : ጻድቅ :: እርሱም : የ
ኃጢአታችን : መታረቅ : ነው :: ፩፤ ዮሐንስ : ፪፤ ፩፤

ከዚያም : ወደ.ያ : ቄስ : ደበል ::

ልባችሁን : ወደ : ላይ : አንሡ ::
ምለሽ :: ወደ : ጌታ : እናነሠዋለን ::
ቄስ :: እግዚአብሔርን : አምላካችንን : እናመስግን ::
ም :: እንደዩ : ማድረግ : በወነት : በቅንም : የሚገባ :
ነው ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ፊቱን : ወደ : ጌታ : ሳድቃ :
ይመልስ : እንደዩ : ሲል ::

በውነት : በቅንም : እጅግ : ደገባናል : በጊዜ : ሁሉ : በስ
ፍራም : ሁሉ : እናመሰግንህ : ዘንድ : ጌታ : ሆይ :: ቅዱስ :
አባት* :: ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ ::
* እለዚህ : ቃላት :: "ቅዱስ : አባት" :: በሥላሤ : ሰንበ
ት : አይነበቡም ::

ከዚህ : በኋላ : በዓል : ባይሆን : ደሀ : መጨረሻ :
ይከተል ::

ስለዚህ : ከመላእክት : ከመላእክትም : አላቆች : ከ
ሰማይም : ጉባዔ : ሁሉ : ጋራ : የከበረውን : ስምህ : እናከ
ብራለን : ታላቅም : እናደርገዋለን :: ለዘወትር : ስናመሰግንህ :
ስንልም :: ቅዱስ : ቅዱስ : ቅዱስ : እግዚአብሔር : የሠራዊ



ት : አምላክ : ሆይ :: ሰማይና : ምድር : በክብርህ : ደመላ
ል :: ክብር : ላንተ : ደሁን : ከሁሉ : ልዑል : የሆንህ : ጌታ :
ሆይ :: አሜን ::

ከዚህ : የሚመጣ : በበዓል : ጊዜ : ያነን : መጨረ
ሻ : ደቀድም :: በልደት : በዓል : ሰባት : ቀንም :
በኋላ : ደሀ : ደቀድም ::

የሱስ : ክርስቶስን : አንደ.ን : ልጅህን : ለውጠሃልና : በ
ዚህ : ጊዜ : ስለኛ : ደወለድ : ዘንድ :: እርሱም : ከኃጢአታ
ችን : ሁሉ : ያነጻን : ዘንድ : በመንፈስ : ቅዱስ : ስራ : ከና
ቱ : ከማርያም : ድንግል : ባሕሪ : ተደዞ : እውነተኛ : የኃ
ጢአት : እድፍም : የሌለበት : ሰው : የሆነ :: ስለዚህ : ከ
መላእክት : የሚቀርም :

በፋሲካና : ሰባት : ቀን : በኋላ : ደሀ : ደቀድም ::

ደልቁንም : እናመሰግንህ : ዘንድ : ደገባናል : ስለ : ከበ
ረች : ስለ : ልጅህ : ስለ : የሱስ : ክርስቶስ : ስለ : ጌታችን :
ትንሣኤ :: እርሱ : ያ : እውነተኛ : ስለኛ : የተሠዋ : የዓለ
ምንም : ኃጢአት : ያስወገደ : የፋሲካ : በግ : ነውና :: እር
ሱም : ሙቶ : ሞትን : ሻረ :: ደግሞ : ለሕይወት : ተነሥቶ :
የዘላለምን : ሕይወት : መለሰልነ :: ስለዚህ : ከመላእክ
ት : የሚቀርም :

በርገት : ሰባት : ቀንም : በኋላ : ደሀ : ደቀድም ::

ከሁሉ : ደልቅ : በተወደደ : ልጅህ : በየሱስ : ክርስቶስ :
በጌታችን : እርሱ : ከከበረ : ትንሣኤው : በኋላ : ለሐዋ
ርያቱ : ሁሉ : በግልጽ : ታደትዋልና :: እርሳቸውም : ሲያዩ :
ወደ : ሰማይ : ወጣ : ከዚያ : ስፍራውን : ያበጅልን : ዘን
ድ : እርሱ : ወደለ : እኛ : ደግመን : ወደ.ያ : እንወጣ : ዘ
ንድ : ከርሱም : ጋራ : በክብር : እንገዛ : ዘንድ :: ስለዚህ :
ከመላእክት : የሚቀርም :

በጰራቅሊጦስ : ቀን : ስድስት : ቀንም : በኋላ : ደሀ :
ደቀድም ::

በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: እርሱ : በውነት : ተስ

ፈ ፡ እንደ ፡ አስደረገ ፡ እንደሁ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ ከሰማይ ፡ ወርዶ ፡ በድንገት ፡ ዓውሎንም ፡ በመሰለ ፡ በታላቅ ፡ ድምጽ ፡ በተከፋፈለችም ፡ በሳት ፡ መላስ ፡ መልክ ፡ በሐዋርያት ፡ ላይ ፡ ያስተምሬቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እውነትም ፡ ሁሉ ፡ ይመራቸው ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጠ ። እርሱም ፡ የልዩ ፡ ልዩን ፡ ቋንቋ ፡ ስጥወታ ፡ ሰጣቸው ፡ በሚቃጥልም ፡ ልብ ፡ ቅናት ፡ ላሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በወንጌል ፡ ይሰብኩ ፡ ዘንድ ፡ ድፍረትን ፡ ሰጣቸው ። እንደሁም ፡ እኛ ፡ ከጨለማና ፡ ከስሕተት ፡ ወጥተን ፡ ወደ ፡ ጽሩ ፡ ብርሃንህ ፡ ወደንተም ፡ ወደ ፡ ልጅህም ፡ ወደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ዕውቀት ፡ ደረስን ። ስለዚህ ፡ ከመላእክት ፡ የሚቀርም ፡

በሥላሢ ፡ በዓል ፡ ደህ ፡ ይቀድም ።

አንድ ፡ አምላክ ፡ አንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለህ ። አንድ ፡ አካል ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ሶስት ፡ አካላት ፡ ባንድ ፡ ባሕሪ ፡ እንጂ ። ስለ ፡ አብም ፡ ምስጋና ፡ ያመነውን ፡ እርሱንም ፡ ስለ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ እናምናለን ፡ መለየትና ፡ መከፈልም ፡ ሳደርግ ። ስለዚህ ፡ ከመላእክት ፡ የሚቀርም ፡

ከዚህም ፡ በላይ ፡ የተገኘ ፡ መጨረሻው ፡ ይከተል ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ በጌታ ፡ ሳድቃ ፡ ዘንድ ፡ በጉልበቱ ፡ ወድቆ ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ እራት ፡ በሚቀርቡ ፡ ሁሉ ፡ ስም ፡ ይህነን ፡ ጸሎት ፡ ይበል ።

እኛ ፡ ወደዚች ፡ እራትህ ፡ የመህረት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ በራሳችን ፡ ጽድቅ ፡ ታምነን ፡ እንቀርብ ፡ ዘንድ ፡ አንደፍርም ፡ በምህረትህ ፡ ብዛትና ፡ ታላቅነት ፡ ታምነን ፡ እንጂ ። ለኛ ፡ አይገባነምና ፡ ከምሳህ ፡ የሚወድቀውን ፡ ፍርፋሪ ፡ ስንኳ ፡ እንለቅም ፡ ዘንድ ። አንተ ፡ ግን ፡ የማትለወጥ ፡ ጌታ ፡ ነህ ። ሁለግዜ ፡ ምህረት ፡ ማሰኘት ፡ ጠባይዕህ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠን ፡ የጸጋ ፡ እግዚአብሔር ። የተወደደውን ፡ የልጅህን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ እንደሁ ፡ እንድንበላ ፡ ደሙንም ፡ እንደሁ ፡ እንድንጠጣ ። ኃጢአት ፡ የመላበት ፡



ሥጋችን ፡ በሥጋው ፡ ይነጻ ፡ ዘንድ ። ነፍሳችንም ፡ እጅግ ፡ በከበረ ፡ ደሙ ፡ ይታጸብ ፡ ዘንድ ። እኛም ፡ ለዘወትር ፡ በርሱ ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡ እርሱም ፡ በኛ ። አሜን ።

ከዚያም ፡ ወደ ፡ ያ ፡ ቄስ ፡ በሳድቃ ፡ ዘንድ ፡ ቁሞ ፡ የቅዳሴን ፡ ጸሎት ፡ ይጸልይ ፡ እንደሁ ፡ ሲል ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ። ሰማያዊ ፡ አባታችን ። ከምህረትህ ፡ የተነሣ ፡ አንደኛውን ፡ ልጅህ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ እርሱ ፡ በመስቀል ፡ ተሰቅሎ ፡ ስለ ፡ መድኃኒታችን ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ ለውጠህዋልና ። እርሱም ፡ ከዚያ ፡ ራሱን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አቅርቦ ፡ ስለ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ምሉን ፡ ፍጹምንም ፡ የሚበቃውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ቍርባባንንም ፡ ካሳውንም ፡ አቀረብ ። ለዚያም ፡ ለከበረ ፡ ሞቱ ፡ ማሳሰብያውን ፡ ለዘወትር ፡ ሰራ ። በቅዱስ ፡ ወንጌሉም ፡ ሁለግዜ ፡ እርሱ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ እንጠብቀው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ስማን ፡ የመህረት ፡ አባት ፡ ሆይ ። በትሕትና ፡ እጅግ ፡ እንለምንሃለን ። እኛ ፡ የህነን ፡ ፍጥረትህ ፡ ያለውን ፡ እንጀራና ፡ ጸጅ ፡ እንደ ፡ ልጅህ ፡ እንደ ፡ መድኃኒታችን ፡ እንደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ቅድስት ፡ ሥርዓቱ ፡ ለሕማማቱና ፡ ለሞቱ ፡ ማሳሰብያ ፡ ሁና ፡ ስንቀበለው ፡ እጅግ ፡ የተባረከውን ፡ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ ስጠን ። እርሱም ፡ በዚያች ፡ በተያዘባት ፡ ሌት ። (a) እንጀራውን ፡ ወሰደ ። ባመሰገነም ፡ ጊዜ ፡ (b) ቈረሰው ። ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሰጠው ፡ እንደሁ ፡ ሲል ። እንኩ ፡ ብሉም ። (c) ደህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፡ ስለላንት ፡ የሚሰጥ ፡ ይህነንም ፡ ለመታሰቤ ፡ አድርጉ ። እንደሁም ፡ እራታቸውን ፡ ከበሉ ፡ በኋላ ፡ (d) ጽዋውን ፡ ወሰደ ። ባመሰገነም ፡ ጊዜ ፡ ለር

(a) ቄስ ፡ ይህነን ፡ ብሎ ፡ የንጀራውን ፡ ወጭት ፡ በጁ ፡ ይውሰድ ።

(b) ይህነንም ፡ ብሎ ፡ እንጀራውን ፡ ይቍረስ ።

(c) ይህነን ፡ ብሎ ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ እንጀራ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያኑር ።

(d) ይህነንም ፡ ብሎ ፡ ጽዋውን ፡ በጁ ፡ ይውሰድ ።

ሳቸው : ሰጠው : እንደዬህ : ሲል ::
ከዚህ : ጥጡ : ሁላችሁ : (e) ይህ : ደሜ : ነውና : ላዲስ : ኪዳን :: ስለላንት : ስለ : ብዙም : ኃጢአት : ለማስተስረይ : የሚፈስ :: ይህነን : አድርጉ : በምትጠጡት : ጊዜ : ሁሉ : ለመታሰቤ :: አሜን ::

(e) ይህነንም : ብሎ : እጁን : በወይን : ጸጽ : ሁሉ : ከዚያ : ለመቀደስ : ባለው : በላየው : ያኑረው ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : በመጀመርያ : የጌታውን : እራት : ሁለት : ክፋሉን : ለራሱ : ይቀበለው :: በኋላ : ከዚያ : ላሉ : ለቅሳውስት :: ከርሳቸውም : በኋላ : ለሕዝብ : እንደ : ሥርዓት : ለሁላቸው : በጕልበታቸው : ኑረው : ወደ : እጃቸው : ይስጣቸው :: እንጀራውንም : ለማንም : ሲሰጥ : እንደዬህ : ይበል ::

ስላንተ : የተሰጠ : የጌታችን : የየሱስ : ክርስቶስ : ሥጋ : ሥጋህንና : ነፍስህን : ለዘላለም : ሕይወት : ይጠብቅ :: ይህነን : እንካ : ብላውም : ክርስቶስ : ስላንተ : እንደ : ሞተ : አስበህ :: በልብህም : በርሱ : ተመገብ : በሃይማኖትና : በምስጋና ::

ለማንም : ጽዋውን : ሲሰጥ : እንደዬህ : ይበል ::
ስላንተ : የፈሰሰ : የጌታችን : የየሱስ : ክርስቶስ : ደም : ሥጋህንና : ነፍስህን : ለዘላለም : ሕይወት : ይጠብቅ :: ይህነን : ጥጣ : የክርስቶስ : ደም : ስላንተ : እንደ : ፈሰሰ : አስበህ : አመስግነውም ::

ቍርባን : ሁሉ : ሳይፈጅ : የተቀደሰ : እንጀራ : ወይስ : ጸጅ : ሁሉ : ያለቀ : እንደሆን : ቄስ : ሌላውን : ይቀድስ : እንደዬህ : ሲል :: መድኃኒታችን : የሱስ : ክርስቶስ : በዚያች : በተያዘባት : ሌት : የሚቀርም ::



ሰው : ሁሉ : በተቍረቡ : ጊዜ : የቀረውን : እንጀራና : ጸጅ : እንደገባው : በጌታ : ሳድቃ : ላይ : ያኑረው : በሻማም : ይከድነው ::

በኋላም : ቄስ : የጌታውን : ጸሎት : ይጸልይ : ሕዝብም : ከርሱ : በኋላ : ልመናውን : ሁሉን : ይድገሙ ::

አባታችን : ሆይ : በሰማይ : የምትኖር :: ስምህ : ይቀደስ :: መንግሥትህ : ትምጻ :: ፈቃድህ : በምድር : ትሁን : እንደ : ሆነች : በሰማይ :: እንጀራችንን : የሚበቃነን : ስጠነ : ዛሬ :: ይቅር : በለነ : በኛ : ያለውን :: እኛም : ደግመን : ይቅር : እንደምንል : ለኛ : የለባቸውን :: ወደ : ፈተናም : አታግባን :: ከክፋ : አድነን : እንጂ :: ያንተ : ነውና : መንግሥት : ኃይልም : ምስጋናም : ለዘላለም :: አሜን ::

ከዚያም : ወዲያ : ይጸልይ : እንደዬህ : ሲል ::

አቤቱ : ሰማያዊ : አባት : ሆይ :: እኛ : የተዋረድነ : ባሮችህ : አባተኛውን : ቸርነትህ : በጣም : እንለምናለን :: ይህነን : የክብር : የምስጋናም : ምሥዋዕታችንን : በምህረት : እንድትቀበል :: በትሕትናም : እንለምንሻለን : ጸጋህን : ልትሰጠነ : በልጅህ : በየሱስ : ክርስቶስ : በምግባረና : በሞቱ : በደሙም : በምታምን : ሃይማኖት : እኛ : የቤተ : ክርስቲያንህም : ሁላንትና : የኃጢአታችነን : ስርየት : የቀረውንም : የሕማማቱን : በረከት : ሁሉን : እንቀበል : ዘንድ :: ከዚህም : ጌታ : ሆይ : ራሳችነን : በሥጋችንና : በነፍችን : እናቀርብልሃለን : አዋቂት : ቅድስትም : ሕያውትም : ምሥዋዕት : እንሆንልህ : ዘንድ :: በትሕትናም : እንለምንሃለን : የዚች : ቅድስት : አንድነት : ተከፋዮች : የሆነ : እኛ : ሁላችን : በጸጋህ : በሰማያዊት : በረከትህም : እንመላ : ዘንድ :: እኛስ : ስለ : ኃጢአታችን : ብዛት : ከቶ : ምሥዋዕትን : እናቀርብልህ : ዘንድ : አይገባነም :: ነገር : ግን : ምግባራችነንም : ሳታስብብን : መበደላችነን : ይቅር : ስትለን : እንጅ : ይህነን : የሚገባነን : መገዛታችን : በምህረት : እንድት

ቀበል : እንለምንሃለን : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: በርሱ : ከርሱም : ጋራ : በመንፈስ : ቅዱስም : አንድነት : ክብርና : ምስጋና : ሁሉ : ላንተ : ይሁን : ሁሉን : የምትችል : አብ : ሆይ : ለዘላለም :: አሜን ::

ወይስ : እንዲህ ::

ሁሉን : የምትችል : ለዘላለምም : የምትኖር : ሕያው : አምላክ :: ከለልባችን : እናመሰግንሃለን : እኛን : ኢሌህን : የተቀደሱትን : ምሥጢራት : እንደ፡ገባ : የተቀበልነውን : በመንፈሳዊት : ምግብ : በልጅህ : በመድኃኒታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : እጅግ : በከበረ : ሥጋውና : ደሙ : ትመግበንበት : ዘንድ : ፈቅደሃልና :: በዚህም : ወደኛ : ያለሀውን : ጸጋህንና : ቸርነትህን : መስክረህልናል : ደግሞ : እጅግም : በከበረ : በተወደደ : ልጅህ : ሕማማትና : ሞት : ያመኑ : ሰዎች : ጉባኤ : የልጅህም : መንፈሳዊት : ሥጋ : በርሱ : በውነት : የተተከልነ : ብልቶች : በተስፋም : የዘላለም : መንግሥትህ : ወራሾች : እንደ : ሆነ : አጸንተህልናል :: በትሕትናም : እንለምንሃለን : የሰማዩ : አባት : ሆይ :: በጸጋህ : እንዲህ : እንድትረደን :: እኛ : በዚያች : ቅድስት : አንድነት : እንድንኖር :: አንተም : እንመላለስበት : ዘንድ : ያዘጋጅሀውን : በጎ : ስራ : ሁሉ : እንድናደርግ :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: ለርሱም : ካንተ : ከመንፈስ : ቅዱስም : ጋራ : ምስጋናና : ክብር : ሁሉ : ይሁን : ለዘላለም :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ጉባዔ : ሁሉ : ባንድ : ድምጽ : ይበሉ ::

ምስጋና : ለእግዚአብሔር : በላይ :: በምድር : ላይም : ሰላም :: ለሰውም : ደስታ :: እናመሰግንሃለን :: እንባርክሀማለን :: እንሰግድልህማለን :: እናከብርህማለን :: በታላቅ : ምስጋናህም : እናስታውቃለን : እግዚአብሔር : አምላክ : ሆይ :: ሰማያዊ : ንጉሥ :: ሁሉን : የምትችል : እግዚአብሔር : አብ ::



አቤቱ : አንድ : የተወለድህ : ልጅ : የሱስ : ክርስቶስ :: እግዚአብሔር : አምላክ : ሆይ :: የእግዚአብሔር : በግ :: የአብ : ልጅ :: ያለምን : ኃጢአት : ያስወገድሀው :: ማረኝ :: አንተ : ያለምን : ኃጢአት : ያስወገድሀው : ማረኝ :: አንተ : ያለምን : ኃጢአት : ያስወገድሀው : ጸሎታችነን : ተቀበል :: አንተ : ወደ : እግዚአብሔር : አብ : ቀኝ : የተቀመጥህ : ማረኝ ::

አንተ : ብቻህን : ቅዱስ : ነህና :: አንተ : ብቻህን : ጌታ : ነህና :: አንተ : ብቻህን : ክርስቶስ : ሆይ : ከመንፈስ : ቅዱስ : ጋራ : እጅግ : ልዑል : ነህና : በእግዚአብሔር : አብ : መስጋና :: አሜን ::

ከዚያም : ወዲያ : ቄስ : ጉባዔን : ያሰንብታቸው : ይህነን : በረከት : ሲል ::

ከአእምሮ : ሁሉ : የበለጠ : የእግዚአብሔር : ሰላም :: ልባችሁንና : መንፈሳችሁን : ይጠብቅ : በእግዚአብሔር : በልጁም : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : በውቀቱና : በውዴ :: ሁሉንም : የሚችል : የእግዚአብሔር : የአብ : የወልድም : የመንፈስ : ቅዱስም : በረከት : በመኻከላችሁ : ይሁን :: ከላንት : ጋራም : ይኑር : ለዘላለም :: አሜን ::

---

ጸሎቶች : ከሌላ : ማመልክ : በኋላ : ይጸለዩ : ዘንድ ::

እንደ : ምህረትህ : እግዚአብሔር : ሆይ : በለዚህ : ልመናቻችንና : በጸሎቶቻችን : እርደን :: የባሮችህንም : መንገድ : ወደ : ዘላለም : ማድኃኒት : አቅናው :: በዚች : ለሞት : በምትገዛ : ሕይወት : በመለዋወጥዋ : ሁሉ : በጸጋ : የተዘጋጀችልነ : ረዴትህ : ሁለግዜ : ትጠብቀን : ዘንድ :: በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

---

ሁሉን : የምትችል : እግዚአብሔር : የዘላለምም : አምላክ : ሆይ :: እኛ : እንለምንሃለን : እንድትፈቅድ : ልባችነን

ና ፡ ሥጋችንን ፡ በሕግህ ፡ መንገድ ፡ በትእዛዛትህም ፡ ስራ ፡ ታቀናው ፡ ትቀድሰውም ፡ ትገዛውም ፡ ዘንድ ። እኛ ፡ በኀይለኛ ፡ መጠበቅህ ፡ ከዚህና ፡ ለዘወትር ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡ በደኅንነት ፡ እንኖር ፡ ዘንድ ፡ በጌታችንና ፡ በመድኀኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

ጸጋህን ፡ ስጠኝ ፡ እንለምንሃለን ፡ ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። ዛሬ ፡ በሥጋዊ ፡ ጆሮዋችን ፡ የሰማነው ፡ ቃልህ ፡ ሁሉ ፡ በጸጋህ ፡ እንደሁ ፡ በውሥጣችን ፡ በልባችን ፡ እንድ ትተከል ፡ የበጎ ፡ ሕይወትን ፡ ፍሬ ፡ እንድታፈራብን ፡ ለስምህ ፡ መስጋናና ፡ ክብር ። በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

በምናደርገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ቅደምን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ በመሀረትና ፡ በጸጋ ። በምትዘወትርም ፡ ረዷትህ ፡ ምራን ። በስራችን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ የምንጀምረው ፡ የምንጨምረውም ፡ የምንጨርሰውም ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናከብር ፡ ዘንድ ። በመጨረሻም ፡ በምህረትህ ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ። የጥበብ ፡ ሁሉ ፡ ምንጭ ። የምንሻውን ፡ ነገር ፡ ሁሉን ፡ ሳንለምነው ፡ ታውቃለህና ። ደንቍርነታችንም ፡ በመልመን ፡ አልተሰወረችብህምና ። እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ድካማችንን ፡ ትምርልን ፡ ዘንድ ። ስለ ፡ አለገባባችንም ፡ እንለምነው ፡ ዘንድ ፡ የማንደፍር ፡ ስለ ፡ ዕውርነታችንም ፡ እንለምነው ፡ ዘንድ ፡ የማንችለው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በጸጋ ፡ ስጠኝ ፡ ስለ ፡ ልጅህ ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ጌታችን ፡ አገባብ ። አሜን ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ። በልጅህ ፡ ስም ፡ የሚለምኑህ ፡ ልመናቸውን ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስ



ደርገሃልና ። እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ወደኛ ፡ ጸሎታችንን ፡ ልመናችንንም ፡ አሁን ፡ ወደንተ ፡ ወደደረግነ ፡ ጆሮህን ፡ ጣል ። ይህንንም ፡ በሃይማኖት ፡ እንደ ፡ ፈቃድህም ፡ የለመነውን ፡ ነገር ፡ በውነት ፡ እናገኘው ፡ ዘንድ ፡ ስጠኝ ፡ ለመሻታችን ፡ ረዷት ፡ ለምስጋናህም ፡ መገለጽ ። በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

ሰዎች ፡ ከቄስ ፡ ጋራ ፡ ይቍረቡ ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ ቢሆኑ ፡ ሶስት ፡ ወይስ ፡ አራት ፡ ባይኖሩ ፡ ቍርባን ፡ አይሁን ። ኢያሌ ፡ ቀሳውስትና ፡ ዲያቆናት ፡ ቢኖሩ ፡ ከቄስ ፡ ጋራ ፡ ይቍረቡ ።

ክርክርና ፡ ጥርጣሬም ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ ያሰት ፡ ነገር ፡ እንደይሁን ፡ የቅደሴ ፡ እንጀራ ፡ የወትሮ ፡ ደህና ፡ የስንዴ ፡ እንጀራ ፡ ይሁን ።

ያልተቀደሰም ፡ እንጀራና ፡ ጸጅ ፡ ቢቀር ፡ ለቄስ ፡ ጥቃሜ ፡ ይሁን ። ከተቀደሰ ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ ቢቀር ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዘንድ ፡ አይውጣ ፡ ደሮ ፡ ቄስ ፡ ካሉ ፡ ከቍረቡ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ይፈጀት ።

ቄስና ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጠባቆች ፡ በጉባኤ ፡ ገንዘብ ፡ ለቍርባን ፡ የሚሆነውን ፡ እንጀራና ፡ ጸጅ ፡ ሊገዙ ።

የተለቀመውን ፡ ምጽዋት ፡ ለፍቅር ፡ ጥቃሜ ፡ ይስጡ ፡ ቄሱ ፡ ከጠባቆች ፡ ጋራ ፡ በጎ ፡ እንደ መስላቸው ። ባይሰማሙ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ቄስ ፡ ፈቃድ ፡ ይከፋፈል ።

### የሕፃናት ፡ የጥምቀታቸው ፡ ምሳሌ ፡

### በግልጽ ፡ በቤት ፡ ክርስቲያን ፡ ለመደረግ ፡፡

ጥምቀት ፡ ሁሉ ፡ ብትችል ፡ በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ትደረግ ፡ ጉባኤ ፡ ትመስክሬት ፡ ዘንድ ፡ ለተጠመቀውም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሬሱ ፡ ጥምቀት ፡ መታሰቢያ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡፡

ለሚጠመቅም ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ የክርስትና ፡ አባቶችና ፡ አንዲት ፡ የክርስትና ፡ እናት ፡ ለምትጠመቅም ፡ ሴት ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ የክርስትና ፡ አባት ፡ ሁለትም ፡ የክርስትና ፡ እናቶች ፡ ይሁኑ ፡፡

ሕፃናትም ፡ ለመጠመቅ ፡ እንደሉ ፡ ወላጀቻቸው ፡ ወደስ ፡ ዘመዷቻቸው ፡ ወይስ ፡ በርሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ቄስን ፡ በፊት ፡ ያስታውቁባቸው ፡፡ በተባለም ፡ ጊዜ ፡ ከጸሎት ፡ በኋላ ፡ መጠመቅያ ፡ ጽሬ ፡ ውኃ ፡ ይመላ ፡ ቄስም ፡ ከሰዎቹ ፡ ጋሬ ፡ በመጠመቅያ ፡ ዘንድ ፡ ቁሞ ፡ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ ይጠይቅ ፡፡

ይህ ፡ (ይህች ፡) ሕፃንን ፡ ተጠመቀ ፡ (ተጠመቀች ፡፡)

አይደለምም ፡ ቢሉ ፡ ቄስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይጨምር ፡፡

ወደጆቹ ፡ ሆይ ፡፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በኃጢአት ፡ ተረግዝዋልና ፡ ተወልድዋልምና ፡ ክርስቶስም ፡ መድኃኒታችን ፡ “ማንም ፡ ከውኃና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሁለተኛ ፡ ካልተወለደ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውም ፡” ብልዋልና ፡፡ እኔ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብ ፡ እንድትጸረ ፡ እለምናችኋለሁ ፡ እር



ሱ ፡ በምህረቱ ፡ ርኅራኄ ፡ {ለዚህ ፡ / ለዚች ፡} ሕፃን ፡ በ {ፍጥረቱ ፡ ይሆንለት ፡ / ፍጥረትዋ ፡ ይሆንላት ፡} ዘንድ ፡ የማይችለውን ፡ ነገር ፡ {እንዲሰጠው ፡ / እንዲሰጣት ፡} በውኃና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ {ይጠመቅ ፡ / ትጠመቅ ፡} ዘንድ ፡ ወደ ፡ ክርስቶስም ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያኑ ፡ {ይገባ ፡ / ትገባ ፡} ዘንድ ፡ የርስዋም ፡ ሕያውት ፡ ብልት ፡ {ይሆን ፡ / ትሆን ፡} ዘንድ ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ቄስ ፡ ይበል ፡፡

እንጸልይ ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ ከታላቅ ፡ ምህረትህ ፡ የተነሣ ፡ ኖህንና ፡ ቤቱን ፡ ከጥፋት ፡ ውኃ ፡ በመርከብ ፡ አደንሃቸው ፡፡ ሕዝብህንም ፡ የእሥራኤልን ፡ ልጆች ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በደህና ፡ መራሃቸው ፡ ለተቀደሰች ፡ ጥምቀትህ ፡ ምሳሌ ፡፡ እጅግም ፡ በተወደደ ፡ ልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መጠመቅ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ወንዝ ፡ ውኃውን ፡ የኃጢአት ፡ ስርየት ፡ ምልክት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀደስሀው ፡፡ እኛ ፡ ወሰን ፡ ስለ ፡ ሌላት ፡ ስለ ፡ ምህረትህ ፡ {ይህነን ፡ / ይህችን ፡} ሕፃን ፡ በሞገስ ፡ እንድ {ታየው ፡ / ታያት ፡} እንለምንሃለን ፡፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ {አጽበው ፡ ቀድሰውም ፡ እርሱ ፡ / አጽባት ፡ ቀድሳትም ፡ እርስዋ ፡} ከቍጣህ ፡ {ድኖ ፡ / ድና ፡} ቤት ፡ ክርስቲያንህ ፡ እንድ {ትቀበለው ፡ / ትቀበላት ፡} በሃይማኖትም ፡ {ጸንቶ ፡ / ጸንታ ፡} በተስፋም ፡ ደስ ፡ {ብሎት ፡ / ብላት ፡} በፍቅርም ፡ {ተመሰርቶ ፡ / ተመሰርታ ፡} የዚህን ፡ ድካም ፡ የመላበቱን ፡ የዓለምን ፡ ሞገድ ፡ እንደህ ፡ {እንዲሻገር ፡ / እንድትሻገር ፡} በመጨረሻ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ዕረፍት ፡ {እስኪደርስ ፡ / እስክትደርስ ፡} ከዚያ ፡

ካንተ : ጋራ : {ሊገዛ : / ልትገዛ :} ለዘላለም : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

ሁሉን : የምትችል : የማትጠፋም : አምላክ : ሆይ : ወደ ንተ : የሚሸሹ : የነደያን : ሁሉ : ረዳት : የምእምናንም : ሕይወት : የሙታንም : ትንሣኤ :: ለ {ዚህ : / ዚች :} ሕፃን : ወደ ንተ : እንጸራለን :: {እርሱ : / እርስዋ :} ወደ : ተቀደሰች : ጥምቀት ህ : {ደርሶ : / ደርሳ :} በመንፈሳዊት : {ልደቱ : የኃጢአቱን : / ልደትዋ : የኃጢአትዋን :} ስ ርየት : {እንዲያገኝ :: ተቀበለው : / እንድታገኝ :: ተቀበላት :} አቤቱ : ተስፋ : እንደ : አስደረግህ : በተወደደ : ልጅህ : እንዴህ : ሲል :: ለምኑ : ይሰ ጣችኋልም :: እሹም : ታገኙማላችሁ :: ደጅንም : ምቱ : ይ ከፈትላችኋልም :: አሁንም : እኛ : እንለምንሃለንና : ስጠነ :: እኛም : እንሻለንና : እናገኝም : ዘንድ : አድርግልን :: እኛ ም : ደጅን : እንመታለንና : ክፈትልን :: {ይህ : / ይች :} ሕፃን : ያነን : ሰማያዊ : ማፀብህን : የዘላለምን : በረከት : በጌታችን : በ የሱስ : ክርስቶስ : ተስፋ : ስለ : አስደረግሀው : {እንዲቀበ ል : / እንድትቀበል :} ወደ : ዘላለምም : መንግሥት : {እንዲደርስ :: / እንድትደርስ ::} አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ጉባኤ : ይነሡ : ቄስም : እንዴህ : ይበል ::

የወንጌልን : ነገር : በቅዱስ : ማርቆስ : ባሥረኛ : ምዕራ ፍ : ባሥራ : ሶስተኛ : ነቍጣም : የተገኘውን : ስሙ : እንዴ ህ : ሲል ::

ሕፃናትን : ወደርሱ : አመጡ : ይደሳቸው : ዘንድ :: ደቀ : መዛሙርት : ግን : ያመጥዋቸውን : ተቈጥዋቸው :: የሱስ ም : ባያቸው : ጊዜ : አዘነ : አላቸውም :: ሕፃናትን : ወደኔ :



አስመጡ : አትከልክልዋቸውም :: የእግዚአብሔር : መን ግሥት : እንደርሳቸው : ላሉት : ናትና :: እውነት : እላችኋ ለሁ :: መንግሥተ : እግዚአብሔርን : እንደ : ሕፃን : የማይ ቀበል : አይገባባትም :: በብብቱም : አኖራቸው :: እጁንም : ጫነባቸው : ባረካቸውም ::

ከዚያም : በኋላ : ቄስ : ይህነን : ምክር : በዚህ : በ ወንጌል : ነገር : ይጨምር ::

ወዳጆቼ : ሆይ :: በዚህ : ወንጌል : የክርስቶስን : የመድኃኒ ታችነን : ነገር : ሕፃናትን : ወደርሱ : ማምጣት : እንዳዘዘ :: ሊከለክልዋቸውም : ይፈልጉ : የነበሩትን : እንደ : ገሠጻቸ ው :: ሰውንም : ሁሉን : የሕፃናትን : ደውሂት : ለመከተል : እንደ : መከረ : ሰማችሁ :: እላንትም : በማድረጉ : ወደር ሳቸው : ያለውን : ውዴን : እንደ : ገለጸው : ታስተውላላች ሁ :: በብብቱ : አኑርዋቸዋልና : እጁንም : ጫነባቸው : ባረ ካቸውም :: ስለዚህም : አትጠራጠሩ : በውነት : እመኑበ ት : እንጅ : እርሱ : {ይህነን : / ይችን :} ከዚህ : {ያለውን : / ያለችውን :} ሕፃ ን : ደግሞ : በፍቅር : እንዲቀበል : በምህረቱም : ብብት : {እንዲያኖረው : / እንዲያኖራት :} የዘላለምንም : መንግሥት : {እንዲከ ፍልለት :: / እንዲከ ፍልላት ::} ስለዚህም : እኛ : በሰማያዊ : አባታችን : ፍቅ ር : {ወደዚህ : / ወደዚች :} ሕፃን : በልጁ : በየሱስ : ክርስቶስ : እንደ : ገለጸ : እንዴህ : እንታመን : እርሱ : ይህነን : የፍቅርን : ስ ራችን : {ይህነን : / ይህችን :} ሕፃን : ወደ : ተቀደሰች : ጥምቀቱ : ማ ምጣታችን : እንዲቀበል : ከቶ : እንደንጠራጠር :: በሃይማ ኖትና : በፍርሃትም : እናመስግነው : እንዴህ : ስንል ::

ሁሉን : የምትችል : የዘላለም : አምላክ : ሆይ : ሰማያ ዊ : አባታችን :: ጸጋህን : ለማወቅ : ባንተም : ለማመን : በ ምህረትህ : ጸርተህናልና : በትሕትና : እናመሰግንሃለን :: ይ

ህችን ፡ ዕውቀት ፡ አብዛልን ። ይህችንም ፡ ሃይማኖት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ በልባችን ፡ አጽና ። ቅዱስ ፡ መንፈስህንም ፡ ስጥ ፡ { ለዚህ ፡ / ለዚች ፡ } ሕፃን ፡ ሁለተኛ ፡ { ይወልደው ፡ / ይወልዳት ፡ } ዘንድ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ወራሽ ፡ { ይሆን ፡ / ትሆን ፡ } ዘንድ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ በሚኖር ፡ በሚገዛም ፡ አሁንና ፡ ወትሮ ። አሜን ።

ቄስም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ለክርስትና ፡ አባቶችና ፡ እናቶች ፡ ይንገር ፡ እንዲህ ፡ ሲል ።

ወዳጆቼ ። { ይህነን ፡ / ይህችን ፡ } ሕፃን ፡ ወዲህ ፡ ለመጠመቅ ፡ አመጣችሁ ። ጌታችንም ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ምህረቱ ፡ መጠን ፡ { እንዲቀበለው ፡ ኃጢአቱንም ፡ ይቅር ፡ እንዲለው ፡ / እንዲቀበላት ፡ ኃጢአትዋንም ፡ ይቅር ፡ እንዲላት ፡ } በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ { እንዲቀድሰው ፡ / እንዲቀድሳት ፡ } የሰማይንም ፡ መንግሥት ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ { እንዲሰጠው ፡ / እንዲሰጣት ፡ } ጸለያችሁ ። ጌታችን ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ይህነን ፡ የለመናችሁትን ፡ ነገር ፡ ለሕፃን ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ በወንጌል ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ አስደረገ ፡ ሰማችሁ ። አሁንም ፡ እርሱ ፡ ለራሱ ፡ ይህችን ፡ ተስፋ ፡ ይጠብቃል ፡ ይፈጽማትም ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጅትዋል ። ስለዚህም ፡ { ለዚህ ፡ / ለዚች ፡ } ሕፃን ፡ ደግሞ ፡ እላንት ፡ ዋሶች ፡ { የምትሆኑለት ፡ እርሱ ፡ / የምትሆኑላት ፡ እርስዋ ፡ } ባፋችሁ ፡ የታመነችውን ፡ ተስፋ ፡ { ያስደርግ ፡ / ታስደርግ ፡ } ዘንድ ፡ { ይገባዋል ፡ ዕድሜው ፡ / ይገባታል ፡ ዕድሜዋ ፡ } እስኪፈጽም ፡ ድረስ ፡ { እርሱም ፡ ባፉ ፡ እስኪችለው ፡ / እርስዋም ፡ ባፏ ፡ እስክትችለው ፡ } ድረስ ። ዲያብሎስንና ፡ የሰይጣንን ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ { እንደ / እንድ



ክድ ፡ / ትክድ ፡ } በእግዚአብሔርም ፡ በቅዱስ ፡ ቃሉ ፡ { ጸንቶ ፡ እንዲያምን ፡ / ጸንታ ፡ እንድታምን ፡ } ለትእዛዙም ፡ { እንዲታዘዝ ፡ / እንድታዘዝ ፡ } ስለዚህም ፡ እጠይቃችኋለሁ ። { አንተ ፡ በዚህ ፡ / አንቺ ፡ በዚች ፡ } ሕፃን ፡ ስም ፡ ዲያብሎስንና ፡ ስራውን ፡ ሁሉን ፡ ያለምንም ፡ ከንቱ ፡ የሚያልፈውን ፡ ሽልምና ፡ ክብር ፡ የሥስትንም ፡ መናፈቅ ፡ ሁሉ ፡ የሥጋውም ፡ ሥጋዊ ፡ ፈቃድ ፡ { ትክደለህን ፡ እንደትከተለው ፡ እንደትሐድበትምን ። / ትክጃለሽን ፡ እንደትከተይው ፡ እንደትሔጅበትምን ። }

ምላሽ ። ይህነን ፡ ሁሉ ፡ እክዳለሁ ።

ቄስ ። ታምናለህን ፡ (ታምኛለሽን) ፡ ሁሉን ፡ በሚችል ፡ በእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ፈጣሪ ።

ባንድ ፡ ልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። እንደ ፡ ተረገዘ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ። እንደ ፡ ተወለደም ፡ ከማርያም ፡ ድንግል ። መከራም ፡ እንደ ፡ ተቀበለ ፡ በጲላጦስ ፡ በጴንጤናዊ ፡ ዘመን ። እንደ ፡ ተሰቀለም ፡ እንደ ፡ ሞተም ፡ እንደ ፡ ተቀበረም ። ወደ ፡ ሢኦልም ፡ እንደ ፡ ወረደ ። በሦስተኛም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ። ወደ ፡ ሰማይም ፡ እንደ ፡ ወጣ ። ሁሉንም ፡ ወደሚችል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ቀኙ ፡ እንደ ፡ ተቀመጠ ። ከዚያውም ፡ እንዲመለስ ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ለመፍረድ ።

ታምናለህምን ፡ (ታምኛለሽምን ፡) በመንፈስ ፡ ቅዱስ ። ባንዲትም ፡ ቅድስትና ፡ ከቶሊካዊት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። በቅዱሳንም ፡ አንድነት ። በኃጢአትም ፡ ስርየት ። በሥጋም ፡ ትንሣኤ ። በዘላለምም ፡ ሕይወት ።

ምላሽ ። ይህናን ፡ ሁሉ ፡ ጸንቼ ፡ አምናለሁ ።

ቄስ ። በዚችም ፡ ሃይማኖት ፡ { ትጠመቅ ፡ / ትጠመቂ ፡ } ዘንድ ፡ { ትሻለህን ። / ትሻለሽን ። }

ምላሽ ፡፡ ይህ ፡ መሻቴ ፡ ነው ፡፡

ቄስ ፡፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቅዱስ ፡ ፈቃዱንና ፡ ትእዛዛ
ቱን ፡ {ጠብቀህ ፡ ትታዘዝላቸው ፡ ዘንድ ፡ የሕይወትህ / ጠብቀሽ ፡ ትታዘዢላቸው ፡ ዘንድ ፡ የሕይወትሽ}
ንም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ {ትመላለስባቸው ፡ / ትመላለሺባቸው ፡} ዘንድ ፡ {ትሻለ / ትሻለ}
{ህን ፡፡ / ሽን ፡፡}

ምላሽ ፡፡ እሻለሁ ፡፡

ይዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ይጸልይ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡

የምህረት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ {ለዚህ ፡ / ለዚች ፡} ሕፃን ፡ ጸጋህን ፡
ስጥ ፡ አሮጊት ፡ {ሰውነቱ ፡ በርሱ ፡ / ሰውነትዋ ፡ በርስዋ ፡} ተቀብሬ ፡ አዲስ ፡
{ሰውነቱ ፡ በርሱ ፡ / ሰውነትዋ ፡ በርስዋ ፡} ትነሣ ፡ ዘንድ ፡፡ አሜን ፡፡

ሥጋዊ ፡ ፍትወት ፡ ሁሉ ፡ {በርሱ ፡ / በርስዋ ፡} ይሞት ፡ ዘንድ ፡ የ
መንፈስ ፡ ነገርም ፡ ሁሉ ፡ ሕያው ፡ {ይሆንበት ፡ ዘንድ ፡ ያድ / ይሆንባት ፡ ዘንድ ፡ ያድ}
{ግበትም ፡ / ግባትም ፡} ዘንድ ፡ ጸጋህን ፡ {ስጠው ፡፡ / ስጣት ፡፡} አሜን ፡፡

በዲያብሎስ ፡ በዓለምም ፡ በሥጋም ፡ ላይ ፡ ድል ፡ {ይነሣ ፡ / ትነሣ ፡}
ዘንድ ፡ ኃይልና ፡ ብርታትን ፡ {ስጠው ፡፡ / ስጣት ፡፡} አሜን ፡፡

ከዚህም ፡ ላሉ ፡ በሹመታችንና ፡ በማገልገላችን ፡ ላንተ ፡ ለተቀደሰ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መንፈስህን ፡ የዘላለምንም ፡ ደህ ንነት ፡ ስጥ ፡ በምህረትህ ፡ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የምትኖ ር ፡ ሁሉንም ፡ የምትገዛ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የተወደደ ፡ ልጅህ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ለኃጢአታ ችን ፡ ስርየት ፡ ከተመሰገነ ፡ ጐኑ ፡ ውኃውንና ፡ ደምን ፡ አፈ ስዋልና ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፡ ወጥተው ፡ አሕዛብን ፡ ሁ



ሉን ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ በአብም ፡ በወልድም ፡ በመን ፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ ያጠምቁቸው ፡ ዘንድ ፡ አዝዋቸዋ ልና ፡፡ የጉባዔህን ፡ ልመና ፡ ታደምጽ ፡ ዘንድ ፡ እንለምንሃ ለን ፡፡ ይህነንም ፡ ውኃ ፡ ለመንፈስ ፡ የኃጢአት ፡ መታጸብያ ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀድስ ፡፡ {ይህም ፡ / ይህችም ፡} አሁን ፡ {የሚጠመቅ / የምትጠመ}
{በት ፡ / ቅበት ፡} ሕፃን ፡ የጸጋህን ፡ ምላት ፡ {ይቀበል ፡ / ትቀበል ፡} ዘንድ ፡
ለወትሮም ፡ በሚያምኑ ፡ በተመረጹም ፡ ልጆችህ ፡ ቍጥር ፡
{ይኖር ፡ / ትኖር ፡} ዘንድ ፡ ውደድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታ
ችን ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ሕፃኑን ፡ በጁ ፡ ይውሰድ ፡ የክርስትናን ፡ አባቶችና ፡ እናቶች ፡ እንዲህ ፡ ብ ሎ ፡ ይንገራቸው ፡፡

{ለዚህ ፡ / ለዚች ፡} ሕፃን ፡ ስምን ፡ አውጡ ፡፡

ስሙንም ፡ ሲያወጡ {ለት ፡ / ላት ፡} እርሱ ፡ በዚህ ፡ ስም ፡
ጸርቶ ፡ ሕፃኑን ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ያጥልቅ ፡ ወይስ ፡ ውኃ
ውን ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ ያፈስስበት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡

ም ፡ ም ፡ እኔ ፡ {አጠምቅሃለሁ ፡ / አጠምቅሻለሁ ፡} በአብ ፡ በወልድም ፡
በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ ይበል ፡፡

{ይህነን ፡ / ይህችን ፡} ሕፃን ፡ ወደ ፡ ጉባኤ ፡ ወደ ፡ ክርስቶስ ፡ መንጋ ፡
{እንቀበለዋለን ፡ / እንቀበላታለን ፡} *በመስቀልም ፡
ምልክት ፡ {እናመልክተዋለን ፡ / እናመልክታታለን ፡} በዚ
ህ ፡ አሳደትን ፡ {እርሱ ፡ / እርስዋ ፡} ከንጊደህ ፡

*ቄስ ፡ ይህነን ፡ ሲ ል ፡ የመስቀልን ፡ ም ልክት ፡ ያድርግ ፡ በሕ ፃን ፡ ግምባር ፡ ላይ ፡፡

ወደህ ፡ በተሰቀለ ፡ በክርስቶስ ፡ ያለቻውን ፡ ሃይማኖት ፡ {ያስታውቅ ፡ / ታስታውቅ ፡} ዘንድ፡ {እንደያፍር ፡ / እንደታፍር ፡} ከባይረቁም ፡ በታች ፡ ኃጢአትን ፡ ዓለምንም ፡ ሰይጣንንም ፡ {ደፋሮ ፡ ይዋጋ ፡ / ደፋራ ፡ ትዋጋ ፡} ዘንድ ፡ የክርስቶስም ፡ የታመነ ፡ ወታደሩና ፡ ባርያው ፡ {ደኖር ፡ / ትኖር ፡} ዘንድ ፡ እስከ ፡ {ሕይወቱ ፡ / ሕይወትዋ ፡} መጨረሻ ፡ ድረስ ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ፡፡

አሁንም ፡ እጅግ ፡ የተወደዳችሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ {ይህነን ፡ / ይህችን ፡} ሕፃን ፡ የሁለተኛ ፡ ልደት ፡ ምልክት ፡ እንደ ፡ {ተቀበለ ፡ / ተቀበለች ፡} በክርስቶስም ፡ ሥጋ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ብልት ፡ {ሁኖ ፡ / ሁና ፡} እንደ ፡ {ተተከለ ፡ / ተተከለች ፡} አይተን ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስለዚህ ፡ ቸርነቱ ፡ እናመስግን ፡፡ {ይህም ፡ / ይህችም ፡} ሕፃን ፡ {ሕይወቱን ፡ / ሕይወትዋን ፡} እንደ ፡ {ጀመረ ፡ / ጀመረች ፡} {እርሱ ፡ / እርስዋ ፡} ደግሞ ፡ በሚመጣ ፡ {ዕድሜው ፡ / ዕድሜዋ ፡} ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ {ይሆን ፡ / ትሆን ፡} ዘንድ ፡ አሁን ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ ሁነን ፡ እንለምነው ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ሁላቸው ፡ ተምበርክከው ፡ ይጸልዩ ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችንን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅርም ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ለኛ ፡ ያለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ፡፡ አሜን ፡፡



ከለልባችን ፡ እናመሰግንሃለን ፡ በሁሉ ፡ መሓሪ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ {ለዚህ ፡ / ለዚች ፡} ሕፃን ፡ የሁለተኛን ፡ ልደት ፡ የጸጋህንም ፡ ልጅነት ፡ ምልክት ፡ {ትሰጠው ፡ / ትሰጣት ፡} ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያንህም ፡ {ትተክለው ፡ / ትተክላት ፡} ዘንድ ፡ ወደሃልና ፡፡ በትሕትናም ፡ እንለምንሃለን ፡ {እርሱ ፡ / እርስዋ ፡} ከኃጢአት ፡ {ሙቶ ፡ / ሙታ ፡} ለጽድቅም ፡ {ሕያው ፡ ሁኖ ፡ / ሕያውት ፡ ሁና ፡} ከክርስቶስም ፡ ጋራ ፡ በሞቱ ፡ {ተቀብሮ ፡ / ተቀብራ ፡} አሮጊት ፡ {ሰውነቱን ፡ / ሰውነትዋን ፡} ለመስቀል ፡ የኃጢአትንም ፡ ሁላንትና ፡ በጣም ፡ ለመሻር ፡ ጸጋህን ፡ {እንድትሰጠው ፡፡ እርሱም ፡ / እንድትሰጣት ፡፡ እርስዋም ፡} በልጅህ ፡ ሞት ፡ ተከፋይ ፡ እንደ ፡ {ሆነ ፡ / ሆነች ፡} እንዲህም ፡ በትንሣኤው ፡ ተከፋይ ፡ {ይሆን ፡ / ትሆን ፡} ዘንድ ፡ በመጨረሻም ፡ ከቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ የዘላለምን ፡ መንግሥትህ ፡ {ደወርስ ፡ / ትወርስ ፡} ዘንድ ፡ በክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ቄስ ፡ የክርስትናን ፡ አባቶችና ፡ እናቶች ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይንገራቸው ፡፡

{ይህ ፡ / ይህች ፡} ሕፃን ፡ በላንት ፡ ዋሶች ፡ በሆናችሁ {ለት ፡ / ላት ፡} ባፋችሁ ፡ ሰይጣንና ፡ ሰራውን ፡ ሁሉ ፡ ለመካድ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ለማመን ፡ ለርሱም ፡ ለመገዛት ፡ ተስፋ ፡ {አስደርጓልና ፡ / አስደርጋለችና ፡} እላንት ፡ {ልትጠብቁት ፡ / ልትጠብቋት ፡} ናችሁ ፡ {አእምሮው ፡ / አእምሮዋ ፡}

ሲከፈት : ጊዜ : አሁን : ባፈችሁ : {ያደረገውን : የስለቱ / ያደረገቸውን : የስለ}
ን : የተሰፋውንም : የካይማኖቱንም : / ትዋን : የተሰፋዋንም : የካይማኖትዋንም :} ታላቅነት : {እ / እ
ንዲማር :: / ንድትማር ::} ይህንንም : ነገር : ደህና : {ሊያስታውል : / ልታስታውል :} ስ
ብከትን : {ይሰማ : ዘንድ : / ትሰማ : ዘንድ :} የሐዋርያትንም : ስምቦሎን :
የጌታችንንም : ጸሎት : አሠርቱንም : ቃላት : ሰው : ሁሉ :
በሚናገርበት : ቋንቋ : ለክርስቲያንም : ሁሉ : ለነፍሱ : ደ
ህንነት : ያውቅ : ዘንድ : ያምንም : ዘንድ : የሚገባውን : ነ
ገር : ሁሉ : {እንዲማር :: / እንድትማር ::} በቡኑነትም : ሁሉ : ለእግዚ
አብሔር : ደስ : በሚያሰኝም : አካሔድ : {እንዲያሳድጉት : / እንዲያሳድጒት :}
አድርጉ ::

ወትሮም : {አሳስቡት : / አሳስብዋት :} ጥምቀት : ምልክት : እንዲሆ
ን : ለክርስትናችን : ማለት : የመድኃኒታችንን : የክርስቶስ
ን : ምሳሌ : ለመከተል : እርሱንም : ለመመሰል : እርሱ :
ስለኛ : ሙቶ : እንደ : ተነሣ : እንዲሁም : እኛ : የተጠመቅ
ነ : ከኃጢአት : እንድንሞት : ለጽድቅም : እንድንነሣ : ክ
ፉ : መሻታችንን : ወትሮ : ሸረን : ዕለት : ዕለትም : በበጎ :
ነገር : ሁሉ : አድገን ::

---

ከተኪስሞስ : ማለት : የክርስቲያን : ትምህርት :
ሰው : ሁሉ : ወደ : ኤጲስቆጶስ : ለመጽናት : ወደ :
ቊርባንም : ለመግባት : ሳይደርስ : ይማር :
ዘንድ : የሚፈለግ ::

ጥያቄ :: {ስምህ : / ስምሽ :} ማን : ነው ::

ምላሽ :: ም :: ም ::

ጥያቄ :: ማን : {አወጣልህ : / አወጣልሽ :} ይደነን : ስም ::

ምላሽ :: የክርስትና : አባቶቼና : እናቶቼ : የክርስቶስ :
ብልት : የእግዚአብሔርም : ልጅ : የመንግሥት : ሰማያት
ም : ወራሽ : በሆንሁባት : በጥምቀቴ ::

ጥ :: የክርስትና : {አባቶችህና : እናቶችህ : / አባቶችሽና : እናቶችሽ :} ምን : አደ
ረጉ {ልህ : / ልሽ :} የዚያን : ጊዜ ::

ም :: በስሜ : ሶስት : ነገርን : ተሳሉና : ተስፋውን : አስደ
ረጉ :: በመጀመርያ : ስፍራ : ዲያብሎስንና : ስራውን : ሁሉ :
የዚህ : ክፉ : ዓለምንም : ሽልምና : ጫወታ : የሥጋም : ኃ
ጢአተኛ : ፈቃድ : ሁሉ : እክድ : ዘንድ :: በሁለተኛም : ስ
ፍራ : የክርስቲያንን : ሃይማኖት : ነገር : ሁሉ : አምን : ዘን
ድ :: በሶስተኛም : ስፍራ : የእግዚአብሔርን : ቅዱስ : ፈቃዱ
ንና : ትእዛዛቱን : እጠብቅ : ዘንድ : የሕይወቴንም : ዘመን :
ሁሉ : እመላለስባቸው : ዘንድ ::

ጥ :: እርሳቸውም : {ባንተ : / ባንቺ :} ስፍራ : ተስፋ : እንደ : አ
ስደረጉ : እንዲሁም : {ታምን : ዘንድና : ታደርግ : ዘንድ : እ / ታምኚ : ዘንድና : ታደርጊ : ዘንድ : እ}
ንዲገባህ : አይመስልህምን ::
ንዲገባሽ : አይመስልሽምን ::

ም ። አውን ፡ በጣም ። በእግዚአብሔር ፡ ረዲትም ፡ አደርገዋለሁ ። የሰማዩንም ፡ አባታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ ወደዚች ፡ ደህንነት ፡ ጸርቶኛልና ፡ ከለልቤ ፡ አመሰግነዋለሁ ። ወደ ፡ ሕይወቴም ፡ መጨረሻ ፡ እጸናበት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጸጋውን ፡ እንዲሰጠኝ ፡ እለምናለሁ ።

ጥ ። {የሃይማኖትህን ፡ / የሃይማኖትሽን ፡} ነገር ፡ {ንገረኝ ። / ንገሪኝ ።}

ም ። እኔ ፡ አምናለሁ ፡ ሁሉን ፡ በሚችል ፡ በእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ፈጣሪ ።

ባንድ ፡ ልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። የተረገዘ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ። የተወለደም ፡ ከማርያም ፡ ድንግል ። መከራም ፡ የተቀበለ ፡ በጲላጦስ ፡ በጴንጤናዊ ፡ ዘመን ። የተሰቀለም ። የሞተም ። የተቀበረም ። ወደ ፡ ሲኦልም ፡ የወረደ ። በሶስተኛም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ የተነሣ ። ወደ ፡ ሰማይም ፡ የወጣ ። ሁሉንም ፡ ወደ ፡ ሚችል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ወደ ፡ ቀኙ ፡ የተቀመጠ ። ከዚያም ፡ የሚመለስ ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ሊፈርድ ።

አምናለሁም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ። ባንዲትም ፡ ቅድስትና ፡ ከቶሊካዊት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያን ። በቅዱሳንም ፡ አንድነት ። በኃጢአትም ፡ ስርየት ። በሥጋውም ፡ ትንሣኤ ፡ በዘላለምም ፡ ሕይወት ። አሜን ።

ጥ ። ከዚህ ፡ {ሃይማኖትህ ፡ / ሃይማኖትሽ ፡} ምን ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ {ትማራለህ ። / ትማርያለሽ ።}

ም ። አምን ፡ ዘንድ ፡ እማርበታለሁ ፡

መጀመርያ ። እኔንና ፡ ዓላምን ፡ ሁሉ ፡ በፈጠረ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አብ ።

ሁለተኛ ። እኔንና ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ባዳነ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ወልድ ።

ሶስተኛ ። እኔንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የተመረጹትን ፡ ሕ



ዝብ ፡ ሁሉ ፡ በሚቀድስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ።

ጥ ። የክርስትና ፡ {አባቶችህና ፡ እናቶችህ ፡ ባንተ ፡ / አባቶችሽና ፡ እናቶችሽ ፡ ባንች ፡} ፈንታ ፡ {አንተ ፡ / አንች ፡} የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዛት ፡ {እንድትጠብቅ ፡ / እንድትጠብቂ ፡} ተስፋ ፡ እንደስደረጉ ፡ {አልሀኝና ፡ / አልሽኝና ፡} እርሳቸው ፡ ስንት ፡ ናቸው ፡ {በልልኝ ። / በይልኝ ።}

ም ። አሥር ።

ጥ ። እለማን ፡ ናቸው ።

ም ። እግዚአብሔር ፡ በጻት ፡ መጽሐፍ ፡ በህያ ፡ ምዕራፍ ፡ ያላቸውን ፡ እንደህ ፡ ሲል ።

I. እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ነኝ ። ሌሎች ፡ አማልክት ፡ በፊቴ ፡ አይሁኑልህ ።

II. ሥእልን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌንም ፡ ከቶ ፡ አትስራልህ ። በላይ ፡ በሰማይ ፡ ካለው ። በታችም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ካለው ። በውኃም ፡ ከምድር ፡ በታች ፡ ካለው ። አትስገድላቸው ። አታምልካቸውም ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ቅናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነኝና ። ያባቶችን ፡ ኃጢአት ፡ የምመረምር ፡ በልጆች ፡ እስከ ፡ ሶስተኛ ፡ እስከ ፡ አራተኛም ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በሚጸሉኝ ። መህረትንም ፡ አደርጋለሁ ፡ ለብዙ ፡ ሽህ ፡ ለሚወደኝ ፡ ትእዛዛቴንም ፡ ለሚጠብቁ ።

III. የእግዚአብሔርን ፡ ያምላክህን ፡ ስም ፡ ከንቱ ፡ አታድርገው ። እግዚአብሔር ፡ ስሙን ፡ ከንቱ ፡ ያደረገውን ፡ ሳይቀስፈው ፡ አይተወውምና ።

IV. የሰንበትን ፡ ቀን ፡ አስብ ፡ ትቀድሰው ፡ ዘንድ ። ስድስት ፡ ቀን ፡ ስራ ፡ ተግባርህንም ፡ ሁሉን ፡ አድርግ ። ሰባተኛ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ያምላክህ ፡ ሰንበት ፡ ነውና ፡ በርሱ ፡ ስራን ፡ ሁሉን ፡ አትስራ ፡ አንተ ፡ ወንድ ፡ ልጅህም ፡ ሴት ፡ ልጅህም ፡ ሎሌህም ፡ ገረድህም ፡ ከብትህም ፡ ወይስ ፡ ባገርህ ፡ ያለ ፡ እንግዳ ። በስድስት ፡ ቀን ፡ እግዚአብ

ሔር ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንም ፡ ያለባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ፈጥርዋልና ፡ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ አረፈ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ባረከ ፡ ቀደሰውም ።

V. አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክበር ። ዕድሜህ ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ በሚሰጠህ ፡ ምድር ።

VI. አትግደል ።

VII. አታመንዝር ።

VIII. አትስረቅ ።

IX. ባሰት ፡ አትመስክር ፡ በባልንጀራህ ፡ ላይ ።

X. የባልንጀራህን ፡ ቤት ፡ አትመኝ ። የባልንጀራህንም ፡ ምሽት ፡ አትመኝ ። ባርያውንም ፡ ባርያዪቱንም ። በሬውንም ፡ አህያውንም ፡ ማናቸውንም ፡ ከባልንጀራህ ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ።

ጥ ። ከሌህም ፡ ትእዛዛት ፡ {የተማርሀው ፡ / የተማርሽው ፡} ታላቅ ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። ሁለት ፡ ነገር ፡ አውቅባቸዋለሁ ፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚገባኝ ፡ ወደ ፡ ባልጀራዬም ፡ የሚገባኝ ፡ አገባቤ ።

ጥ ። ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ {የሚገባህ ፡ / የሚገባሽ ፡} ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚገባኝ ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ። አምንበት ፡ ዘንድ ፡ እፈራውም ፡ ዘንድ ፡ ከለልቤም ፡ ከለመንፈሴም ፡ ከለነፍሴም ፡ ከለኃይሌም ፡ ሁሉ ፡ እወደው ፡ ዘንድ ፡ አመልከውም ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ቸርነቱም ፡ አመሰግነው ፡ ዘንድ ፡ መታመኔንም ፡ ሁሉ ፡ አደርግበት ፡ ዘንድ ፡ እጸራበትም ፡ ዘንድ ፡ ቅዱስ ፡ ስሙንና ፡ ቃሉንም ፡ አክብር ፡ ዘንድ ፡ የዕድሜዬንም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በውነት ፡ እገዛለት ፡ ዘንድ ።

ጥ ። ወደ ፡ {ባልንጀራህም ፡ የሚገባህ ፡ / ባልንጀራሽም ፡ የሚገባሽ ፡} ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ።



ም ። ወደ ፡ ባልንጀራዬ ፡ የሚገባኝ ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ። እንደ ፡ ነፍሴ ፡ እወደው ፡ ዘንድ ፡ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ለኔ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ወደድሁ ፡ እንደሁም ፡ እኔ ፡ አደርግለት ፡ ዘንድ ። አባቴንና ፡ እናቴን ፡ እወድ ፡ ዘንድ ፡ አከብራቸውም ፡ ዘንድ ፡ አግዛቸውም ፡ ዘንድ ። ንግሥትንም ፡ ክርስዋም ፡ በታች ፡ የተሾሙትን ፡ ሁሉ ፡ አከብራቸው ፡ ዘንድ ፡ እታዘዝላቸውም ፡ ዘንድ ። ላለቆቼም ፡ ለመምህራኔም ፡ ለመንፈሳውያንም ፡ ጠባቆቼ ፡ እገዛ ፡ ዘንድ ። የሚበልጡኝንም ፡ ሁሉ ፡ ተዋርጄ ፡ አከብራቸው ፡ ዘንድ ። ማንንም ፡ በመንገር ፡ ወይስ ፡ በማድረግ ፡ ላልጐዳ ። ባደራረጌም ፡ ሁሉ ፡ እውነተኛና ፡ ቅን ፡ ልሆን ። ክፋትንና ፡ ጸላትነትንም ፡ በልቤ ፡ ላላሳድር ፡ እጄንም ፡ ከመሙጥሙጥና ፡ ከስርቅ ፡ መላሴንም ፡ ከስድብ ፡ ካሰትም ፡ ከክፉ ፡ ነገርም ፡ ሁሉ ፡ እከለክል ፡ ዘንድ ፡ ሥጋዬንም ፡ እጅግ ፡ በመብላትና ፡ በስካር ፡ ላላከብድ ፡ በንጽሕናም ፡ እንድጠብቀው ። የሌላውን ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ ላልሻ ፡ ተምሬና ፡ ደክሜ ፡ ገንዘቤን ፡ እበላ ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በሚጸራኝ ፡ በንብረቴ ፡ የሚገባኝን ፡ ነገር ፡ አድርግ ፡ ዘንድ ።

ጥ ። ልጄ ፡ ሆይ ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ለማድረግ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ትእዛዛት ፡ ለመመላለስ ፡ ለርሱም ፡ ለመገዛት ፡ {በኃይልህ ፡ / በኃይልሽ ፡} እግዚአብሔር ፡ ልዩን ፡ ምህረቱ ፡ {ባይሰጥህ ፡ እንደይቻልህ ፡ ዕወቅ ፡ / ባይሰጥሽ ፡ እንደይቻልሽ ፡ ዕወቂ ፡} የእግዚአብሔርንም ፡ ልዩ ፡ ምህረት ፡ {አዘውትረህ ፡ / አዘውትረሽ ፡} በመለመን ፡ {ልትሻው ። / ልትሺው ።} ስለ ዚህም ፡ የጌታችነን ፡ ጸሎት ፡ {ብታውቅ ፡ አስማኝ ። / ብታውቂ ፡ አስሚኝ ።}

ም ። አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ። ስምህ ፡ ይቀደስ ። መንግሥትህ ፡ ትምጸ ። ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ። እንጀራችነን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ። ይቅር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ። እኛ ፡ ደግመን ፡

ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ልኛ ፡ ያለባቸውን ። ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ። ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ። አሜን ።

ጥ ። ምን ፡ {ትፈልጋለህ ፡ / ትፈልግያለሽ ፡} ከእግዚአብሔር ፡ በዚች ፡ ጸሎት ።

ም ። እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ የበጐነት ፡ ሁሉ ፡ ሰጭ ፡ ያለ ፡ ለኔና ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ እኛ ፡ እንደ፡ ገባነ ፡ እናከብረው ፡ ዘንድ ፡ እንገዛለትም ፡ ዘንድ ፡ እንታዘዝለትም ፡ ዘንድ ፡ ጸጋውን ፡ እንዲያወርድልን ፡ እለምነዋለሁ ። ለሥጋችንና ፡ ለነፍሳችንም ፡ የሚያሻነን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንዲሰጠን ። ምሕረም ፡ እንዲሆንልን ፡ ኃጢአታችንንም ፡ ይቅር ፡ እንዲበልለን ። ከሥጋና ፡ ከነፍስም ፡ ፍርሃትና ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲጠብቀንና ፡ እንዲረደን ፡ ከኃጢአትና ፡ ከክፋትም ፡ ከሰይጣንም ፡ ከዘላለም ፡ ሞትም ፡ እንዲያድነን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እለምናለሁ ። ይህነንም ፡ በምህረቱና ፡ በቸርነቱ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ እንዲያደርግ ፡ አምኛለሁና ፡ ‘አሜን ፡’ “እንደህ ፡ ይሁን ፡” እላለሁ ።

ጥ ። ስንት ፡ ምሥጢራት ፡ ሠራ ፡ ክርስቶስ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያኑ ።

ም ። ሁለት ፡ ብቻ ፡ እርሳቸውም ፡ ጥምቀትና ፡ ቍርባን ፡ ማለቱ ፡ የጌታችን ፡ እራት ።

ጥ ። ምሥጢር ፡ {ማለትህ ፡ / ማለትሽ ፡} ምንድር ፡ ነው ።

ም ። ለኛ ፡ የተሰጠች ፡ የውሥጥና ፡ የመንፈሳዊት ፡ ጸጋ ፡ ሜደዊትና ፡ የምትታይ ፡ ምልክት ፡ ክርስቶስ ፡ ራሱን ፡ የሠራት ፡ የጸጋው ፡ መቀበያ ፡ መያዣም ፡ አረቡንም ፡ ትሆንለን ፡ ዘንድ ።

ጥ ። ስንት ፡ ክፍል ፡ አለ ፡ በምሥጢር ።

ም ። ሁለት ፡ እርሳቸውም ፡ ሜደዊትና ፡ የምትታይ ፡ ምልክት ፡ ውሥጣዊትና ፡ መንፈሳዊትም ፡ ጸጋ ።

ጥ ። ምን ፡ ሜደዊትና ፡ የምትታይ ፡ ምልክት ፡ ወይስ ፡ መልክ ፡ አለች ፡ በጥምቀት ።



ም ። ውኃ ፡ ሰው ፡ የሚጠመቅበት ፡ በአብና ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ።

ጥ ። ውሥጣዊትና ፡ መንፈሳዊት ፡ ጸጋውም ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። ሞት ፡ ከኃጢአት ፡ አዲስ ፡ ልደትም ፡ ለጽድቅ ። ከፍጥረታችን ፡ በኃጢአት ፡ እንደ ፡ ተወለድነ ፡ የቍጣም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዴሁም ፡ በዚህ ፡ የጸጋ ፡ ልጆች ፡ እንሆናለንና ።

ጥ ። ምን ፡ ይፈለጋል ፡ ከሚጠመቁ ፡ ሰዎች ።

ም ። ከኃጢአት ፡ የሚመለሱባት ፡ ንስሓ ። በዚች ፡ ምሥጢርም ፡ በተደረገች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ ጸንተው ፡ የሚያምኑባት ፡ ሃይማኖት ።

ጥ ። እንኪያስ ፡ ምነው ፡ ሕፃናት ፡ ይጠመቃሉ ፡ ከሕፃንነታቸው ፡ የተነሣ ፡ የሚፈለግባቸውን ፡ ነገር ፡ ይፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡ አይቻላቸውምና ።

ም ። በዋሳቸው ፡ አፍ ፡ ተስፋውን ፡ ያስደርጋሉና ፡ ዕድሜያቸውም ፡ ሲበስል ፡ ጊዜ ፡ ይህችን ፡ ተስፋ ፡ በራሳቸው ፡ ይፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡ ይገባቸዋል ።

ጥ ። ለምንድር ፡ ተሠራች ፡ የቍርባን ፡ ምሥጢር ።

ም ። በክርስቶስ ፡ ሞት ፡ ለሆነች ፡ ምሥዋዕት ፡ ክርስዋም ፡ ለኛ ፡ ለወጣች ፡ በረከት ፡ የወትሮ ፡ ማስታሰቢያ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ።

ጥ ። የቍርባን ፡ ሜደዊ ፡ ክፍልና ፡ ምልክት ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። እንጀራና ፡ የወይን ፡ ጸጅ ፡ ጌታችን ፡ እንቀበለው ፡ ዘንድ ፡ ያዘዘ ።

ጥ ። የተመለከተም ፡ የውሥጥ ፡ ነገርዋ ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። የክርስቶስ ፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ ምእምናን ፡ በቍርባን ፡ በውነት ፡ የሚወስዱና ፡ የሚቀበሉት ።

ጥ ። የምናገኝበትም ፡ በረከት ፡ ምንድር ፡ ነው ።

ም ። ሥጋችን ፡ በንጀራና ፡ በወይን ፡ ጸጅ ፡ እንዲበረታ ፡ እንዲመግብም ፡ እንዴሁም ፡ ነፍሳችን ፡ በክርስቶስ ፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ ትበረታለችና ፡ ትመገባለች ።

ጥ ። ምንድር ፡ ይፈለጋል ፡ ወደ ፡ ቍርባን ፡ ከሚደርሱ ፡ ሰዎች ።

ም ። ባደረጉት ፡ ኀጢአታቸው ፡ በውነት ፡ ያዘኑ ፡ እንደሆን ፡ ባዲስ ፡ ሕይወትም ፡ ይመላለሱ ፡ ዘንድ ፡ በጣም ፡ እንዲፈቅዱ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ምህረት ፡ በክርስቶስ ፡ ጸንተው ፡ ያምኑ ፡ እንደሆን ፡ ሞቱንም ፡ በስብሓት ፡ እንዲያስቡ ፡ ከሰውም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ፍቅር ፡ ያላቸው ፡ እንደሆን ፡ ነፍሳቸውን ፡ ሊመርምሩ ።

---

## የማጽናት ፡ ምሳሌ ፡

ኤጲስቆጶስ ፡ ተጠምቀው ፡ ወደ ፡ ዕውቀት ፡ ዕድሜ ፡ በደረሱ ፡
እጁን ፡ ሲጭንባቸው ፡ በክርስትና ፡
ያጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቍርባንም ፡
ያገባቸው ፡ ዘንድ ።

ለማጽናት ፡ በተደረገ ፡ ቀን ፡ የሚጸኑ ፡ ሰዎች ፡ በሥርዓት ፡ በኤጲስቆጶስ ፡ ፊት ፡ ቁመው ፡ እርሱ ፡ (ወይስ ፡ በርሱ ፡ ፈንታ ፡ ያደረገው ፡ ቄስ ፡) ከዚህ ፡ የሚከተለውን ፡ ነገር ፡ ይድገም ።

ማጽናት ፡ ለተቀባዮቹ ፡ ለመሥራታቸው ፡ ይጠቅም ፡ ዘንድ ፡ ብላ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይህነን ፡ ታዝ ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ መሰላት ፡ ከንጊዜህ ፡ በማንም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እጅ ፡ እንደይጫን ፡ የሐዋርያትን ፡ ስምቦሎን ፡ የጌታችንንም ፡ ጸሎት ፡ አሥርቱ ፡ ቃላትንም ፡ ባያውቅ ፡ የታናሽ ፡ ክተኪስሞስንም ፡ ጥያቄ ፡ ለመመለስ ፡ ባይቻል ። ይህችም ፡ ትእዛዝ ፡ መጠበቅ ፡ ትፈልጋለች ፡ ወደ ፡ ዕውቀት ፡ እድሚያቸው ፡ የደረሱ ፡ የክርስትና ፡ አባቶቻቸውና ፡ እናቶቻቸው ፡ በጥምቀት ፡ በርሳቸው ፡ ፈንታ ፡ ያስደረጉትን ፡ ተስፋ ፡ የተማሩ ፡ ልጆች ፡ አሁን ፡ ራሳቸውን ፡ ባፋቸውና ፡ በፈቃዳቸው ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ይቀበሉትና ፡ ያጸኑት ፡ ዘንድ ፡ ለማድረጉም ፡ እሺ ፡ ያሉትን ፡ ነገር ፡ ታምነውና ፡ ደክመው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ወትሮ ፡ ለመፈጸሙ ፡ ይጋደሉ ፡ ዘንድ ።



ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ይበል ።

እላንትን ፡ ከዚህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በዚችም ፡ ጉባኤ ፡ ፊት ፡ ያችን ፡ ቅድስት ፡ ተስፋ ፡ ስለት ፡ በስማችሁ ፡ በጥምቀታችሁ ፡ ጊዜ ፡ የተደረገቸውን ፡ ታድሳላችሁን ፡ በነፍሳችሁም ፡ እሺ ፡ ትሉበታላችሁን ። የክርስትና ፡ አባቶቻችሁና ፡ እናቶቻችሁም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በላንት ፡ ስፍራ ፡ ታምኑ ፡ ዘንድ ፡ ታድርጉም ፡ ዘንድ ፡ ታስፈ ፡ ያስደረጉትን ፡ ይህነንም ፡ እንፈጽም ፡ ዘንድ ፡ በጣም ፡ ይገባናል ፡ ትላላችሁን ።

ሁሉም ፡ ኢያንዳንዳቸው ፡ በሚሰማ ፡ ድምጽ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።

አዎን ።

ኤጲስቆጶስ ። ረዲታችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ነው ።

ምላሽ ። ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በፈጠረ ።

ኤጲስ ። የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ።

ም ። ለዘላለም ።

ኤጲስ ። አቤቱ ፡ ልመናችነን ፡ ስማ ።

ም ። ጩኸታችንም ፡ ወደንተ ፡ ይድረስ ።

ኤጲስ ። እንጸልይ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ ለዘላለምም ፡ የምትኖር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። አንተ ፡ እሌህን ፡ ባሮችህ ፡ በውኃና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሁለተኛ ፡ ትወልድ ፡ ዘንድ ፡ የኀጢአታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ስርያት ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ፈቅደሃልና ። እንለምንሃለን ፡ አቤቱ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በጰራቅሊጦስ ፡ አጽናቸው ፡ የጸጋህንም ፡ ብዙና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስጥወታ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ አብዛላቸው ፡ የጥበብና ፡ የአእምሮን ፡ መንፈስ ። የምክርና ፡ የመንፈሳዊት ፡ ኃይልን ፡ መንፈስ ። የዕውቀትንና ፡ የደህና ፡ አምልኮትን ፡ መንፈስ ፡ የተቀደሰችም ፡ ፍርሃትህ ፡ መንፈስ ፡ ምላባቸው ፡ አቤቱ ፡ አሁንና ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

በኋላ ፡ ኢያንዳንዳቸው ፡ በየሥርዓቱ ፡ ወደ ፡ ኤጲስ

256



ቀጾስ ፡ ይድረስ ፡ በፊቱም ፡ ይምበርክክ ፡ ኢጲስ ቆጶስም ፡ እጁን ፡ በየራሱ ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፡ እንደህ ፡ ይበል ፡፡

በሰማያዊት ፡ ጸጋህ ፡ አቤቱ ፡ {ይህነን ፡ / ይህችን ፡} ልጅህ ፡ (ባርያህ ፡) ለዘወትር ፡ ላንተ ፡ {ይሆን ፡ / ትሆን ፡} ዘንድ ፡ በቅዱስ ፡ መንፈስህ ም ፡ {ጨምር ፡ ይበዛ ፡ / ጨምራ ፡ ትበዛ ፡} ዘንድ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ መንግሥ ትህ ፡ {እስኪደርስ ፡ / እስክትደርስ ፡} ድረስ ፡ {ጠብቀው ፡፡ / ጠብቃት ፡፡} አሜን ፡፡

በኋላም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እንደህ ፡ ይበል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ከላንት ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡፡
ም ፡፡ ከመንፈስህም ፡ ጋራ ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁላቸው ፡ ተንበርክከው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እንደህ ፡ ይበል ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችነን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ለኛ ፡ ያለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጀ ፡፡ አሜን ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ ለዘላለምም ፡ የምትኖር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ በጎን ፡ ለአምላካዊት ፡ ግርማህም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ነገር ፡ እንወድ ፡ ዘንድ ፡ እንፈጽመውም ፡ ዘንድ ፡ ያንተ ፡ ስራ ፡ ብቻ ፡ ነውና ፡፡ በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ ለሌህ ፡ ባሮችህ ፡፡ የተቀደሱ ፡ ሐዋርያትህ ፡ እንደደረጉ ፡ እንደሁም ፡ እኛ ፡ አሁን ፡ ወደርሳቸው ፡ ያለሃትን ፡ ሞገስና ፡ ቸርነት ፡ እናመልክትላቸው ፡ ዘንድ ፡ ብለን ፡ እጃችነን ፡ ጫነባቸው ፡ እንለምንህማለን ፡ ያባትነት ፡ እጅህ ፡ ለወትሮ ፡ በላያቸው ፡ ትሁን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህም ፡ ወትሮ ፡ ከርሳቸው ፡ ጋ



ራ ፡ ይሁን ፡ በቃልህም ፡ ዕውቀትና ፡ መታዘዝ ፡ ይምራቸው ፡ እርሳቸው ፡ በመጨረሻ ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንዲያገኙ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ካንተና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ ጋራ ፡ በሚኖር ፡ በሚገዛም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡፡ በትእዛዛትህ ፡ መንገድ ፡ በሕጋጋትህም ፡ ስራ ፡ ልባችነንና ፡ ሥጋችነን ፡ ታቀና ፡ ዘንድ ፡ ትቀድስም ፡ ዘንድ ፡ ትገዛም ፡ ዘንድ ፡ እንድትወድ ፡ እንለምንሃለን ፡ እኛ ፡ ከዚህና ፡ ለዘላለም ፡ በታላቅ ፡ ኃይልህ ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡ እንጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ በጌታችንና ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡ ይባርካቸው ፡፡

ሁሉን ፡ የሚችል ፡ የእግዚአብሔር ፡ የአብ ፡ የወልድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በረከት ፡ በላያችሁ ፡ ትሁን ፡ ከላንት ፡ ጋራም ፡ ትኑር ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

---

* ከቶ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ቍርባን ፡ አይድረስ ፡ ለመጽናት ፡ የተዘጋጀ ፡ ሳይሆን ፡፡



## የመጋባት ፡ ቅዳሴ ፡፡

¶ ደጋቡ ፡ ዘንድ ፡ የሚሹ ፡ ሰዎች ፡ እንደሉ ፡ ማጫታቸው ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሶስት ፡ በሚከታተሉ ፡ ሰንበታት ፡ በጽዋት ፡ ወይስ ፡ በማታ ፡ ጸሎት ፡ ጊዜ ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ጀሮ ፡ ይወራ ፡ ቄስ ፡ አውሮት ፡ ከሁለተኛ ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ማንበብ ፡ በኋላ ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡

——ና ፡ —— ፡ መጋባትን ፡ ሽተው ፡ እንደ ፡ ታጩ ፡ አወራለሁ ፡፡ ማንም ፡ የሌህ ፡ ሁለቱን ፡ ቅድስት ፡ መጋባት ፡ የሚከለክለውን ፡ ደህና ፡ መክንያት ፡ ቢያውቅ ፡ ያስታውቀው ፡፡ ደህ ፡ የመጠየቂ ፡ መጀመርያ ፡ (ሁለተኛ ፡፡ ሶስተኛ ፡) ጊዜ ፡ ነው ፡፡

¶ መጋባትንም ፡ የሚሹ ፡ በተለዩ ፡ ጉባኤዎች ፡ ቢኖሩ ፡ ማጫታቸው ፡ በሌህ ፡ ሁለት ፡ ጉባኤዎች ፡ ሊወራ ፡ ነው ፡፡ ያንደኚት ፡ ጉባኤም ፡ ቄስ ፡ አያገባቸው ፡ የሚመሰክርውን ፡ ወረቀት ፡ ከሁለትኛ ፡ ጉባኤ ፡ ቄስ ፡ ካልተቀበለ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ከጠየቁ ፡ በኋላ ፡፡

ለመጋባት ፡ በተደረገ ፡ ቀን ፡ በጊዜው ፡ ጦኞች ፡ ከወዳጆቻቸውና ፡ ከዘመደቻቸው ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ደምጡ ፡፡ ወንድም ፡ ወደ ፡ ቄስ ፡ ወደ ፡ ቅኙ ፡ ሴትም ፡ ወደ ፡ ግራው ፡ ደቆሙ ፡፡ ስም ፡ እንደህ ፡ ደበል ፡፡

ወዳጆቼ ፡ ሆይ ፡፡ እኛ ፡ ከዚህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በዚች ፡ ጉባኤም ፡ ፊት ፡ ተሰበሰብነ ፡ ለቅድስት ፡ መጋባት ፡ ደህነን ፡ ወንድና ፡ ደህችን ፡ ሴት ፡ እናገናኝ ፡ ዘንድ ፡፡ መጋባት ፡ ግን ፡ የከበረች ፡ ንብረት ፡ ናት ፡፡ ከእግዚአብሔር ፡ ካደም ፡ ኃጢአት ፡ በፊት ፡ የተዘጋጀች ፡፡ በክርስቶስና ፡ በቤተ ፡ ክር



ስቲያንም ፡ መኻከል ፡ ያለቸውን ፡ አንድነት ፡ ትመስላለች ፡፡ ደህችንም ፡ ቅድስት ፡ ንብረት ፡ ክርስቶስ ፡ አከበራት ፡ አመሰገናትም ፡ እርሱ ፡ በቃና ፡ በገሊላ ፡ በሰርግ ፡ ሁኖ ፡ ፊተኛውን ፡ ታምራቱን ፡ አድርጎልና ፡፡ ጳውሎስም ፡ ደግሞ ፡ ደህችን ፡ ንብረት ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ መኻከል ፡ እናከብራት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡፡ ስለዚህ ፡ ማንም ፡ ወደርስዋ ፡ ያለ ፡ ማሰብ ፡ አደግባ ፡፡ በቃሊል ፡ ልብም ፡ ወይስ ፡ በድፍረት ፡፡ የሥጋ ፡ ፈቃድና ፡ መሻት ፡ ሊያጸግብ ፡ ብቻ ፡ አእምሮ ፡ እንደ ፡ ሌለው ፡ እንስሳ ፡፡ በክብር ፡ እንጂ ፡፡ በፍርሃትም ፡፡ በማሰብም ፡፡ ልብም ፡ በዓለም ፡ ነገር ፡ ሳይከብድ ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ፍርሃትም ፡፡ ለምን ፡ መክንያትም ፡ መጋበት ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀች ፡ ምልካምም ፡ አስቦ ፡፡ መጋባት ፡ ተሠርታለችና ፡

፩፡፡ ልጆችን ፡ ለመውለድ ፡፡ እርሳቸውንም ፡ ለማሳደግ ፡ በተግሣጽና ፡ በምክር ፡ ለእግዚአብሔር ፡፡ ለቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ምስጋና ፡፡

፪፡፡ እርስዋም ፡ የኃጢአት ፡ መከልከያ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጀች ፡፡ ከዝሙት ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ፡፡ የብችነትም ፡ ስጥወታ ፡ የሌላቸው ፡ ያጋቡ ፡ ዘንድ ፡ ራሳቸውንም ፡ ሊጠብቁ ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሥጋው ፡ ብልቶች ፡ ርኩሳት ፡ እንደ ፡ ሌላቸው ፡፡

፫፡፡ እርሱዋም ፡ ባልና ፡ ምሽት ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ በደስታ ፡ በመከራም ፡ ረዷትና ፡ ማጽናት ፡ ደሆኑላቸው ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጀች ፡፡

እለዚህ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ስለዚህ ፡ መክንያት ፡ በዚች ፡ ቅድስት ፡ ንብረት ፡ ሊገናኙ ፡ መጡ ፡፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ ቅን ፡ መክንያት ፡ መንገር ፡ የሚችል ፡ እንደ ፡ ሥርዓት ፡ ካለው ፡ መጋባት ፡ የሚከለከላቸው ፡፡ እርሱ ፡ አሁን ፡ ደንገር ፡ ወይስ ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ለወትሮ ፡ ዝም ፡ ደበል ፡፡

---

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ቄስ ፡ ለጫኞች ፡ ደበል ፡፡

እኔ ፡ እላንትን ፡ ሁለታችሁን ፡ እመሰክራችኋለሁ ፡፡ በሚያስፈራ ፡ የልብ ፡ ሁሉ ፡ መሥጢር ፡ በሚገለጽበት ፡ በ

ፍርድ : ቀን : ምላሽ : ልትሰጡ : ትሆናላችሁና :: አንድ : ከላንት : አንዷችን : ቢያውቅ : እንደ : ሥርዓት : ካለች : ከቅድስት : መጋባት : ከማስማማቱ : የሚከለክላችሁ : አሁን : ልትናገሩት :: ይህነንም : በውነት : እወቁና :: በሌላ : በእግዚአብሔር : ቃል : ባልታዘዘ : መንገድ : የተሰማሙ : ሁሉ : እግዚአብሔር : አላገናኛቸው :: መጋባታቸውም : እንደ : ሥርዓት : አይደለችምና ::

---

በዚያም : ለመጋባት : በተደረገ : ቀን : ሰው : አንዷችን : በእግዚአብሔር : ሕግ : ወይስ : በመንግሥት : ሕግ : ከመጋባት : የሚከለክላቸውን : ነገር : ቢያመጣ : ዋሶችንም : ይዞ : ከጨኞች : ጋራ : በዚያ : መከልከያ : መክንያት : ይፈራረድ : ዘንድ : ቢሻ : እውነቱ : እስኪገለጽ : ድረስ : መጋባት : ይቅር ::

መከልከያ : የለም : ብለው : ቢሉ : ቄስ : ወንድን : እንዲህ : ይጠየቅ ::

ይህችን : ሴት : ምሽትህ : ትሆን : ዘንድ : ከርስዋም : ጋራ : እንደ : እግዚአብሔር : ትእዛዝ : ባንድ : ትኖር : ዘንድ : በቅድስት : መጋባት : ትሻለህን :: እርስዋን : ትወደለህን :: ታጽናትማለህን :: ታከብሬትማለህን :: በሕማምና : በጤናም : ትጠብቃታለህን :: ሌላውንም : ሁሉን : ትተህ : እርስዋን : ብቻ : ትከተላለህን : በሁለታችሁ : ዕድሜያችሁ : ሁሉ ::

ወንድ : ይመልስ ::

አወን : ይህ : ፈቃዴ : ነው ::

ከዚህም : በኋላ : ቄስ : ሴትን : እንዲህ : ይጠየቅ ::

ይህነን : ወንድ : ባልሽ : ሊሆን : ከርሱም : ጋራ : እንደ : እግዚአብሔር : ትእዛዝ : በቅድስት : መጋባት : ባንድ : ልትኖሪ : ትሻለሽን :: እርሱን : ትሰሚያለሽን :: ትገዢለትማለሽን :: ትወጂውማለሽን :: ታከብርየውማለሽን :: በሕማምና : በጤናም : ትረጂዋለሽን :: ሌላውንም : ሁሉን : ትተሽ : እርሱን : ብቻ : ትከተያለሽን : በሁለታችሁ : ዕድሜ : ሁሉ ::



ሴት : ደገማ : ትመልስ ::

አወን : ይህ : ፈቃዴ : ነው ::

ከዚያ : ወዲያም : ቄስ : እንዲህ : ሲል : ይጠይቅ ::

ይህችን : ሴት : ማን : ይሰጣል : ለዚህ : ወንድ : ለመጋባት ::

የዚያን : ጊዜ : መሐላቸውን : እንዲህ : ያድርጉ :: የሴት : አባት : ወይስ : ወዳጅ : እርስዋን : ወደ : ቄስ : ይወስዷል :: ቄስም : ወንድን : የሴትን : ቀኝ : እጅዋን : በቀኝ : እጁ : ይዝ : ዘንድ : ያዛል :: ወንድም : ቄስን : በመንገሩ : እንዲህ : ብሎ : ይከተል ::

እኔ : ——— : አንችን : ——— : ለምሽቴ : እወስድሻለሁ :: አንች : ከዚህ : ቀን : ጀምረሽ : ለኔ : ልትሆኚ : ልትኖሪም : በበጎ : ቀንና : በክፉ :: በባለጠግነትና : በድኻነትም :: በሕማምና : በጤናም : እወድሽ : ዘንድ : እረዳሽም : ዘንድ : ሞት : እስኪለይን : ድረስ :: እንደ : እግዚአብሔር : እንደ : ቅዱስ : ሥርዓቱ :: ለዚህም : ነገር : እምነቴን : እሰጥሻለሁ ::

የዚያን : ጊዜም : እጆቻቸውን : ይፈቱ :: ሴትም : በቀኝ : እጅዋ : የወንድ : ቀኝ : እጅን : ትውሰድ :: እርስዋም : ደግማ : ቄስን : በመንገሩ : ትከተል : እንዲህ : ስትል ::

እኔ : ——— አንተን : ——— ለባሌ : እወስድሃለሁ :: አንተ : ከዚህ : ቀን : ጀምረህ : ለኔ : ትሆን : ዘንድ : ከኔ : ጋራም : ትኖር : ዘንድ : በበጎ : ቀንና : በክፉ :: በባለጠግነትና : በድኻነትም :: በሕማምና : በጤናም : እወድህ : ዘንድ : እረዳህም : ዘንድ : እገዛለህም : ዘንድ :: ሞት : እስኪለይን : ድረስ :: እንደ : እግዚአብሔር : እንደ : ቅዱስ : ሥርዓቱ :: ለዚህም : እምነቴን : እሰጥሃለሁ ::

ከዚህም : በኋላ : ደግሞ : እጆቻቸውን : ይፈቱ ::
ሙሽሪውም : ለሙሽሪይቱ : ቀለበትን : ይስ
ጥ :: ይህነንም : በመጽሐፍ : ላይ : ያኑረው :: ቄ
ስም : ይውሰደው :: ለወንድም : ይስጠው :: እር
ሱም : ወደ : ሙሽሪይቱ : ግራ : ወደ : አራተኛ : ጻ
ትዋ : ያኑረው :: የዚያን : ጊዜም : ቀለበትን : በ
ጻትዋ : ይያዝ : ቄስንም : በመንገር : ይከተል : እ
ንደዚህ : ሲል ::

በዚህ : ቀለበት : አጨሻለሁ :: በሥጋዬም : አከብርሻለ
ሁ :: ግንዘቤንም : ሁሉን : ካንች : ጋራ : እከፈፍላለሁ : በ
አብና : በወልድ : በመንፈስ : ቅዱስም : ስም :: አሜን ::

---

ከዚያ : ወዲያም : ወንድ : ቀለበትን : በሙሽሪ
ይቱ : ግራ : እጅ : ባራተኛው : ጻትዋ : ትቶ : እር
ሳቸው : ሁለታቸው : በጉልበታቸው : ይምበርከ
ኩ :: ቄስም : ፊቱን : ወደርሳቸው : መልሶ :: በእ
ግዚአብሔርም : ሳድቃ : ፊት : ቁሞ : እንደዚህ :
ይበል ::

እንጸልይ ::

የዘላለም : አምላክ : ሆይ :: የሰዎች : ሁሉ : ፈጣሪና :
ጠባቂ :: የመንፈሳዊ : ስጥወታም : ሁሉ : ሰጭ :: የዘላለ
ም : ሕይወት : ምንጭ :: ለለዚህ : ሁለት : ባሮችህ : ለዚህ :
ወንድና : ለዚች : ሴት : በስምህ : ለምንባረካቸው : በረከ
ትህን : አውርድላቸው :: ይስሐቅና : ርብቃ : ታምነው : ባን
ድ : ይቀመጡ : እንደ : ነበረ :: እንደዚህ : ደግሞ : እለዚህ : ሁ
ለት : ያደረጉትን : ስለታቸውንና : መሓላቸውን : ይህ : ቀለ
በት : ምልክትና : መያዣ : የሆነላቸው : በውነት : ሊፈጸሙ
ት : ሊያደርጉትም :: ጸጋ : ስጣቸው : ሁለግዜ : በፍጹም :
ፍቀርና : በሰላም : ባንድ : ይኖሩ : ዘንድ : እንደ : ሕግህም :
ይሔዱ : ዘንድ :: በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ :: አሜን ::

ከዚህም : በኋላ : ቄስ : ቀኝ : እጆቻቸውን : ያስማ
ማቸው : እንደዚህ : ሲል ::



እግዚአብሔር : አንድ : ያደረገውን : ሰው : አይለየው ::

---

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ከዚያ : ያሉትን : ሰዎች :
እንደዚህ : ይንገራቸው ::

————ና : ————: ለቅድስት : መጋባት : ባንድ : አገና
ኙተናቸዋልና :: ይህነንም : በእግዚአብሔርና : በዚህች : ጉባ
ዔ : ፊት : መሰከሩ :: ከዚያ : ወዲያም : እርሱ : በርሳቸው :
ቃላቸውን : እንደ : መያዣ : ሰጥተዋልና :: ይህነንም : በግል
ጽ : ቀለበትን : በመስጠትና : በመቀበል : ገልጸውታልና ::
እርሳቸው : እርሱ : በርሳቸው : ባልና : ምሽት : እንደሉ :
እላለሁ :: በአብና : በወልድ : በመንፈስ : ቅዱስም : ስ
ም :: አሜን ::

ከዚህም : በኋላ : ቄስ : ይህነን : በረከት : ይጨምር ::

እግዚአብሔር : አብ :: እግዚአብሔር : ወልድም :: እግ
ዚአብሔር : መንፈስ : ቅዱስም : ይባርካችሁ :: ያጽናችሁ
ም :: እግዚአብሔርም : በጸጋው : ወደላንት : ተመልክቶ :
በመንፈሳዊ : በረከትና : ጸጋ : ሁሉ : ይምላችሁ :: በምድ
ር : ያለውን : ሕይውታችሁን : ባንድ : እንደዚህ : ታድርጉ : ዘ
ንድ : በሚመጣ : ዓለም : የዘላለሙን : ሕይወት : እንድት
ቀበሉ :: አሜን ::

---

ከዚያ : ወዲያም : ቄስ : ይህነን : መዝሙር : ፻፳፯
ያንብብ ::

ምስጉን : ነው : እግዚአብሔርን : የሚፈራ : ሁሉ : በመን
ገዱም : የሚሔድ ::

የጅህን : ድካም : ትበላለህ :: ምስጉን : ነህ : ደህንነት
ም : ትሆንልሃለች ::

ምሽትህ : እንደ : ፍርያም : ወይን : በቤትህ : አጸገብ ::

ልጆችህም : እንደ : ወይራ : አታክልት : በማዕድህ : ዙርያ ::

እነሆ : እንደሁ : እግዚአብሔርን : የሚፈራ : ሰው : ደባ
ረካል ::

እግዚአብሔር : ይባርክሃል : ከፅዮን :: የየሩሳሌምንም :

በጕነት ፡ ታያለህ ፡ የሕይወትህን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ።

የልጆችህንም ፡ ልጆች ፡ ታያለህ ። ደኅንነት ፡ በእሥራኤል ፡ ላይ ፡ ይሁን ።

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ።

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ። ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

ወይስ ፡ መዝሙር ፡ ፳፯ ።

እግዚአብሔር ፡ ይማረን ፡ ይባርክነም ። ፊቱንም ፡ ያበራልና ።

በምድር ፡ መንገድህ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ። በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ መኻከል ፡ ማደንህ ።

አሕዛብ ፡ ይገዙልህ ፡ አቤቱ ። ይገዙልህ ፡ አሕዛብ ፡ ሁላቸው ።

አሕዛብ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትም ፡ ያድርጉ ። ባሕዛብ ፡ በቅን ፡ ትፈርደለህና ። አሕዛብንም ፡ በምድር ፡ ትመራለህና ።

አሕዛብ ፡ ይገዙልህ ፡ አቤቱ ። ይገዙልህ ፡ አሕዛብ ፡ ሁላቸው ።

ምድርም ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ። እግዚአብሔር ፡ አምላካችንም ፡ ይባርክናል ።

ይባርክናል ፡ እግዚአብሔር ፡ የምድርም ፡ ደርቻ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩታል ።

---

መስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ።

በመጀመርያው ፡ እንደ ፡ ነበረ ። አሁንም ፡ እንዲሆን ። ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

---

ደህም ፡ ተጨርሶ ፡ ወንድና ፡ ሴትም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሳድቃ ፡ በፊቱ ፡ ተንበርክከው ፡ ቄስም ፡ በርሶ ፡ ቁሞ ፡ ፊቱንም ፡ ወደርሳቸው ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።



አቤቱ ፡ ማረን ።

ምላሽ ። ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረን ።

ቄስ ። አቤቱ ፡ ማረን ።

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ። ስምህ ፡ ይቀደስ ፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ። ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ። እንጀራችንን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ። ደቅር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ። እኛም ፡ ደገመን ፡ ደቅር ፡ እንደምንል ፡ ለኛ ፡ ያለባቸውን ። ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባነ ፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ። አሜን ።

---

ቄስ ። አቤቱ ፡ ባርያህንና ፡ ባርያዪትህን ፡ እርዳ ።

ምላሽ ። ባንተ ፡ አምነዋልና ።

ቄ ። አቤቱ ፡ ረዲትን ፡ ስደድላቸው ፡ ከቅዱስ ፡ ማደርያህ ፡ ዘንድ ።

ም ። ሁለግዜም ፡ ጠብቃቸው ።

ቄ ። ብርቱ ፡ አምባ ፡ ሁንላቸው ።

ም ። ከጸላቶቻቸው ፡ ፊት ።

ቄስ ። አቤቱ ፡ ጸሎታችነን ፡ ስማ ።

ምላሽ ። ጩኸታችንም ፡ ወደንተ ፡ ይድረስ ።

ቄስ ።

አቤቱ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ። የይስሐቅም ፡ አምላክ ። የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ። ይህነን ፡ ባርያህና ፡ ይህችን ፡ ባርያዪትህ ፡ ባርክ ። የዘላለምንም ፡ ሕይወት ፡ ዘር ፡ ወደ ፡ ልባቸው ፡ ዝራ ። ከቃልህም ፡ ስለ ፡ መደናቸው ፡ የሚማሩትን ፡ በውነት ፡ ይፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡ ስጣቸው ። አቤቱ ፡ በጸጋ ፡ ወደርሳቸው ፡ ከሰማይ ፡ ተመልከት ። ላብርሃምና ፡ ለሳራ ፡ በረከትህን ፡ እንደ ፡ ሰደድህላቸው ፡ እንዲህ ፡ ደግሞ ፡ እርሳቸውንም ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ውደድ ፡ እርሳቸው ፡ ለፈቃድህ ፡ ሁለግዜ ፡ ተገዝተው ፡ በመጠበቅህም ፡ ዐርፈው ፡ በውድህ ፡ ደኖሩ ፡ ዘንደ ፡ እስከ ፡ ሞታቸው ፡ ድረስ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

የሴት ፡ የመውለድዋ ፡ ዘመን ፡ ያለፈባት ፡ እንደ
ሆን ፡ ከዚህ ፡ የሚከተለውን ፡ ልመና ፡ አያድርጉ ፡
የምሕረት ፡ አምላክ ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ በበረከትህ ፡ ይበዛሉና ፡፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ እሌህ ፡ ሁለቱን ፡ በበረከትህ ፡ እርዳቸው ፡ የሚያፈሩ ፡ ሊሆኑ ፡ ሊበዙም ፡፡ በውነተኛም ፡ ፍቅርና ፡ በጽድቅ ፡ ባንድ ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ የልጆቻቸውን ፡ ማደግያ ፡ እንደ ፡ ክርስቲያናት ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እስኪያዩ ፡ ድረስ ፡ ላንተ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

አቤቱ ፡ አንዳች ፡ ሳይሆን ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በችሎትህ ፡ ፈጥረሃልና ፡፡ አንተ ፡ ለቀረውም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሥርዓትን ፡ ከሠራህ ፡ በኋላ ፡ ወንድን ፡ በፊት ፡ እንደ ፡ መልክህ ፡ ፈጠርህው ፡ ከርሱም ፡ ዘንድ ፡ ሴትን ፡ ፈጠርሃት ፡፡ ሁለታቸውንም ፡ አንድ ፡ አደረግሃቸው ፡፡ በዚህም ፡ ከቶ ፡ እንደይገባ ፡ አንተ ፡ በመጋባት ፡ አንድ ፡ ያደረግሃቸውን ፡ እንለይ ፡ ዘንድ ፡ አስተማርህን ፡፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ የመጋባትን ፡ ንብረት ፡ እንዴህ ፡ ላለው ፡ ለተመሰገነ ፡ ምሥጢር ፡ ቀደስህው ፡ ያነን ፡ መንፈሳዊ ፡ መጋባትን ፡ በክርስቶስና ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ መኻከል ፡ ያለውን ፡ አንድነት ፡ እንዲያመለክተው ፡ እንዲመስለውም ፡፡ በጸጋ ፡ ተመልከት ፡ ወደለዚህ ፡ ባሮችህ ፡፡ ይህ ፡ ወንድ ፡ ቃልህ ፡ እንደ ፡ አዘዘ ፡ ምሽቱን ፡ ይወድ ፡ ዘንድ ፡ ክርስቶስም ፡ ሙሽራዪቱን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑን ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡፡ ራሱን ፡ ስለርስዋ ፡ ለውጦታልና ፡ እንደ ፡ ሥጋውም ፡ በፍቅር ፡ ይጠብቃታል ፡፡ ይህችም ፡ ሴት ፡ የምትወድ ፡ የተወደደችም ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ አድርግ ፡ ለባልዋም ፡ የታመነች ፡ የተገዛችም ፡፡ በረፍትም ፡ በጭምትም ፡ በሰላምም ፡ ሁሉ ፡ እለዚያን ፡ ቅዱሳት ፡ ሴቶች ፡ ልትከተል ፡ ምሳልያቸው ፡ በቃልህ ፡ ያበራላትን ፡፡ አወን ፡ አቤቱ ፡ ሁለታቸውን ፡ ባርካቸው ፡ ጸጋም ፡ ስጣቸው ፡ የዘላለምን ፡ መንግሥትህ ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

---



ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ቄስ ፡ ይበል ፡፡

ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአብሔር ፡ በመጀመርያ ፡ ፈተኞችን ፡ ወላጆቻችን ፡ አደምና ፡ ሔዋን ፡ የፈጠራቸው ፡ የቀደሳቸውም ፡፡ በመጋባት ፡ ያሰማማቸውም ፡፡ የጸጋውን ፡ ባለጠግነት ፡ በላንት ፡ ላይ ፡ ይስጣችሁ ፡፡ ይቀድሳችሁም ፡ ይባርካችሁም ፡፡ እላንት ፡ በመንፈስና ፡ በሥጋ ፡ ደስ ፡ ታሰኙት ፡ ዘንድ ፡፡ በተቀደሰም ፡ ፍቅር ፡ ባንድ ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ እስከ ፡ ዘመናችሁ ፡ መጨርሻ ፡ ድረስ ፡፡ አሜን ፡፡

---

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ለባልና ፡ ለምሽቱ ፡ እርሱ ፡ በር
ሳቸው ፡ የሚገባቸውን ፡ ነገር ፡ የምታስተምር ፡ስ
ብከት ፡ ባትሆን ፡ ቄስ ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ያንብብ ፡፡

እላንት ፡ ያጋባችሁ ፡ ሁሉ ፡፡ ወደስ ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ መጋባት ፡ ንብረት ፡ ልትግቡ ፡ የምታስቡ ፡፡ መጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ ወንዶች ፡ ለምሽቶቻቸው ፡ ሴቶችም ፡ ለባሎቻቸው ፡ ስለ ፡ ሚገባ ፡ ነገር ፡ የሚለውን ፡ ስሙ ፡፡

ጳውሎስ ፡ ለባሎች ፡ ሁሉ ፡ ይህነን ፡ ትእዛዝ ፡ ይሰጣቸዋል ፡፡

ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ሰዎች ፡ በመልእክቱ ፡ ምዕራፍ ፡ ፭። ቍጥር ፡ ፳፪። ፴፫።

እላንት ፡ ወንዶች ፡ ምሽቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፡ ክርስቶስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኒቱን ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡፡ ስለርስዋም ፡ ራሱን ፡ እንደ ፡ ለወጠ ፡፡ በውኃ ፡ ማፀብያ ፡ በቃሉም ፡ ያነጻት ፡ ዘንድ ፡ ይቀድሳትም ፡ ዘንድ ፡፡ እርስዋን ፡ ለማቆም ፡ ለርሱ ፡ የተመሰገነች ፡ አድርጎ ፡ እድፈ ፡ ርኵሰትም ፡ እንዴህ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ የሚመስል ፡ የሌለባት ፡፡ ንጽሕት ፡ እንድትሆን ፡ እንጅ ፡ ያለ ፡ ነውርም ፡፡ እንዲሁም ፡ ይገባል ፡ ለወንዶች ፡ ሴቶቻቸውን ፡ እንደ ፡ ሥጋቸው ፡ ይወዱ ፡ ዘንድ ፡፡ ምሽቱን ፡ የሚወድ ፡ ራሱን ፡ ይወዳልና ፡፡ ማንም ፡ ሥጋውን ፡ የሚጠላ ፡ ከቶ ፡ የለምና ፡፡ ይመግባዋል ፡ እንጅ ፡ ያቅፈዋልም ፡፡ ክርስቶስም ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያኒቱ ፡ እንደደረገ ፡፡ እኛ ፡ የሥጋው ፡ ብልቶች ፡ ነንና ፡ ከሥጋው ፡ ካጽንቱም ፡፡

ስለዚህም ፡ ሰው ፡ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ይተዋል ፡ ለምሽቱም ፡ ይጣበቃል ፡፡ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ይሆናሉ ፡፡ ይህም ፡ ምሥጢር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ክርስቶስና ፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተናግሬያለሁ ፡፡ ይህም ፡ ሳይቀር ፡ ከላንትም ፡ ኢያንደንዳችሁ ፡ ምሽቱን ፡ ይውደድ ፡ እንደ ፡ ራሱ ፡፡

እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ በመልእክቱ ፡ ወደ ፡ ቆሎሳውያን ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡፡ ምዕራፍ ፡ ፫፡፡ ቍጥር ፡ ፲፱፡፡

እላንት ፡ ወንዶች ፡ ሴቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፡ የመረራችሁባቸውም ፡ አትሁኑ ፡፡

ቅዱስ ፡ ጴጥሮስም ፡ የክርስቶስ ፡ ሐዋርያ ፡ እርሱ ፡ ተጋብቶ ፡ የነበረ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡፡ ፩፤ መልእክቱ ፡፡ ምዕራፍ ፡ ፫፡፡ ቍ ፡ ፯፡፡

እላንት ፡ ወንዶች ፡ እንዲሁ ፡ በውቀት ፡ ተቀመጡ ፡ ከምሽቶቻችሁ ፡ ጋራ ፡፡ አውቃችሁ ፡ የሴቶች ፡ ፍጥረት ፡ ደካማ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አክብርዋቸው ፡፡ ከላንትም ፡ ጋራ ፡ የሕይወት ፡ ጸጋ ፡ ይወርሳሉና ፡፡ በነገሩ ፡ ሁሉ ፡ ጸሎታችሁን ፡ እንዳትቈርጡ ፡፡

እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ለወንድ ፡ ወደ ፡ ምሽቱ ፡ የሚገባውን ፡ ሰማችሁ ፡፡ አሁንም ፡ እላንት ፡ ሴቶች ፡ ወደ ፡ ባሎቻችሁ ፡ የሚገባችሁትን ፡ ስሙ ፡፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ እንዲል ፡፡

ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ ይላል ፡፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ም ፡ ፭፤ ፳፪፡፡

እላንት ፡ ሴቶች ፡ ለባሎቻችሁ ፡ ተገዙ ፡ ለጌታ ፡ እንደምትገዙ ፡፡ ወንድ ፡ የሴት ፡ ራስ ፡ ነውና ፡፡ ክርስቶስ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ራስ ፡ እንደሆነ ፡፡ እርሱም ፡ ሥጋውን ፡ የሚያድን ፡ ነው ፡፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ለክርስቶስ ፡ እንድትገዛ ፡፡ እንዲሁም ፡ ሴቶች ፡ ይገዙ ፡ ለባሎቻቸው ፡ በሁሉ ፡፡

ቍ ፡ ፴፫፡፡ ምሽቱም ፡ ባልዋን ፡ የምትፈራ ፡ ትሁን ፡፡

እርሱም ፡ ደግሞ ፡ በመልእክቱ ፡ ወደ ፡ ቆሎሳይስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡፡ ም ፡ ፫፡፡ ቍ ፡ ፲፰፡፡

እላንት ፡ ሴቶች ፡ ለባሎቻችሁ ፡ ተገዙ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ገባ ፡፡

ቅዱስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ይህነን ፡ መልካም ፡ ትእዛዝ ፡ ይሰጣቿል ፡፡ ፩፡፡ መልእክቱ ፡ ም ፡ ፫፡፡ ቍ ፡ ፩፤ እስከ ፡ ፯፡፡ ድረስ ፡፡



እላንት ፡ ሴቶች ፡ ለባሎቻችሁ ፡ ተገዙ ፡፡ ከርሳቸው ፡ ሰዎች ፡ ቢኖሩ ፡ ለነገር ፡ የማይገዙ ፡ ደረቡ ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በሴቶቻቸው ፡ አካሔድ ፡፡ የንጻችውን ፡ አካሔዳችሁን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ በፍርሃት ፡፡ እሊያ ፡ ጌጻቸው ፡ ከአፍአ ፡ ያደደለ ፡ የራስ ፡ ጸጕር ፡ በመሰራት ፡ በወርቅም ፡ ዝርግፍ ፡፡ በጌጸም ፡ ልብስ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ በማጠፊ ፡ በተሰወረች ፡ በልብ ፡ ሰውነት ፡፡ በየዋህም ፡ ነፍስ ፡ ጸጥ ፡ ባለ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ገናንነቱ ፡ የከበረ ፡፡ ቀድሞ ፡ እንዲህ ፡ ነበሩና ፡ ደግሞ ፡ የተቀደሱት ፡ በእግዚአብሔርም ፡ የታመኑ ፡ ሴቶች ፡፡ ነፍሳቸውን ፡ ያስጌጹ ፡ ለባሎቻቸውም ፡ የተገዙ ፡፡ ለአብርሃም ፡ እንደ ፡ ተገዛች ፡ እንደ ፡ ሳራ ፡ ጌታዬም ፡ ትለው ፡ ነበረች ፡፡ እላንት ፡ ልጆችዋ ፡ የሆናችሁ ፡ መልካም ፡ ስታደርጉ ፡፡ ከፍርሃትም ፡ ሁሉ ፡ አንዳች ፡ ሳትፈሩ ፡፡

---

የተጋቡ ፡ ሰዎች ፡ በመጋባት ፡ ቀን ፡ ወይስ ፡ በሚከተለው ፡ በመጀመርያ ፡ ቍርባን ፡ ጊዜ ፡ ቢቈረቡ ፡ መልካም ፡ የሚገባም ፡ ነው ፡፡

---

## የገንዘት ፡ ሥርዓት ፡፡

ያለ ፡ ጥምቀት ፡ ወይስ ፡ ተገዝተው ፡ ወይስ ፡ ነፍሳቸውን ፡ ገድለው ፡ ለሞቱ ፡ ይህች ፡ ሥርዓት ፡ አትገለገልላቸው ፡፡

ሬሳው ፡ ወደ ፡ መቃበር ፡ ስፍራ ፡ ሲደርስ ፡ ቄስና ፡ የጉባኤ ፡ አገልጋዮች ፡ በመግቢያው ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይገናኑ ፡ በፊቱም ፡ ቀድመው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ወይስ ፡ ወደ ፡ መቃበር ፡ ሒደው ፡ ይናገሩ ፡ ወይስ ፡ ያዝመሩ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡፡

እኔ ፡ ትንሣኤና ፡ ሕይወት ፡ ነኝ ፡ ይላል ፡ ጌታችን ፡፡ ያመነብኝ ፡ ቢሞት ፡ እንኳ ፡ ሕያው ፡ ይኖራል ፡፡ ሕያውም ፡ ሁኖ ፡ የሚያምንብኝ ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ አይሞትም ፡፡ ዮሐንስ ፡ ፲፩፤ ፳፭፤ ፳፮፤

የሚያድነኝ ፡ ሕያው ፡ እንደ ሆነ ፡ አውቃለሁ ፡ እርሱም ፡ ኋለኛ ፡ ሁኖ ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ይቆማል ፡፡ በኋላም ፡ ትል ፡ እንኳ ፡ ይህችን ፡ ቍርበቴን ፡ ሲፈጅ ፡ በሥጋዬ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አያለሁ ፡፡ እርሱንም ፡ እኔ ፡ ለኔ ፡ አየዋለሁ ፡ ዓይኖቼም ፡ ይመለከቱታል ፡ እንግዳም ፡ አይደለም ፡፡ ኢዮብ ፡ ፲፱፡ ፳፭፡ ፳፯፡፡

እንደችን ፡ ይዘን ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ አልገባነም ፡ እንደችንም ፡ ይዘን ፡ ከርሱ ፡ መውጣት ፡ እንደይሆንለን ፡ አይጠረጠርም ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ሰጠ ፡፡ እግዚአብሔርም ፡ ወሰደ ፡፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡፡ ፩፡ ጢሞቴዎስ ፡ ፮፡ ፯፡፡ ኢዮብ ፡ ፩፡ ፳፩፡፡

ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ከገቡ ፡ በኋላ ፡ ከዚህ ፡ ከሚከተሉ ፡ መዝሙራት ፡ አንድ ፡ ወይስ ፡ ሁለ ታቸው ፡ ይነበቡ ፡፡

መዝሙር ፡ ፴፱፡

በመላሴ ፡ እንዳልስት ፡ መንገዴን ፡ እጠብቃለሁ ፡ አለሁ ፡፡ አፌን ፡ በልጓም ፡ እጠብቃለሁ ፡ ኃጢአተኛ ፡ በፊቴ ፡ ሳለ ፡፡

ዝም ፡ አልሁ ፡ ለበጎም ፡ እንኳ ፡ ዝም ፡ አልሁ ፡፡ ሕማሜም ፡ ታደሰብኝ ፡፡

ልቤ ፡ በውሥጤ ፡ ሞቀብኝ ፡፡ ከማሰቤ ፡ የተነሣ ፡ እሳት ፡ ነደደብኝ ፡ በመላሴም ፡ ተናገርሁ ፡፡

አቤቱ ፡ ጫሬሼን ፡ አስታውቀኝ ፡ የዘመኔም ፡ ቍጥር ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ነው ፡፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደካማ ፡ የሆንሁ ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡፡

እነሆ ፡ ዘመኖቼን ፡ እንደ ፡ ስንዝር ፡ ርዝመት ፡ አደረግኋቸው ፡፡ አካሌም ፡ በፊትኽ ፡ እንደችን ፡ አይመስልም ፡፡ በውነት ፡ የሰው ፡ መኖር ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡፡

በውነት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በጽላ ፡ ይመላለሳል ፡፡ በውነት ፡ በከንቱ ፡ ይታወካሉ ፡፡ ያከማቻል ፡ የሚሰበስበውም ፡ ምን ፡ ይሆናል ፡ አያውቅም ፡፡



አሁንስ ፡ ተስፋዬ ፡ አቤቱ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡፡ ተስፋዬን ፡ አንተን ፡ አደረግሁ ፡፡

ከኃጢአቴ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝ ፡፡ የሰነፎችን ፡ ስድብ ፡ አታድርገኝ ፡፡

ዝም ፡ አልሁ ፡ አፌንም ፡ አልከፈትም ፡ አንተ ፡ አድርገኸዋልና ፡፡

መቅሠፍትኽን ፡ ከኔ ፡ አርቅ ፡፡ ከእጅኽ ፡ አመታት ፡ የተነሣ ፡ እኔ ፡ አልቅያለሁና ፡፡

በተግሣፅኽ ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ሰውን ፡ ዘለፍኸው ፡ መልካምነቱም ፡ እንደ ፡ ትንኝ ፡ ትፈጀለች ፡፡ በውነት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡፡

ጸሎቴን ፡ ስማ ፡ አቤቱ ፡ ጬኸቴንም ፡ አድምፅ ፡፡ ለልቅሶዬም ፡ ዝም ፡ አትበል ፡፡ እኔ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ መጻተኛ ፡ ነኝና ፡ እንደባቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ተቀምጬለሁና ፡፡

ተወኝ ፡ አርፍ ፡ ዘንድ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወደማልመለስበት ፡ ስፍራ ፡ ሳልሔድ ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ፡፡ ለዘወተርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

መዝሙር ፡ ፺፡

አቤቱ ፡ አንተ ፡ መኖርያ ፡ ሆንኽልነ ፡ በትውልድ ፡ ሁሉ ፡፡

ተራሮች ፡ ሳይወለዱ ፡ ምድርም ፡ ዓለምም ፡ ሳይፈጠር ፡፡ ከዘላለምም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ አንተ ፡ አምላክ ፡ ነኽ ፡፡

ሰውን ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ትመልሳለኽ ፡ ተመለሱም ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ትላለኽ ፡፡

ሺኽ ፡ አመት ፡ በፊትኽ ፡ እንደለፈች ፡ እንደ ፡ ትላንት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሌትም ፡ ትጋት ፡ ናትና ፡፡

አጠፋኻቸው ፡ እንደ ፡ እንቅልፍም ፡ ናቸው ፡፡ ማልደ ፡ እንደ ፡ ለመለመ ፡ እንደሚያልፍም ፡ እሳር ፡፡

ማልደ ፡ ያብባል ፡ ያልፋልም ፡፡ በሰርክም ፡ ይቈረጣልና ፡ ይደርቃል ፡፡

በቍጣኽ ፡ አልቀናልና ፡፡ በመዓትኽም ፡ ደነገፅን ፡፡

ኃጢአታችንን ፡ በፊትኽ ፡ አስቀመጥኽ ፡፡ የተሰወረም ፡ ኃጢአታችን ፡ በፊትኽ ፡ ብርሃን ፡፡

ዘመናችን ፡ ሁሉ ፡ በመዓትኽ ፡ አልፎዋልና ፡፡ አመታታችንም ፡ እንደ ፡ ጨወታ ፡ ፈጸምን ፡፡

ያመታታችን ፡ ዘመን ፡ ሰብዓ ፡ አመት ፡ ነው ፡፡ በብርታትም ፡ ቢሆን ፡ ስማንያ ፡ አመት ፡፡ ኃይላቸው ፡ ግን ፡ ድካምና ፡ መከራ ፡ ነው ፡፡ ቶሎ ፡ አልፎዋልና ፡ እኛም ፡ በረን ፡ እንሔደለን ፡፡

ማነው ፡ የቍጣኽን ፡ ጽናት ፡ የሚያውቅ ፡፡ እንደ ፡ ፍርሃትኽም ፡ እንደሁም ፡ ቍጣኽ ፡ እንደለ ፡፡

ዘመናችንን ፡ እንቈጥር ፡ ዘንድ ፡ አስታውቀን ፡፡ ልባችንን ፡ ወደ ፡ ጥበብ ፡ እንድናገባ ፡፡

ተመለስ ፡ አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡፡ ለባሮችኽም ፡ እዘን ፡፡

ማልደ ፡ ምሕረትኽን ፡ አጽግበን ፡፡ ደስም ፡ ይለናል ፡ ሐሤትም ፡ እናደርጋለን ፡ በዘመናችን ፡ ሁሉ ፡፡

ደስ ፡ አሰኘን ፡ መከራ ፡ በተቀበልንባት ፡ ቀን ፡ ፈንታ ፡፡ ክፉም ፡ ባየነበት ፡ ዘመን ፡ ፈንታ ፡፡

ባሮችኽ ፡ ስራኽን ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቻቸውም ፡ ምስጋናኽን ፡፡

የአምላካችንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሞገስ ፡ በላያችን ፡ ይሁን ፡፡ የጆቻችንንም ፡ ስራ ፡ በላያችን ፡ አቅና ፡ የጆቻችንን ፡ ስራ ፡ አቅና ፡፡

ምስጋና ፡ ይሁን ፡ ለአብ ፡ ለወልድም ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡፡

በመጀመርያ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡፡ አሁንም ፡ እንዲሆን ፡፡ ለዘወትርም ፡ እንደለው ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡



ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ይህች ፡ ንባቤ ፡ ትከተል ፡፡

፩፤ ቆሮንቶስ ፡ ፲፭፤ ፳፤ — ፶፰፡፡

አሁን ፡ ግን ፡ ክርስቶስ ፡ ከሙታን ፡ ተነሣ ፡፡ ላንቀላፉትም ፡ መጀመርያ ፡ ሆነ ፡፡ ሞትም ፡ በሰው ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡፡ እንደሁም ፡ በሰው ፡ የሙታን ፡ ትንሣኤ ፡ ሆነች ፡፡ ሁሉ ፡ በአደም ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ እንደሁም ፡ በክርስቶስ ፡ ሁሉ ፡ ሕያዋን ፡ ይሆናሉና ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ኢያንዳንዱ ፡ በየሥርዓቱ ፡፡ ክርስቶስ ፡ አስቀድሞ ፡ ነው ፡፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የክርስቶስ ፡ ወገኖች ፡ ያሉ ፡ በመምጣቱ ፡ ጊዜ ፡፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ፍጻሜ ፡ ይሆናል ፡፡ መንግሥቱን ፡ ለእግዚአብሔርና ፡ ለአብ ፡ አሳልፎ ፡ ሲሰጥ ፡ ጊዜ ፡፡ አለቅነትን ፡ ሁሉ ፡ ሥልጣንንም ፡ ሁሉ ፡ ኃይልንም ፡ ሁሉ ፡ ሲሽር ፡ ጊዜ ፡፡ ይነግሥ ፡ ዘንድ ፡ አለውና ፡ ጸላቶቹን ፡ ሁሉ ፡ ከግሩ ፡ በታች ፡ እስኪጥል ፡ ድረስ ፡፡ ከሁሉም ፡ በኋላ ፡ የሚሻር ፡ ጸላት ፡ እርሱ ፡ ሞት ፡ ነው ፡፡ ሁሉን ፡ ከግሩ ፡ በታች ፡ አስገዝቶለታልና ፡፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ተገዛለት ፡ ሲል ፡፡ የታወቀ ፡ ነው ፡ ሁሉን ፡ ለርሱ ፡ ካስገዛለት ፡ በቀር ፡ እንደለ ፡፡ ሁሉም ፡ በተገዛለት ፡ ጊዜ ፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ልጅ ፡ ይገዛል ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ሁሉን ፡ ላስገዛለት ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁሉ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በሁሉም ፡፡ እንኪያ ፡ ምን ፡ ያደርጋሉ ፡ ስለ ፡ ሙታን ፡ የሚጠመቁ ፡፡ ሙታን ፡ ባይነሡ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ፡ መጠመቃቸው ፡ ስለ ፡ ሙታን ፡፡ ለምንስ ፡ ሁልጊዜ ፡ መከራ ፡ እንቀበላለን ፡፡ ለኔ ፡ በሆነው ፡ ትምክሕት ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እምልላችኋለሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እንድሞት ፡፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ካራዊት ፡ ጋራ ፡ በኤፌሶን ፡ ከታገልሁ ፡፡ በዚያ ፡ ምን ፡ እጠቀማለሁ ፡ ሙታን ፡ ባይነሡ ፡፡ እንብላና ፡ እንጠጣ ፡ ነገ ፡ እንሞታለንና ፡፡ አትሳቱ ፡፡ ክፉ ፡ ጨወታ ፡ መልካሙን ፡ አካሔድ ፡ ያጠፋልና ፡፡ ልባችሁን ፡ ለጽድቅ ፡ አስነሡ ፡ ኃጢአትንም ፡ አታድርጉ ፡፡ አያሌ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የማያውቁ ፡ አሉና ፡፡ ይህነንም ፡ ማለቴ ፡ ሳሳፍራችሁ ፡ ነኝ ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከላንት ፡ ሰው ፡ ይላል ፡፡ ሙታን ፡

እንዴት : ይነሣሉ : በምንስ : ሥጋ : ይመጣሉ ። አንተ : ሰነፍ ። አንት : የምትዘራው : ሕያው : አይሆንም : ካልሞተ ። ያም : የምትዘራው : ዘር : የሚሆነው : ሥጋ : አይደለም ። ነገር : ግን : ቅንጣት : ብቻ : ነው ። የስንዴ : ወይም : የገብስ : ወይም : የማናቸውም : ዘር : ቢሆን ። እግዚአብሔር : ግን : ገላውን : ያደርግለታል : እንደ : ወደደ ። ለሁሉም : ኢያንደንዱ : ገላውን : ይሰጠዋል ። ሥጋም : ሁሉ : አንድ : አይደለም ። የሰው : ሥጋ : ሌላ : ነውና ። የከብትም : ሥጋ : ሌላ : ነውና ። ያሣም : ሥጋ : ሌላ : ነው : የዎፎም : ሥጋ : ልዩ : ነው ። የሰማይም : ወገን : ሥጋ : አለ ። የምድርም : ወገን : ሥጋ ። ነገር : ግን : የሰማይ : ወገን : ክብሬቸው : ሌላ : ነው ። የምድርም : ወገን : ክብር : ሌላ ። የጸሓይ : ክብር : ሌላ : ነው ። የጨረቃም : ክብር : ሌላ ። የከዋክብትም : ክብር : ሌላ : ነው ። ኮከብም : ከኮከብ : በክብር : ይለያል ። እንዲሁም : የሙታን : ትንሣኤ : ናት ። በጥፋት : ይዘራል ። ባለ : ጥፋትም : ይነሣል ። በነውር : ይዘራል ። በክብርም : ይነሣል ። በድካምም : ይዘራል ። በኀይልም : ይነሣል ። ነፍሳዊ : ሥጋ : ይዘራል ። መንፈሳዊ : ሥጋም : ይነሣል ። ነፍሳዊ : ሥጋ : አለ : መንፈሳዊም : ሥጋ : አለ ። እንዲሁም : ደግሞ : ተጽፍዋል ። አደም : የፊተኛው : ሰው : ለሕያው : ነፍስ : ሆነ ። ሁለተኛው : አደም : ሕይወት : ለሚሰጥ : መንፈስ ። ማንፈሳዊ : ግን : የፊተኛው : አይደለም ። ነፍሳዊ : ነበረ : እንጅ ። ከዚያም : በኋላ : መንፈሳዊ ። የፊተኛው : ሰው : መሬታዊ : ነው : ከምድር : ሁለተኛው : ሰው : ጌታ : ከሰማይ ። እንደ : መሬታዊም : እንዲሁም : መሬታውያን : ናቸው ። እንደ : ሰማያዊም : እንዲሁ : ደግሞ : ሰማያውያን : ናቸው ። የዚያንም : የመሬታዊን : መልክ : እንደ : ለበስነ ። እንዲሁም : የዚያን : የሰማያዊውን : መልክ : እንለብሳለን ። ይህንንም : እላለሁ : ወንድሞቼ : ሆይ ። ሥጋና : ደም : የሰማይን : መንግሥት : ይወርስ : ዘንድ : እንዳይችል ። የሚጠፋም : አለመጥፋትን : አይወርስም ። እነሆ : በምሥጢር :



እነግራችኋለሁ ። እኛ : ሁላችን : እንደንተኛ ። ነገር : ግን : ሁላችን : እንለወጣለን ። ድንገት : እንደ : ቅጽበተ : ዓይን ። የኋለኛው : መለከት : ሲነፋ : ጊዜ ። መለከት : ይነፋልና : ሙታንም : ያለ : ጥፋት : ይነሣሉ : እኛም : እንለወጣለን ። ይኽ : የሚጠፋው : አለመጥፋትን : ይለብስ : ዘንድ : አለውና ። ይኽም : የሚሞተው : አለመሞትን : ይለብስ : ዘንድ : አለው ። ይኽም : የሚጠፋው : አለመጥፋትን : ሲለብስ : ጊዜ : ይኽም : የሚሞተው : አለመሞትን : ሲለብስ : ጊዜ ። የዚያን : ጊዜ : ይፈጸማል : የተጻፈው : ነገር ። ሞት : በማሸነፍ : ተዋጠ ። የታለ : ሾህኽ : ሞት : ሆይ ። ማሸነፍኽስ : የታለ : ሲኦል : ሆይ ። የሞት : ሾህ : ኃጢአት : ነው ። የኃጢአትም : ኃይል : ኦሪት : ናት ። ነገር : ግን : ለእግዚአብሔር : ምስጋና : ይድረሰው : ማሸነፍ : የሰጠን : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ ። ስለዚኽም : የተወደዳችሁ : ወንድሞቼ : ሆይ : የጸናችሁ : ሁኑ ። ሳትናወጡም ። የተረፋችሁም : ሁኑ : የጌታን : ስራ : በመስራት : ሁልግዜ ። አውቃችሁ : ድካማችሁ : በከንቱ : እንዳይደለ : በጌታ : ዘንድ ።

ወደ : መቃበርም : ሲደርሱ : ሬሳውንም : ወደርሱ :
ለመግባት : ሲያበጁ : ጊዜ : ቄስ : ብቻውን : ወ
ይስ : ካንባቦች : ጋራ : እንዲህ : ይበል ።

ከሴት : የተወለደ : ሰው : ጥቂት : ዘመን : ይኖራል : መከራም : ይመላበታል ። እንደ : አበባም : ይወጣል : ይጨዷልም ። እንደ : ጽላም : ይኰበላል : አይኖርምም ።

በሕይወት : መኻከል : ሞት : ይከበናል ። ከማንም : ረዴትን : ልንሻ : ካንተ : ባይሆን : አቤቱ : በቅን : በኃጢአታችን : መክንያት : ከተቈጣህብን ።

ነገር : ግን : አቤቱ : በሁሉ : ቅዱስ : ሁሉንም : የምትችል : እግዚአብሔር : ሆይ : ቅዱስ : በሁሉም : መሓሪ : ማደን : ሆይ : ለዘላለም : ጭንቀትና : ሞት : አትስጠን ።

አንተ : አቤቱ : የልባችነን : ምሥጢር : ታውቃለህና : የ

ምህረትህን ፡ ጀር ፡ በጸሎታችን ፡ አትዝጋ ። አዘንልን ፡ አን ጅ ፡ አቤቱ ፡ በሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ፡ ሁሉንም ፡ የምትችል ፡ አ ምላክ ፡ ሆይ ፡ ቅዱስም ፡ በሁሉም ፡ መሐሪ ፡ ማደን ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ለዘላለም ፡ የከበርህ ፡ ፈራጅ ፡ ሆይ ፡ በኋለኛ ፡ ሰዓታ ችንና ፡ በጻረሞታችንም ፡ ጠብቅን ፡ ካንተ ፡ እንደንወድቅ ።

ከዚያ ፡ ወደ ፡ ያም ፡ ከዚያ ፡ ቁመው ፡ ካሉ ፡ ሰዎች ፡ አንድ ፡ ሬሳውን ፡ ባፈር ፡ ይድፈን ፡ ቄስም ፡ እን ዲህ ፡ ይበል ።

ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአብሔር ፡ በታላቅ ፡ ምህረቱ ፡ ከዚህ ፡ የፈለሰውን ፡ የተወደደውንም ፡ ወንድማችን ፡ ነፈ ስ ፡ ወደርሱ ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ወድዋልና ፡ እኛ ፡ ሥጋውን ፡ ለምድር ፡ አሳልፈን ፡ እንሰጣለን ፡ መሬትን ፡ ለመሬት ፡ አመድንም ፡ ላመድ ፡ አፈርንም ፡ ላፈር ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፡ መንሣቱን ፡ የጸናችውን ፡ የማንጠራጠርባትን ም ፡ ተስፈ ፡ አድርገን ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። እርሱም ፡ የበላሻውን ፡ ሥጋችንን ፡ ይለውጣልና ፡ ለከበረ ውንም ፡ ሥጋው ፡ ምሳሌ ፡ ያደርገዋልና ፡ ሁሉን ፡ ለራሱ ፡ ያስገዛ ፡ ዘንድ ፡ እንደሚችልባት ፡ እንደ ፡ ኃይሉ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንዲህ ፡ ይባል ፡ ወይስ ፡ ይ ዘመር ።

ከሰማይም ፡ ቃልን ፡ ሰማሁ ፡ እንዲህ ፡ ያለኝን ። ጻፈ ። በጌ ታ ፡ የሚሞቱ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ ካሁን ፡ ጀምረው ። አወ ን ። መንፈስ ፡ ይላል ፡ ከድካማቸው ፡ ያርፉ ፡ ዘንድ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቄስ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።

አቤቱ ፡ ማረን ።

ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረን ።

አቤቱ ፡ ማረን ።

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ። ስምህ ፡ ይቀደ ስ ። መንግሥትህ ፡ ትምጻ ። ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እ ንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ። እንጀራችንን ፡ የሚበቃንን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ። ይቅር ፡ በለን ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡ እኛ ፡ ይግመን ፡ ይቅር ፡



እንደምንል ፡ ለኛ ፡ ያለባቸውን ። ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባ ን ። ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ። አሜን ።

ቄስ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ በጌታ ፡ ኑረው ፡ ከ ዚህ ፡ የሚፈልሱ ፡ ሰዎች ፡ መናፍስታቸው ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ሕያዋን ፡ ናቸውና ፡ የምእምናንም ፡ ነፍስ ፡ ከሥጋ ፡ ሸክ ም ፡ ተፈትታ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ በደስታና ፡ በደህንነት ፡ ትኖራ ለችና ። ይህነን ፡ ወንድማችን ፡ ከዚህ ፡ ኃጢአት ፡ ከመላበ ት ፡ ካለም ፡ ጭንቀት ፡ ስለ ፡ አደንህው ፡ እናመሰግንሃለን ። ደግሞም ፡ በምህረትህ ፡ ቸርነት ፡ የምራጨችህን ፡ ቍጥር ፡ ቶሎ ፡ እንድትፈጽም ፡ የመንግሥትህንም ፡ መምጣት ፡ እ ንድታስቸኵል ፡ እንለምንሃለን ፡ እኛ ፡ በተቀደሰች ፡ ስም ህ ፡ በውነተኛ ፡ ሃይማኖትዋ ፡ ከፈለሱ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ በሥጋ ና ፡ በነፍስ ፡ በዘላለም ፡ ምስጋና ፡ ፍጽምት ፡ ፍጻሜና ፡ ደ ስታ ፡ እንከፈፈል ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

ጸሎት ።

መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አባት ፡ እርሱ ፡ ትንሣኤና ፡ ሕይወት ፡ ነውና ፡ በርሱም ፡ የ ሚያምን ፡ ሁሉ ፡ ቢሞት ፡ እንኳ ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ፡ ሕያ ውም ፡ ሁኖ ፡ የሚያምንበት ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ አይሞት ም ። እርሱም ፡ በቅዱስ ፡ ሐዋርያው ፡ በጳውሎስ ፡ አፉ ፡ ተ ስፈ ፡ እንደ ፡ ሌላቸው ፡ ሰዎች ፡ በርሱ ፡ ላንቀላፉ ፡ እንደናለ ቅስ ፡ አስተማረነ ። እኛ ፡ በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ አባ ታችን ፡ ሆይ ፡ ከኃጢአት ፡ ሞት ፡ ለጽድቅ ፡ ሕይወት ፡ እን ድታስነሣን ፡ ይህ ፡ ወንድማችን ፡ በርሱ ፡ እርፎ ፡ ተስፈ ፡ እ ንድናደርግ ፡ እንደሁም ፡ እኛ ፡ ይህችን ፡ ሕይወት ፡ ስንሰኑብ ት ፡ ጊዜ ፡ በርሱ ፡ እናርፍ ፡ ዘንድ ፡ በኋለኛ ፡ ቀንም ፡ በሙ ታን ፡ ትንሣኤ ፡ እኛ ፡ በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ እናገኝ ፡ ዘንድ ፡ የ ተወደደ ፡ ልጅህም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በሚወዱህና ፡ በሚፈ ሩህ ፡ ሁሉ ፡ የሚባርከውን ፡ በረከት ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ፡

እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ ኑ ፡ የተባረካችሁ ፡ ያባቴ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ ካለም ፡ አስቀድሞም ፡ የተሰናደችላችኋትን ፡ መንግሥት ፡ ተቀበሉ ፡፡ ይህነን ፡ ስጥ ፡ እንለምንሃለን ፡ መሐሪ ፡ አብ ፡ ሆይ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በመኻከለኞችንና ፡ ማድኃናችን ፡፡ አሜን ፡፡

የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ፍቅር ፡፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አንድነት ፡ ከሁላችን ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

---

# የዳዊት ፡ መዝሙራት ፡፡

## መጀመርያ ፡ ቀን ፡፡

### የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

### መዝሙር ፡ ፩፤

፩፤ ምስጉን ፡ ነው ፡ በክፎች ፡ ምክር ፡ ያልሔደ ፡ ሰው ፡
በኃጢአተኞችም ፡ መንገድ ፡ ያልቆመ ፡
በዋዘኞችም ፡ ወንበር ፡ ያልተቀመጠ ፡፡
፪፤ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ደስ ፡ የሚለው ፡ እንጂ ፡
ነፍሱንም ፡ ወደ ፡ ሕጉ ፡ የሚያደርግ ፡ በቀንና ፡ በሌት ፡፡
፫፤ እርሱ ፡ በውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ ደር ፡ እንደ ፡ ተተከለች ፡
ይሆናል ፡
ፍሬዋን ፡ በየጊዜዋ ፡ እንደምትሰጥ ፡
ቅጸልዋም ፡ እንደማይረግፍ ፡፡
የሚሰራውንም ፡ ሁሉ ፡ በጅ ፡ ይለዋል ፡፡
፬፤ ክፎች ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አይደሉም ፡
ንፋስ ፡ ነፋሶ ፡ እንደሚወስደው ፡ ትቢያ ፡ እንጂ ፡፡
፭፤ ስለዚኽ ፡ ክፎች ፡ በፍርድ ፡ አይቆሙም ፡
ኃጢአተኞችም ፡ በጻድቃን ፡ ማኅበር ፡፡
፮፤ እግዚአብሔር ፡ የጻድቃንን ፡ መንገድ ፡ ያውቃልና ፡፡
የኃጢአተኞች ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ትጠፋለች ፡፡

### መዝሙር ፡ ፪፤

፩፤ ለምን ፡ ያብዳሉ ፡ አሕዛብ ፡
ሰዎችም ፡ ከንቱ ፡ ይናገራሉ ፡፡
፪፤ ነገሥተ ፡ ምድር ፡ ተነሡ ፡
መኳንንትም ፡ ባንድ ፡ ተማከሩ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ በመሢሑም ፡፡
፫፤ ማሰርያቸውን ፡ እንብጠስ ፡

454

## ቅያሜ ፡

የእግዚአብሔር ፡ ቍጣና ፡ ፍርድ ፡ ነገር ፡ በኃጥአን ፡ ላይ ። አያሌ ፡ ለመናችም ። ባርባ ፡ ጾም ፡ በ መጀመርያ ፡ ቀን ፡ በሌላ ፡ ጊዜም ፡ የቀሳውስት ፡ አለቃ ፡ ደህና ፡ ሁኖ ፡ ሲመስለው ፡ ለመድገም ።

---

ከጽዋት ፡ ጸሎት ፡ ከሊጣንያም ፡ በኋላ ፡ ቄስ ፡ በጸሎት ፡ ወይስ ፡ በስብከት ፡ ስፍራ ፡ ቁሞ ፡ እንደዚህ ፡ ይበል ።

ወንድሞቼ ፡ ሆይ ። በድር ፡ ቤት ፡ ክርስቲያን ፡ ደህች ፡ ደ ህና ፡ ተግሣጽ ፡ ነበረች ፡ በግልጽ ፡ በታላቅ ፡ ኃጢአት ፡ ኑረው ፡ የተጸየፉ ፡ ሰዎች ፡ በጾም ፡ አርብዓ ፡ መጀመርያ ፡ በግልጽ ፡ ተገሠጹ ፡ በዚህ ፡ ዓለምም ፡ ተቀሠፉ ። ነፍሳቸው ፡ በእግ ዚአብሔር ፡ በሚመጣ ፡ ቀኑ ፡ ትድን ፡ ዘንድ ። ሌሎችም ፡ በምሳሌያቸው ፡ ተመክረው ፡ ከመበደል ፡ ደፈሩ ፡ ዘንድ ።

በዚህ ፡ ማድረግም ፡ ፈንታ ፡ የሚገባ ፡ ይመስላል ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በሁላችሁ ፡ ጆሮ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መርገም ፡ በማይ መለሱ ፡ ኃጥአን ፡ ላይ ፡ ከኦሪት ፡ ዘዳግም ፡ ከ፳፯፤ ምዕ ራፍ ፡ ከሌላም ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ክፍል ፡ ተይዞ ፡ ይነ በብ ፡ ዘንድ ፡ እላንትም ፡ ለነገሩ ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ብላችሁ ፡ ትመልሱ ፡ ዘንድ ። እላንት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታላቅ ፡ ቍጣ ፡ በኃጢአተኞች ፡ ላይ ፡ ሰምታችሁ ፡ ለውነተኛና ፡ ለደ ህና ፡ ንስሐ ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡ በዚህም ፡ እጅግ ፡ ፍርሃትና ፡ ስሕተት ፡ ያለበት ፡ ዘመን ፡ በጣም ፡ ተጠንቅቃችሁ ፡ እንድ ትመላለሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መርገም ፡ እንደ ገባለት ፡ እላንት ፡ ባፈችሁ ፡ ካጸናችሁት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ትሸሹ ፡ ዘንድ ።

ቄስ ። የተጸረበችን ፡ የተቀለጠችንም ፡ ምሳሌ ፡ ለመሰ ገድ ፡ የሚያድርግ ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ሕዝብም ፡ መልሰው ፡ እንደዚህ ፡ ይበሉ ። አሜን ።



ቄ ። አባቱን ፡ ወይስ ፡ እናቱን ፡ የሚረግም ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። የጎረቤቱን ፡ የወሰኑን ፡ ምልክት ፡ የሚያርቅ ፡ ር ጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። ዕውርን ፡ ከመንገዱ ፡ የሚያስት ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። የንግደውን ፡ አባትና ፡ እናትም ፡ የሌለውን ፡ የባል ቴትንም ፡ ፍርድ ፡ የሚያጠማማ ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። ባልንጀራውን ፡ በስውር ፡ የሚመታ ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። ከባልንጀራው ፡ ምሽት ፡ ጋራ ፡ የሚተኛ ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። ንጹሑን ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ለማድረስ ፡ መማለጀውን ፡ የሚወስድ ፡ ርጉም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። ሰውን ፡ ተስፋውን ፡ የሚያደርግ ፡ ሥጋንም ፡ ለክን ዱ ፡ የሚያደርግ ፡ ልቡም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚርቅ ፡ ርጉ ም ፡ ነው ።

ም ። አሜን ።

ቄ ። የማይምሩ ፡ የሚዘሙም ፡ የሚያመነዝሩም ፡ የ ሚስሱም ፡ ለጣዖታትም ፡ የሚሰግዱ ፡ አላካኮችም ፡ ሰካ ሮችም ፡ ዐራጠኞችም ፡ ሰዎች ፡ የተረገሙ ፡ ናቸው ።

ም ። አሜን ።

ቄስ ። አሁንም ፡ (ነቢዩ ፡ ደዊት ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ መሰከረ ፡) የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዛት ፡ ትተው ፡ የሚናቅፉ ፡ እን ደ ፡ ተረገሙ ፡ አይታችኋልና ፡ በራሳችን ፡ ላይ ፡ የተንጠለጠ ለቸውን ፡ ወትሮም ፡ እንደትወድቅብን ፡ ጥቂት ፡ የቀረላ ትን ፡ የምታስፈራውን ፡ ኩነኔ ፡ አስበን ፡ ወደ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ እንመለስ ፡ በተሰበረና ፡ በተዋረ ደ ፡ ልባችን ፡ ኃጢአት ፡ በመላች ፡ ሕይወታችን ፡ አዝነን ፡ በ

መበደላችንም ፡ አስታውቀንና ፡ ተናዝን ፡ ለንስሓም ፡ የሚ
ገባውን ፡ ፍሬ ፡ እናወጣ ፡ ዘንድ ፡ ተጋድለን ። መቍረጫ ፡ አ
ሁን ፡ ወደ ፡ ዛፎች ፡ ሥር ፡ ተጨምራለችና ፡ በጎ ፡ ፍሬንም ፡
የማታፈራ ፡ ዛፍ ፡ ትቈረጣለች ፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ትጣላለ
ች ። ወደ ፡ ሕያው ፡ አምላክ ፡ እጅ ፡ መውደቅ ፡ የሚያስፈ
ራ ፡ ነገር ፡ ነው ። እርሱ ፡ በኀጥአን ፡ ላይ ፡ ወጽመድን ፡ እሳ
ትንም ፡ ዲንንም ፡ ያዘንባል ። ይህም ፡ የጽዋቸው ፡ ፈንታ ፡
ለመጠጣቸው ፡ ይሆናል ። እነሆ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከስፍራ
ው ፡ መጥትዋልና ፡ በምድር ፡ የሚኖሩ ፡ ዐመፃቸውን ፡ ይ
መራምር ፡ ዘንድ ። ደሮ ፡ ማን ፡ ይችላል ፡ መታየቱን ፡ ይታገ
ሥ ፡ ዘንድ ። መሽኑ ፡ በጁ ፡ ነውና ፡ አውድማውንም ፡ ያነጻ
ል ፡ ስንዴንም ፡ ወደ ፡ መክተቻው ፡ ይለቅማል ፡ ትቢያው
ንም ፡ በማይጠፋ ፡ እሳት ፡ ያቃጥላል ። የጌታም ፡ ቀን ፡ እ
ንደ ፡ ሌባ ፡ በሌት ፡ ይመጣልና ፡ ሰውም ፡ ደህና ፡ ነገርም ፡
ሁሉ ፡ ምንም ፡ አይለም ፡ ሲሉ ፡ ጊዜ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጥፋ
ት ፡ በድንገት ፡ ትመጣባቸዋለች ፡ ምጥ ፡ በጸነሰች ፡ ሴት ፡
እንደምትመጣ ፡ መሸሸትም ፡ የለም ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በ
በቀል ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ትነደለችና ፡ ያልተመ
ለሱ ፡ ኀጥአን ፡ በልባቸው ፡ ድንዛዜ ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ያ
ከማቹዋት ፡ እርሳቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡ መታ
ገሡንም ፡ ርኅራኄውንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ንስሓ ፡
በጸራቸው ፡ ጊዜ ፡ ንቀው ፡ ነበሩና ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይላል ፡
እግዚአብሔር ፡ ይጸሩበኛል ፡ እኔም ፡ አልሰማም ፡ ማልደው
ም ፡ ይሹኛል ፡ አያገኙኝም ። ዕውቀትን ፡ ጸልተው ፡ ነበሩና ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ፍርሃት ፡ አልተቀበሉም ፡ ምክሬን ፡
ጣሉ ፡ እንጅ ፡ ተግሣጼንም ፡ ናቁ ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደጁ ፡ በ
ተቈለፈ ፡ ጊዜ ፡ የመውቃት ፡ ጊዜ ፡ አለፈ ። የመፍረድም ፡
ጊዜ ፡ ሲሆን ፡ የምህረት ፡ ጊዜ ፡ አልፎ ፡ ይሆናል ። እንደ ፡
ምን ፡ ያስፈራል ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ጻድቅ ፡ ያለው ፡ የፈራጅ ፡
ቃል ፡ በላያቸው ፡ እንዴህ ፡ ሲል ። ሒዱ ፡ እላንት ፡ ርጉማ
ን ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ እሳት ፡ ለሰይጣንና ፡ ለመላእክቱ ፡ ወ
ደ ፡ ተዘጋጀ ። ስለዚህ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ በጊዜ ፡ እንጠንቀ



ቅ ፡ የመድኀኒት ፡ ቀን ፡ ሲሆን ፡ ሰው ፡ አንደችን ፡ ይሰ
ራባት ፡ ዘንድ ፡ የማይችል ፡ ሌት ፡ ትመጻለችና ። ብርሃ
ን ፡ ሲኖርልን ፡ በብርሃን ፡ እንመን ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ል
ጆችም ፡ እንመላለስ ፡ ወደ ፡ ጭራሽ ፡ ጨለማ ፡ ልቅሶና ፡
የጥርስ ፡ መፋጨት ፡ ወደለበት ፡ እንደንጣል ። የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቸርነት ፡ አናቃልል ። እርሱ ፡ በምህረቱ ፡ ወደ ፡
ንስሓ ፡ ጸርቶናልና ፡ ወሰንም ፡ በሌላት ፡ በርኅራኄው ፡
ያለፈውን ፡ ኀጢአታችን ፡ ይሰርይልን ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡
አስደርጎልናልና ፡ እኛ ፡ ከለልባችን ፡ ወደርሱ ፡ ብንመለ
ስ ። ኀጢአታችን ፡ እንኳ ፡ እንደ ፡ ናስም ፡ ቢቀላ ፡ እንደ ፡ በ
ረደ ፡ ነጭ ፡ ይሆናል ፡ እንደ ፡ ቀርመዝም ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ነ
ጭ ፡ ሱፍ ፡ ይነጻል ። እግዚአብሔርም ፡ እንደህ ፡ ይላል ።
ከኀጢአታችሁ ፡ ተመለሱ ፡ ኀጢአታችሁም ፡ ጥፋታችሁ ፡
አይሆንም ። ያደረጋችሁትን ፡ ኀጢአታችሁን ፡ አውጥታችሁ ፡
ተው ። አዲሱን ፡ ልብና ፡ አዲስ ፡ መንፈስን ፡ አድርጉላች
ሁ ። ስለ ፡ ምን ፡ ሞታችሁን ፡ ትሻላችሁ ፡ እላንት ፡ የእሥ
ራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ የሚሞተው ፡ ሞት ፡ ደስ ፡ አይ
ለኝምና ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ። ተመለሱ ፡ እ
ንጊዴህ ፡ ትድኑማላችሁም ። መበደልስ ፡ በደልነ ፡ ደሮ ፡ በ
አብ ፡ ዘንድ ፡ መድኅን ፡ አለን ፡ እርሱም ፡ የሱስ ፡ ክርስቶ
ስ ፡ ያ ፡ ጻድቁ ፡ እርሱም ፡ የኀጢአታችን ፡ ማስተስረያ ፡ ነ
ው ። እርሱ ፡ ስለ ፡ መበደላችን ፡ ቍስልዋልና ፡ ስለ ፡ ዐመ
ፃችንም ፡ ተመትትዋልና ። ስለዚህ ፡ ወደርሱ ፡ እንመለስ ፡
እርሱ ፡ ስለ ፡ ኀጢአታቸው ፡ በውነት ፡ የሚያዝኑትን ፡ ሁሉ
ን ፡ በምህረት ፡ ይቀበላልና ። እርሱም ፡ በውነተኛ ፡ ንስሓ ፡
በንደርስለት ፡ ይቀበለን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀ ፡ ይሰርይል
ንም ፡ ዘንድ ፡ እንደ ወድ ፡ እንመን ። ለርሱም ፡ በጣም ፡ እ
ንገዛ ። ከንጊዴህ ፡ ወዴህም ፡ በመንገዱ ፡ እንመላለስ ፡ ዘን
ድ ፡ የቀለለውንም ፡ ቀምበሩንና ፡ ሸክሙን ፡ በላያችን ፡ እ
ንሸከም ፡ ዘንድ ፡ በትሕትናም ፡ በትዕግሥትም ፡ በፍቅርም ፡
እንከተለው ፡ ዘንድ ፡ ለመንፈስ ፡ ቅዱሱም ፡ ስራ ፡ እንታዘ
ዝ ፡ ዘንድ ፡ ወትሮ ፡ ክብሩን ፡ ሽትን ፡ በመጸራታችንም ፡ ደ

ስ : ብለን : ስናመሰግነው : ለርሱም : አገልግለን : የጸናች : ፈ
ቃደኞችን : ትሁን :: እንዲህ : ቢሆን : ክርስቶስ : ከኦሪት :
መርገም : ወደ : ግራ : እጁም : በሚቆሙ : ላይ : ከምትወ
ድቅ : ኩነኔው : ያድነናል : ወደ : ቀኙም : ያኖረናል : ያባቱ
ንም : የተወደደውን : በረከት : ይሰጠናል : ወደ : ከበረች
ም : መንግሥቱ : ለመግባት : ያዘናል :: ይህም : በዘላለም :
ምህረቱ : ለሁላችን : ፈንታ : ይስጠን :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ሁላቸው : ይምበርክኩ : ቀሳው
ስትና : አንባቦችም : ሊጣኒያ : ወትሮ : ወደሚ
ደገምበት : ስፍራ : ተምበርክከው : ይህነን : መ
ዝሙር : ብለው : ይጸልዩ ::

መዝሙር : ፶፩፤

አቤቱ : እንደ : ምህረትኽ : መጠን : ማረኝ ::
እንደ : ርኅራኄኽም : ብዛት : ዐመፃዬን : ደምስስ ::
ከመበደሌ : ፈጽመኽ : አጽበኝ : ከኃጢአቴም : አንጻኝ ::
እኔ : ዓመፃዬን : አውቃለሁና :
ኃጢአቴም : ሁልግዜ : በፊቴ : ነው ::
አንተን : ብቻ : በደልሁ : በፊትኽም : ክፉ : አደረግሁ ::
በነገርኽ : ትጸድቅ : ዘንድ : በፍርድኽም : ንጹሕ : ትሆን :
ዘንድ ::
ባመፃ : እነሆ : ተሰርቻለሁና : እናቴም : በኃጢአት :
አረገዘችኝ ::
እነሆ : እውነትን : በውስጥ : ወደኻል :
በስውርም : ጥበብን : ታስታውቀኛለኽ ::
በሂሶጵ : ርጪኝ : እነጻማለሁ :
አጽበኝ : ከበረደም : ነጭ : እሆናለሁ ::
ሐሤትንና : ደስታውን : አስማኝ ::
የሰበርኻቸውም : አፅንቶች : ደስ : ይላቸዋል ::
ከኃጢአቴ : ፊትኽን : መልስ : በደሌንም : ሁሉን : ደምስስ ::
ንጹሕ : ልብ : ፍጠርልኝ : አቤቱ :: የቀናውንም : መንፈስ :
በውስጤ : አድስ ::



ከፊትኽ : አጣለኝ : ቅዱስ : መንፈስኽንም : አትውሰድብኝ ::
የማደንኽን : ደስታ : መልስልኝ : በእሽታ : መንፈስም :
ደግፈኝ ::
ዐመፀኞችንም : በመንገድህ : አስተምራለሁ :
ኃጢአተኞችም : ወደንተ : ይመለሳሉ ::
ከደምም : አድነኝ : እግዚአብሔር : የመድኃኒቴ : አምላክ ::
መላሴም : በጽድቅኽ : ሐሤትን : ታደርጋለች ::
ከንፈሮቼን : ክፈት : አቤቱ : አፌም : ምስጋናኽን : ይነግራል ::
ብትወድስ : መሥዋዕትን : በሰጠሁ ::
የሚቃጠለውን : መሥዋዕት : አትወድም ::
የእግዚአብሔር : መሥዋዕት : የተሰበረ : መንፈስ : ነው :
የተሰበረውን : የተደቈሰውንም : ልብ : አትንቅም : እግዚ
አብሔር : ሆይ ::
በሞገስኽ : ፅዮንን : አብጀት : አቤቱ ::
የየሩሳሌምንም : መከበብዮች : ሥሪ ::
የዚያን : ጊዜ : የጽድቅን : መሥዋዕት : ትወደለኽ :
የመቃጠል : መሥዋዕትም : ፍጹም : መሥዋዕትም ::
የዚያን : ጊዜ : በመሠዊያኽ : ላይ : ፍሪዳችን : ይሠዋሉ ::
ምስጋና : ይሁን : ለአብ : ለወልድም : ለመንፈስ : ቅዱ
ስም ::

በመጀመርያ : እንደ : ነበረ : አሁንም : እንዲሆን : ለዘወ
ትርም : እንደለው :: ለዘላለም :: አሜን ::

አቤቱ : ማረነ ::
ክርስቶስ : ሆይ : ማረነ ::
አቤቱ : ማረነ ::

አባታችን : ሆይ : በሰማይ : የምትኖር :: ስምህ : ይቀደ
ስ :: መንግሥትህ : ትምጻ :: ፈቃድህ : በምድር : ትሁን : እ
ንደ : ሆነች : በሰማይ :: እንጀራችንን : የሚበቃንን : ስጠነ :
ዛሬ :: ይቅር : በለነ : በኛ : ያለውን :: እኛ : ደግመን : ይቅ
ር : እንደምንል : ለኛ : ያለባቸውን :: ወደ : ፈተናም : አታግ
ባን :: ከክፉ : አድነን : እንጅ :: አሜን ::

ቄስ :: አቤቱ : ባሮችህን : አድን ::

ምላሽ :: ባንተ : የሚታመኑትን ::

ቄ :: ረድኤትን : ከበላይ : አውርድልን ::

ም :: ለዘላለምም : በኃይልህ : ጠብቀን ::

ቄ :: አቤቱ : መድኃኒታችን : ሆይ : እርዳን ::

ም :: ስለ : ስምህም : ምስጋና : አድነን :: ስለ : ስምህም : መክንያት : እኛን : ኃጢአተኞችን : ማረነ ::

ቄ :: አቤቱ : ጸሎታችንን : ስማ ::

ም :: ጩኸታችንም : ወደንተ : ትድረስ ::

ቄስ :: እንጸልይ ::

አቤቱ : እንለምንሃለን : ጸሎታችንን : ስማ : በኃጢአታቸውም : ለሚያስታውቁህ : ሁሉ : እዘንላቸው : እርሳቸው : ልባቸው : በኃጢአት : ተከስዊልና : በምህረትህ : ስርየት : ይፈቱ : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::

ሁሉን : የምትችል : አምላክ : መሐሪም : አባት : ሆይ :: አንተ : ለሰው : ሁሉ : ትራራለህና : ከፈጠርሀውም : ሁሉ : አንዳችን : አትጸላምና : የኃጢአተኛውን : ሞት : የማትሻ : ከኃጢአቱ : እንዲመለስ : እንዲድንም : እንጅ :: አንተ : በምህረትህ : መተላለፋችንን : ይቅር : በለነ : ተቀበለነም : አጽናናንም : በኃጢአታችን : ሸክም : በታች : ሁነን : አዝነናልና : ደክመናልምና :: ወትሮ : ምህረት : ማድረግ : ጠባይህ : ነውና : ኃጢአትንም : ይቅር : ማለት : ላንተ : ብቻ : ይገባልና : እዘንልን : አቤቱ : ለተበዝሃቸው : ሕዝብህ : እዘን :: ከባሮችህ : ጋራ : ወደ : ፍርድ : አትግባ : እኛ : ርኩስ : መሬት : ችጋረኞች : ኃጥአንም : ነነ :: ቍጣህን : ከኛ : ዘንድ : መልስ : እንጅ :: ርኵስነታችንን : አውቀናልና : ስለ : መበደላችንም : በውነት : አዝነናልና :: ፈጥነህም : አድነን : በዚህ : ዓለም : በሚመጣ : ዓለም : ካንተ : ጋራ : ለዘላለም : ሕያዋን : ሁነን : እንኖር : ዘንድ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን :: አሜን ::



የዚያን : ጊዜ : ጉባኤ : ቄስን : ተከትለው : እንዲህ : ይበሉ ::

አንተ : አቤቱ : መልሰን : እኛም : እንመለሳለን :: ራራ : አቤቱ : ለሕዝብህ : ራራ : አልቅሰው : ጹመውም : ለምኑውም : ወደንተ : ለሚመለሱ :: አንተ : መሐሪ : አምላክ : ነህና : ርኅራኄህ : የመላች : ትዕግሥትህም : የረዘመች : ምህረትህም : የበዛች :: እኛስ : መቅሠፍት : ቢገባነ : አንተ : በቍጣህ : እንኳ : ለምህረት : ታስባለህ :: ለሕዝብህ : እዘን : አቤቱ : እዘንልን : ርስትህም : አትፈር :: አቤቱ : ስማነ : ምህረትህ : በዝታለችና :: በምህረትህም : ብዛት : እይን : በተባረከ : ልጅህ : በየሱስ : ክርስቶስ : በጌታችን : ምግባርና : መኻከለኝነት :: አሜን ::

የዚያን : ጊዜም : ቄስ : ብቻውን : እንዲህ : ይበል ::

እግዚአብሔር : ይባርከን : ይጠብቀንም :: እግዚአብሔር : የፊቱን : ብርሃን : በላያችን : ያብራልን :: ሰላምንም : ይስጠን : አሁንና : ለዘላለም :: አሜን ::

---

# የእንግሊዝ፡ቤት፡ክርስቲያን፡የሃይማኖትዋ፡ ትምህርት፡በ፴፱፡ ቃላት።

## ፩። ስለ፡ቅድስት፡ሥላሴ።

አንድ፡ሕያውና፡እውነተኛ፡አምላክ፡ብቻ፡አለ። እርሱም፡ለዘላለም፡የሚኖር። ሥጋም፡ክፍልም፡ሕማማትም፡የሌለው። ኃይሉም፡ጥበቡም፡ቸርነቱም፡ያልተወሰነች። የሚታይም፡የማይታይም፡ነገር፡ሁሉ፡ፈጣሪና፡ጠባቂ። በዚች፡መለኮትም፡አንድነት፡ሦስት፡አካላት፡አሉ፡ያንዲት፡ህላዌ፡ኃይልም፡ዘላለምናም። እርሳቸውም፡አብ፡ወልድም፡መንፈስ፡ቅዱስም።

---

## ፪። ስለ፡ቃል፡ስለ፡እግዚአብሔር፡ልጅ፡እርሱም፡ እውነተኛ፡ሰው፡የሆነ።

ወልድ፡የአብ፡ቃል፡የሚሆን፡ከአብም፡ከዘላለም፡የተወለደ፡እርሱም፡እውነተኛ፡የዘላለምም፡አምላክ፡ከአብም፡ጋራ፡ያንድ፡ባሕሪ፡ያለ፡በተመሰገነች፡ድንግል፡በማኅፀንዋ፡ሲሆን፡ከባሕሪዋ፡የሰውን፡ጠባይዕ፡ተቀበለ። እንደሁም፡ሁለት፡ምሉኣትና፡ፍጹማት፡ጠባያት፡እርሳቸውም፡መለኮትና፡ሰውነት፡ባንድ፡አካል፡ተዋህደ፡ከቶ፡የማይለዩ። አንድ፡ክርስቶስ፡የሆነ። እርሱም፡እውነተኛ፡አምላክ፡እውነተኛም፡ሰው፡ነው። እርሱም፡በውነት፡መከራ፡ተቀበለ። ተሰቀለም። ሞተም። ተቀበረም። አባቱን፡ያስታርቅልን፡ዘንድ። መሥዋዕትም፡ይሆን፡ዘንድ፡ስለ፡ሚወረስ፡ዕዳችን፡ብቻ፡አይደለም፡ሰው፡ስለ፡ሚያደርገውም፡ኃጢአት፡ሁሉ፡እንጅ።

---

## ፫። ስለ፡ክርስቶስ፡መውረድ፡ወደ፡ሲዖል።

ክርስቶስ፡ስለኛ፡እንደ፡ሞተ፡እንደ፡ተቀበረም፡እንደሁም፡ወደ፡ሲዖል፡እንደ፡ወረደ፡እናምናለን።

---



## ፬። ስለ፡ክርስቶስ፡ትንሣኤ።

ክርስቶስ፡በውነት፡ከሞት፡ተነሣ። ተመልሶም፡ገላውን፡ካፅንት፡ለሰው፡ጠባይዕም፡ፍጻሜ፡ከሚገባ፡ነገር፡ሁሉ፡ጋራ፡ወሰደ፡እንደሁም፡ወደ፡ሰማይ፡ወጣ። ከዚያም፡ይቀመጣል፡በሰው፡ሁሉ፡ይፈርድ፡ዘንድ፡እስኪመለስ፡ድረስ፡በኋለኛ፡ቀን።

---

## ፭። ስለ፡መንፈስ፡ቅዱስ።

መንፈስ፡ቅዱስ፡ከአብና፡ከወልድ፡የሚወጣ፡ያንድ፡ባሕሪ፡ምስጋናም፡ክብርም፡ነው፡ከአብና፡ከወልድ፡ጋራ፡እውነተኛም፡የዘላለምም፡አምላክ።

---

## ፮። መጽሐፍ፡ቅዱስ፡ለመድኃኒታችን፡ ይበቃል።

ለመድኃኒታችን፡የሚገባ፡ነገር፡ሁሉ፡በመጽሐፍ፡ቅዱስ፡ይገኛል። ስለዚህም፡በርሱ፡ያልተገኘ፡ወይስ፡እውነቱ፡ከርሱ፡የማይገለጽ፡ነገር፡ሁሉ፡እንደ፡ሃይማኖት፡ነገር፡አንቀበለውም። ለዘላለም፡መድኃኒትም፡አይፈለግም። መጽሐፍ፡ቅዱስ፡ግን፡የምንላቸው፡መጻሕፍት፡እሊያ፡መጻሕፍት፡ናቸው፡የቃኖን፡የሚሉት፡የብሉይና፡ያዲስ፡ኪዳን፡መጻሕፍት፡በሥልጣናቸው፡ከቶ፡ያልተጠራጠሩ፡

የቃኖንም፡መጻሕፍት፡ስምና፡ቍጥር፡ይህ፡ነው።

፩፡ ኦሪት፡ዘፍጥረት።
፪፡ ኦሪት፡ዘፀአት።
፫፡ ኦሪት፡ዘሌዋውያን።
፬፡ ኦሪት፡ዘኊልቊ።
፭፡ ኦሪት፡ዘዳግም።
፮፡ መጽሐፈ፡ኢያሱ፡ወልደ፡ነዌ።
፯፡ መጽሐፈ፡መሳፍንት።
፰፡ መጽሐፈ፡ሩት።
፱፡ መጽሐፈ፡ሳሙኤል፡ቀደማዊ።

፲፡ መጽሐፈ : ሳሙኤል : ካልእ ::
፲፩፡ መጽሐፈ : ነገሥት : ቀዳማዊ ::
፲፪፡ መጽሐፈ : ነገሥት : ካልእ ::
፲፫፡ መጽሐፈ : ዜና : መዋዕል : ቀዳማዊ ::
፲፬፡ መጽሐፈ : ዜና : መዋዕል : ካልእ ::
፲፭፡ የዕዝራ : መጀመርያ : መጽሐፍ ::
፲፮፡ የዕዝራ : ሁለተኛ : መጽሐፍ ::
፲፯፡ መጽሐፈ : አስቴር ::
፲፰፡ መጽሐፈ : ኢዮብ ::
፲፱፡ መጽሐፈ : መዝሙራት : ዘዳዊት ::
፳፡ መጽሐፈ : ምሳሌ ::
፳፩፡ መጽሐፈ : መክብብ ::
፳፪፡ መጽሐፈ : መኃልየ : መኃልይ ::
፳፫፡ ትንቢተ : ኢሳይያስ ::
፳፬፡ ትንቢተ : ኤርምያስ ::
፳፭፡ ሰቆቃወ : ኤርምያስ ::
፳፮፡ ትንቢተ : ሕዝቅኤል ::
፳፯፡ ትንቢተ : ዳንኤል ::
፳፰፡ ትንቢተ : ሆሴዕ ::
፳፱፡ ትንቢተ : ኢዮኤል ::
፴፡ ትንቢተ : ዓሞጽ ::
፴፩፡ ትንቢተ : አብድዩ ::
፴፪፡ ትንቢተ : ዮና ::
፴፫፡ ትንቢተ : ሚክያስ ::
፴፬፡ ትንቢተ : ናሆም ::
፴፭፡ ትንቢተ : አንባቆም ::
፴፮፡ ትንቢተ : ሰፎንያስ ::
፴፯፡ ትንቢተ : ሐጌ ::
፴፰፡ ትንቢተ : ዘካርያስ ::
፴፱፡ ትንቢተ : መልክያስ ::(*)

* እሌህ : ፴፱፡ የመጽሐፍ : ቅዱስ : መጀመርያ : ክፍል : ናቸው : የብሉይ : ኪዳንም : መጻሕፍት : ይባላሉ ::



የቀረም : መጻሕፍት : አጶክርፈውያን : ማለት : የተሰወሩ : መጻሕፍት : የሚልዋቸው : ቤተ : ክርስትያን : ሔሮንሙስ : እንዳለ : ለሕይወት : ምሳሌና : ለበጎ : ልማድ : ማስተማርያ : ብላ : ታነባቸዋለች : ለትምህርት : ማጽናትና : ምስክር : ግን : አታደርጋቸውም :: እርሳቸውም : እሌህ : ናቸው ::

የዕዝራ : ሶስተኛ : መጽሐፍ ::
የዕዝራ : አራተኛ : መጽሐፍ ::
የጦቢያስ : መጽሐፍ ::
የይሁዲት : መጽሐፍ ::
የአስቴር : መጽሐፍ : መጨመርያ ::
የጥበብ : መጽሐፍ ::
የየሱስ : የሲራክ : ልጅ : መጽሐፍ ::
የባሩክ : የነቢይ : መጽሐፍ ::
የሶስት : አሽከሮች : ዝማሬ ::
የሱሳና : ታሪክ ::
ስለ : ቤልና : ስለ : ዘንዶ ::
የምናሴ : ጸሎት ::
የመቃባውያን : መጀመርያ : መጽሐፍ ::
የመቃባውያን : ሁለተኛ : መጽሐፍ ::

ያዲስ : ኪዳንን : መጻሕፍት : ሁሉ : አብያተ : ክርስቲያናት : ሁሉ : እንደሚቀበልዋቸው : እኛም : እንቀበላቸዋለን : ቃናናውያንም : ሁነው : እንቈጥራቸዋለን ::(*)

* ያዲስ : ኪዳን : መጻሕፍት : እሌህ : ናቸው ::
፩፡ የማቴዎስ : ወንጌል ::
፪፡ የማርቆስ : ወንጌል ::
፫፡ የሉቃስ : ወንጌል ::
፬፡ የዮሐንስ : ወንጌል ::
፭፡ የሐዋርያት : ስራ ::
፮፡ የጳውሎስ : መልእክት : ወደ : ሮሜ : ሰዎች ::

## ፯። ስለ ፡ ብሉይ ፡ ኪዳን ።

የብሉይ ፡ ኪዳን ፡ ካዲስ ፡ ጋሪ ፡ አይጻላም ። በሁለታቸው ፡ በብሉይና ፡ ባዲስ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ለሰው ፡ ለመቀበል ፡ ተሰጥታላችና ፡ በክርስቶስ ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡

---

፯፡ የጳውሎስ ፡ መጀመርያ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ።
፰፡ የጳውሎስ ፡ ሁለተኛ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ።
፱፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ገላትያን ፡ ሰዎች ።
፲፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ሰዎች ።
፲፩፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ፊልጵስዩስ ፡ ሰዎች ።
፲፪፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቆላሳይስ ፡ ሰዎች ።
፲፫፡ የጳውሎስ ፡ መጀመርያ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ።
፲፬፡ የጳውሎስ ፡ ሁለተኛ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ።
፲፭፡ የጳውሎስ ፡ መጀመርያ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።
፲፮፡ የጳውሎስ ፡ ሁለተኛ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።
፲፯፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቲጦስ ።
፲፰፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ፊልሞን ።
፲፱፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ዕብራውያን ።
፳፡ የያዕቆብ ፡ ከቶሊካዊት ፡ መልእክት ።
፳፩፡ የጴጥሮስ ፡ መጀመርያ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።
፳፪፡ የጴጥሮስ ፡ ሁለተኛ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።
፳፫፡ የዮሐንስ ፡ መጀመርያ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።
፳፬፡ የዮሐንስ ፡ ሁለተኛ ፡ መልእክት ።
፳፭፡ የዮሐንስ ፡ ሦስተኛ ፡ መልእክት ።
፳፮፡ የይሁዳ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።
፳፯፡ የዮሐንስ ፡ ራእይ ።



መካከለኛ ፡ በሚሆን ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሰው ፡ መካከል ፡ እውነተኛ ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡ ሁንዋልና ። ስለዚህ ፡ ያባቶች ፡ አለቆች ፡ ስለሚያልፍ ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ ተስፋ ፡ እንደደረጉ ፡ የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡ አንሰማም ።

ከእግዚአብሔርስ ፡ በሙሴ ፡ የተሰጠች ፡ የሌዋውያን ፡ ሕግ ፡ ስለ ፡ ምድራዊ ፡ ማምለክ ፡ ባዘዘች ፡ ነገር ፡ ክርስቲያንን ፡ ሰዎች ፡ በውነት ፡ አትገዛም ። ያገርም ፡ ትእዛዛትዋ ፡ በመንግሥት ፡ ሁሉ ፡ በግድ ፡ መቀበል ፡ ከቶ ፡ አይገባም ። ይህ ፡ ግን ፡ ሳይቀር ፡ የሰውን ፡ ፈቃድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ለሚገዙ ፡ ትእዛዛት ፡ ከመታዘዝ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከቶ ፡ አልተፈታም ።

---

## ፰። ስለ ፡ ሦስት ፡ የሃይማኖት ፡ ምሳሌዎች ፡ ወይስ ፡ ስምቦሎች ።

እልያን ፡ ፫፡ የሃይማኖትን ፡ ምሳሌዎች ። የኒቅያን ፡ ምሳሌ ። ያታናስዮስንም ፡ ምሳሌ ። የሐዋርያትንም ፡ ምሳሌ ፡ በጣም ፡ ይቀበልዋቸው ፡ ዘንድ ፡ ያምንዋቸውም ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡እውነታቸው ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ትገለጻለችና ።

---

## ፱። ስለ ፡ ሚወረስ ፡ ኃጢአት ።

የሚወረስ ፡ ኃጢአት ፡ እርሱ ፡ አደምን ፡ መከተል ፡ አይደለም ፡ የጰላግዩስ ፡ ወገን ፡ በከንቱ ፡ እንደ ፡ ተጫወቱ ። እርሱ ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ የጠባዩ ፡ የባሕርዩም ፡ ጉድልና ፡ ጥፋት ፡ ነው ፡ እንጅ ፡ በልደቱ ፡ ከአደም ፡ የተቀበለው ። በዚህ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከመጀመርያ ፡ ጽድቅ ፡ እጅግ ፡ ራቀ ፡ በሰውነቱም ፡ ለክፉ ፡ ይዘነብላል ። ሥጋው ፡ ሁለግዜ ፡ ተመኝትዋልና ፡ በመንፈስ ፡ ላይ ። በመክንያቱም ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ለሚወለድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ የዘላለምም ፡ ኵነኔ ፡ ይገባዋል ። ይህም ፡ የሰውነታችን ፡ ሕማም ፡ ሁለተኛም ፡ በተወለዱ ፡ ሰዎች ፡ እንኳ ፡ ይቀራል ፡ በርሱም ፡ ይሆናል ፡ በዮናኒ ፡ ቋንቋ ፡ *φρόνημα σαρκὸς* ፍሮኔማ ፡ ሰርቆስ ፡ የተባለ ፡ ሥጋዊ ፡ ልብ ፡ እርሱም ፡ ሥጋዊ ፡ ማሰብ ፡

መመኸትም ፡ ፈቃድም ፡ የሚሆን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ እንደይገዛ ። በክርስቶስስ ፡ በውነት ፡ በሚያምኑ ፡ ፍርድና ፡ ኵነኔ ፡ የለባቸውም ። ይህ ፡ ግን ፡ ሳይቀር ፡ ሐዋርያ ፡ ደግሞ ፡ የሥጋ ፡ መናፈቅና ፡ መመኸት ፡ እንዲያው ፡ የኀጢአት ፡ ወገን ፡ እንዲሆን ፡ ያስታውቀናል ።

---

## ፲፡ ስለ ፡ አርነት ፡ ፈቃድ ።

የሰው ፡ ንብረት ፡ ከአደም ፡ ኀጢአት ፡ በኋላ ፡ እንደህ ፡ ነው ፡ በሰውነቱ ፡ ኃይል ፡ በበጎ ፡ ስራውም ፡ እንደይችል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ ነፍሱንም ፡ ለሃይማኖት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመጽሬት ፡ ያዘጋጀ ፡ ዘንድ ። ስለዚህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ በክርስቶስ ፡ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ በልባችን ፡ ሰርቶት ፡ ሳይቀድምልን ፡ ይህንንም ፡ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ካገኘነ ፡ በኋላ ፡ ሳይረደን ፡ ለኛ ፡ በጎን ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ስራ ፡ ለመስራት ፡ ኃይል ፡ የለነም ።

---

## ፲፩። ስለ ፡ ሰው ፡ መጸደቅ ።

እኛ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጻድቃን ፡ ሁነን ፡ እንቈጠራለን ፡ በሃይማኖት ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ጌታችን ፡ ስለ ፡ መድኃኒታችንም ፡ ስለ ፡ ምግባሩ ። ስለ ፡ ምግባራችንም ፡ ስለ ፡ ስራችንም ፡ አይደለም ። ይህችም ፡ ትምርት ፡ በሃይማኖት ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ መጸደቃችን ፡ ማጽናናት ፡ ይመላባታል ፡ ጳውሎስ ፡ እጅግ ፡ ጽፎ ፡ እንደገለጸው ፡ በመልእክቱ ፡ ወደ ፡ ሮሜ ፡ ሰዎች ።

---

## ፲፪፡ ስለ ፡ በጎ ፡ ስራ ።

በጎ ፡ ስራ ፡ የሃይማኖት ፡ ፍሬ ፡ ሁኖ ፡ መጸደቃችንንም ፡ ተከትሎ ፡ ኀጢአታችንን ፡ ይሽር ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ፍርድ ፡ ይታገሥ ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ። በክርስቶስ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ፡ እርሱም ፡ ይቀበለዋል ። እውነተኛውም ፡ ሕያውም ፡ ሃይማኖት ፡ ያለ ፡ በጎ ፡ ስ



ራ ፡ አይገኝም ፡ ይታወቅበታል ፡ እንጅ ፡ ዛፍ ፡ ሁለግዜ ፡ በፍሬው ፡ እንዲታወቅ ።

---

## ፲፫። ሰው ፡ ሳይጸደቅ ፡ ስለሚያደርገው ፡ ስራ ።

የክርስቶስን ፡ ጸጋ ፡ የመንፈሱንም ፡ መቀበል ፡ የሚቀደም ፡ ስራ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ አያሰኝም ። ከሃይማኖት ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አይነሣምና ፡ ሰውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ ለመቀበል ፡ አያዘጋጀውም ። እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈቃድም ፡ አልተሰራምና ፡ የኀጢአት ፡ ወገን ፡ እንኳ ፡ እንዲሆን ፡ አንጠራጠርም ።

---

## ፲፬፡ ስለ ፡ ትሩፋት ፡ ስራ ።

በሰው ፡ ፈቃድ ፡ የተሰራ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሕጉ ፡ ካዘዘው ፡ በቀር ፡ በላየውም ፡ በጎ ፡ ስራ ፡ የትሩፋትም ፡ ስራ ፡ የሚሉት ፡ እንደገኘ ፡ ብሎ ፡ የሚያስተምር ፡ ሰው ፡ ያለ ፡ ትዕቢትና ፡ ዐመፃ ፡ እንደህ ፡ ማስተማር ፡ አይችልም ። ማለቱ ፡ እንደህ ፡ ነውና ። ለሰው ፡ የሚገባውን ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ ያዘዘውን ፡ ብቻ ፡ አያደርግም ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሚገባው ፡ የሚበዛ ፡ ያደርጋል ፡ እንጅ ። ክርስቶስ ፡ ግን ፡ ይላል ። የታዘዛችሁበትን ፡ ሁሉ ፡ ብታደርጉ ። እኛ ፡ የማንጠቅም ፡ ባሮች ፡ ነን ፡ በሉ ።

---

## ፲፭፡ ክርስቶስ ፡ ብቻውን ፡ ያለ ፡ ኀጢአት ፡ ነበረ ።

ክርስቶስ ፡ በውነት ፡ በፍጥረታችን ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ እኛን ፡ የመሰለ ፡ ሆነ ፡ ከኀጢአት ፡ በቀር ። ከኀጢአት ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ በጣም ፡ ንጹሕ ፡ ነበረ ፡ በሥጋው ፡ በመንፈሱም ። እርሱ ፡ ያለ ፡ እድፍ ፡ የሚኖር ፡ በግ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ሰውነቱንም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ምሥዋዕት ፡ ሁኖ ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ በዚህም ፡ ምሥዋዕት ፡ ያለምን ፡ ኀጢአት ፡ ያስወግድ ፡ ዘንድ ፡ መጣ ። ኀጢአትም ፡ በርሱ ፡ አልነበረም ፡ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ እንደል ። እኛ ፡ ሁላችን ፡ ግን ፡ የቀረነ ፡ ጥምቀታችንና ፡ በክርስቶስ ፡ ሁለተኛ ፡ ልደታችን ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡

ቢብዙ : ነገር : እንበድላለን :: ኃጢአትም : የሌብነም : ብንል : ራሳችነን : እናስታለን : እውነትም : የሌብነም ::

---

**፲፯:: ከጥምቀት : በኋላ : ስለ : ሚደረግ : ኃጢአት ::**

ከጥምቀት : በኋላ : በሰው : ፈቃድ : የሚሰራ : የሞት : ኃጢአት : ሁሉ : በመንፈስ : ቅዱስ : ላይ : ወይስ : ስርየት : የማይገኝለት : አይደለም :: ስለዚህም : ከተጠመቁ : በኋላ : በኃጢአት : የሚወድቁ : ሁሉ : ከንስሓ : አይከለከሉ :: መንፈስ : ቅዱስን : ከተቀበልነ : በኋላ : እንኳ : እንችላለን : ከተሰጠነ : ጸጋ : እንርቅ : ዘንድ : በኃጢአትም : እንወድቅ : ዘንድ : በእግዚአብሔርም : ጸጋ : ተመልሰን : እንነሣ : ዘንድ : ሕይወታችነንም : የተሻለውን : እናደርገው : ዘንድ :: ስለዚህም : በምድራዊት : ሕይወታቸው : ኃጢአትን : ማድረግ : እንደይችላቸው : የሚሉ : ወይስ : በውነት : ንስሓ : የሚገቡትን : ከኃጢአት : ስርየት : ስፍራ : የሚከለክሉ : ትምህርታቸው : ትወገዛለች ::

---

**፲፰:: ስለ : እግዚአብሔር : ስለ : ድሮ : መለየቱና : መምረጹ ::**

ለሕይወት ፣ አስቀድሞ : መለየት : እርሱ : የእግዚአብሐር : የዘላለም : ፈቃዱ : ነው : ያለም : መሠረት : ሳይሠራ : ጽኑ : አድርጎ : የፈቀደበት : በተሰወረ : ምክሩ : ከሰው : ወገን : ሁሉ : በክርስቶስ : የመረጻቸውን : ሁሉን : ከመርገምና : ከፍርድ : ያድናቸው : ዘንድ :: ለምስጋናም : እንደ : ተሰራ : እቃ : በክርስቶስ : ወደ : ዘላለም : መድኃኒት : ያደርሳቸው : ዘንድ :: እንጊዴህ : እርሳቸው : እግዚአብሐር : እንዴህ : የከበረውን : ስጥወታውን : የሰጣቸው : እንደ : እግዚአብሐር : ፈቃድ : በጊዜው : በልባቸው : በመንፈሱ : ይጸራሉ :: እርሳቸውም : በጸጋው : መጽራቱን : ይከተላሉ :: እርሳቸውም : እንደ : ያው : ይጸደቃሉ :: እርሳቸውንም : እግዚአብሔር : የጸጋ : ልጆቹን : ያደርጋቸዋል :: እርሳቸውም : እንደ : አንደኛ : ልጁ : እንደ : የሱስ : ክርስቶስ : ምሳሌ : ይሆናሉ :: እርሳቸውም : በፍርሃቱ : በበጎ : ስራ : ይመላለሳሉ :: እርሳቸውም : በመጨረሻቸው : በእግዚአብሔር : ምህረት : ወደ : ዘላለም : ደህንነት : ይደርሳሉ ::

መልካም : ማሰብ : ስለ : እግዚአብሔር : ስለ : ድሮ : መለየቱ : ስለ : መመረጻችንም : በክርስቶስ : የጻፈጠ : ያመረም : የማይናገርም : ማጽናናት : ይመላበታል : ለበጎ : ሰዎች : በልባቸው : የክርስቶስን : የመንፈሱን : መስራት : ለሚያውቁ : የሥጋቸውን : ስራ : ምድራዊን : ብልታቸውን : ገድሎ : ነፍሳቸውንም : ወደ : ላይ : ወደ : ሰማያዊ : ነገር : ወስደ :: ደች : ትምርት : ሃይማኖታቸውን : በዘላለም : መድኃኒታቸው : በክርስቶስ : የሚቀበሉ : እጅግ : ታቆማቸዋለች : ታጸናቸውማለች :: እግዚአብሔርንም : መውደዳቸውን : እጅግ : ታቃጥላለች :: በሥጋዊ : ሰዎች : ግን : የክርስቶስ : መንፈስ : በሌላቸው : የመሰናከል : ዕንቅፋት : ነው : ይህ : ፍርድ : የእግዚአብሔር : መለየት : በፊታቸው : ቢሆን :: ሰይጣን : ይህነን : መክንያት : ያደርግባቸዋል : ተስፋቸውን : እንዲጥሉ : ወይስ : እንዴህ : ከማድረጋቸው : ወደልተሻለ : ወደ : ርኩስ : አካሔዳቸው : ጥፋት : ይወስዳቸዋል ::

ደግሞም : የእግዚአብሐርን : ተስፋ : በቅዱስ : መጽሐፍ : እንደ : ተገለጸች : እንቀበለው : ዘንድ : ይገባናል : ባካሔዳችንም : ያነን : በቁም : ነገር : በእግዚአብሐር : ቃል : የተገለጸውን : የእግዚአብሐርን : ፈቃድ : እንከተል : ዘንድ ::

---

**፲፱፡ የዘላለም : መድኃኒት : በክርስቶስ : ስም : ብቻ : ትገኛለች ::**

ሰው : ሁሉ : በሚያምነው : በሚያስታውቀውም : ሕግ : ወይስ : መለየት : ያችን : ሕግ : የፍጥረትንም : ብርሃኑን : ብቻ : ቢከተል : ይድናል : የሚሉ : የርሳቸው : ትምርት : ርግምት : ሁና : ትቈጠር :: መጽሐፍ : ቅዱስ : የየሱስ : ክርስቶስን : ስም : ብቻ : ሰው : ሁሉ : ይድንበት : ዘንድ : ይገልጽልናልና ::

---

## ፲፱፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ::

የክርስቶስ ፡ የምትታይ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የሚያምኑ ፡ ሰዎች ፡ ጉባኤ ፡ ናት ፡ የእግዚአብሐር ፡ ጽሩ ፡ ቃል ፡ የሚሰበክባት :: ምሥጢራትንም ፡ እንደ፡ገባቸው ፡ የሚያገለግሉባት ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥርዓት ፡ እንደ፡ህ ፡ ወደ፡ለ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሚደርስ ::

የየሩሳሌም ፡ የስክንድርያም ፡ ያንጾኪያም ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ እንደ ፡ ሳቱ ፡ እንደ፡ህ ፡ የሮምም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሳተች ፡ በማምለካቸው ፡ ሥርዓት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ በሃይማኖት ፡ ትምህርታቸውም ፡ እንጂ ::

---

## ፳፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሥልጣን ::

ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሥልጣን ፡ አላተ ፡ የማምለክን ፡ ሥርዓት ፡ ትቍርጥ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ ነገርም ፡ ክርክር ፡ ቢሆን ፡ ታስቀምጠው ፡ ዘንድ :: ነገር ፡ ግን ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አይገባም ፡ በእግዚአብሐር ፡ በተጻፈ ፡ ቃሉ ፡ ላይ ፡ አንደኛን ፡ ታዝ ፡ ዘንድ ፡ ወይስ ፡ ምናቸውን ፡ የመጽሐፈ ፡ ቅዱስን ፡ ስፍራ ፡ እንደ፡ህ ፡ ለማስተርጐም ፡ ከሌላ ፡ ስፍራ ፡ ጋራ ፡ እንዲጻላ :: ስለዚህም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የመጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ ምስክርና ፡ ጠባቂ ፡ ሁና ፡ አንደኛን ፡ ላታዝ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የሚጻላውን :: ሰውንም ፡ ላትፈልግ ፡ ባንደች ፡ ያምን ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ መድኀኒቱ ፡ በግድ ፡ ይገባል ፡ ብላ ፡ ከመጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ በቀር ::

---

## ፳፩፡ ስለ ፡ ኦይኩሜኒኮች ፡ ሲኖዶች ::

ኦይኩሜኒኮችን ፡ ሲኖደች ፡ ያለ ፡ መኳንንት ፡ ፈቃድና ፡ ትእዛዝ ፡ መሰብሰብ ፡ አይገባም :: ተሰብስበውም ፡ ይስቱ ፡ ዘንድ ፡ ይችላሉ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በውነት ፡ ሳቱ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሐር ፡ እንኳ ፡ በተቈረጠ ፡ ነገር :: የተሰበሰቡ ፡ እርሳቸው ፡ ሰዎች ፡ ናቸውና ፡ ሁላቸውም ፡ ኢያንዳንደቸው ፡ ለእግዚአብሐር ፡ መንፈስና ፡ ለቃሉ ፡ አይገዙም :: ስለዚህም ፡ እርሳቸው ፡ ለመድኀኒታችን ፡ እንደ፡ገባ ፡ የሚያዙት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ኀይልና ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፡ ከመጽሐፈ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ባይገጥም ::

---



## ፳፪፡ ስለ ፡ አያሌ ፡ ነገር ፡ ሰው ፡ ያወጣው ፡ ከመጽሐፈ ፡ ቅዱስም ፡ ጋራ ፡ የሚጻላ ::

የሮማውያን ፡ ትምህርት ፡ ስለ ፡ ነፍስ ፡ ንብረት ፡ ከሞት ፡ በኋላ :: ስለ ፡ ኀጢአት ፡ ስርየት ፡ በከንቱ ፡ ስራ ፡ በብርም :: ስለ ፡ ሥእልም :: ከክርስቶስና ፡ ከቅዱሳንም ፡ ስለ ፡ ተረፈ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ አፅንት ፡ ልብስም ፡ እንጨትም ፡ መሬትም ፡ ስለ ፡ መሰገደቸውም ፡ ስለ ፡ መጸራታቸውም ፡ ወደ ፡ ቅዱሳንም ፡ ስለ ፡ መጽሬት :: ይህ ፡ ሁሉ ፡ ከሰው ፡ ልብ ፡ ብቻ ፡ ተነሣ :: በእግዚአብሐር ፡ ቃልም ፡ አልተመሠረተም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይጻላል ፡ እንጂ ::

---

## ፳፫፡ በጉባኤ ፡ ስለ ፡ ማገልገል ::

ለሰው ፡ ሁሉ ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ይሰብክ ፡ ዘንድ ፡ ምሥጢራትንም ፡ ያገለግል ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ፡ ለዚህ ፡ ማገልገል ፡ ካልተጸራ ፡ ካልተላከም :: እልያንም ፡ ብቻ ፡ በሥርዓት ፡ እንደ ፡ ተጸሩ ፡ እንደ ፡ ተላኩም ፡ እንቍጥራለን ፡ ለዚህ ፡ ማገልገል ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ሰራተኞችን ፡ ወደ ፡ ጌታችን ፡ ወይን ፡ ይጸሩ ፡ ዘንድ ፡ ይሰዱም ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ ከተቀበሉ ፡ ሰዎች ፡ የተመረጹ ፡ የተጸሩም ::

---

## ፳፬፡ ቄስ ፡ በጉባኤ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሚሰማው ፡ ቋንቋ ፡ ይናገር ::

ቄስ ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ቢጸልይ ፡ ምሥጢራትንም ፡ ቢያገለግል ፡ ጉባኤ ፡ በማይሰማው ፡ ቋንቋ ፡ ተናግሮ ፡ ይህ ፡ ከእግዚአብሐር ፡ ቃል ፡ ከመጀመርያም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወግ ፡ ጋራ ፡ ይጻላል ::

---

### ፷፭፡ ስለ ፡ ምሥጢራት ።

በክርስቶስ ፡ የተሰራ ፡ ምሥጢራት ፡ እርሳቸው ፡ ክርስቲያን ፡ ሰዎች ፡ የሚታወቁባቸው ፡ ምልክቶች ፡ ብቻ ፡ አይደሉም ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ስለ ፡ ፍቅሩም ፡ ወደኛ ፡ እውነተኞት ፡ ምስክሮች ፡ ኀይለኞችም ፡ ምልክቶች ፡ ናቸው ። እግዚአብሔር ፡ በርሳቸው ፡ በማይታይ ፡ መንገድ ፡ በልባችን ፡ ሰርትዋልና ። በርሱም ፡ ያለ ፡ ሃይማኖታችንን ፡ ሕያውን ፡ ያደርግባቸዋል ፡ ያጸናባቸውማል ።

ክርስቶስም ፡ ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ የሠራቸው ፡ ምሥጢራት ፡ ሁለት ፡ ናቸው ። እርሳቸውም ፡ ጥምቀትና ፡ የጌታ ፡ እራት ።

እልያ ፡ ፭ም ፡ ሮማውያን ፡ ደግሞ ፡ ምሥጢራት ፡ የሚልዋቸው ፡ እርሳቸውም ፡ የጥምቀት ፡ ማጽናት ። ንስሐም ፡ የቀሳውስትም ፡ እጅ ፡ መጫን ። መጋባትም ። ኋለኛ ፡ መቅባትም ፡ ሁሉ ፡ የወንጌል ፡ ምሥጢራት ፡ ሁነው ፡ አይቍጠሩ ። ከርሳቸው ፡ ተከፍለው ፡ የሐዋርያትን ፡ አካሔድ ፡ በነኵል ፡ ከመከተላቸው ፡ ተነሥተዋልና ፡ ተከፍለውም ፡ የሕይወት ፡ ንብረት ፡ ናቸው ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ያዘዘም ፡ ያላዘዘም ። ምሥጢራትን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ጥምቀትና ፡ የጌታችን ፡ እራት ፡ አይመስሉም ። የሚታይ ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ የተሰራ ፡ ምልክት ፡ ከማይታይ ፡ ጸጋው ፡ ጋራ ፡ የለባቸውምና ።

ምሥጢራትን ፡ እንደሚገባ ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥርዓት ፡ ብንቀበላቸው ፡ ብናገለግላቸውም ፡ ደባረኩልናል ። እንደይገባ ፡ ግን ፡ የሚቀበልዋቸው ፡ ለራሳቸው ፡ ኵነኔ ፡ ያደርጓቸዋል ፡ ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ እንዲል ።

---

### ፷፮፡ የቀሳውስት ፡ ክፋት ፡ የምሥጢርን ፡ ኀይል ፡ አይከለክልም ።

በምትታይ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በውነት ፡ ክፉ ፡ ሁልግዜ ፡ ከበጎ ፡ ጋራ ፡ ተደብልቆ ፡ ይገኛል ፡ ጊዜም ፡ አለ ፡ ለክፉ ፡ እጅግ ፡ ሥልጣን ፡ እንደለ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃልና ፡ ምሥጢራትንም ፡ በማገልገል ። ክፉ ፡ አገልጋዮች ፡ ግን ፡ በስማቸው ፡ አያገለግሉምና ፡ በክርስቶስ ፡ ስም ፡ እንጂ ፡ በትእዛዙም ፡ በሥልጣኑም ፡ ማገልገላቸውን ፡ መቀበል ፡ እንችላለን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ካፊቸው ፡ ብንሰማ ፡ ምሥጢራቱንም ፡ ከርሳቸው ፡ ስንቀበል ። የክርስቶስም ፡ የሥርዓቱ ፡ ኀይል ፡ ባገልጋዮቱ ፡ ዐመፃ ፡ አይሻርም ። የእግዚአብሔርም ፡ ስጥወታ ፡ አያንስም ፡ በሃይማኖትና ፡ በቅን ፡ ምሥጢራትን ፡ ከጃቸው ፡ በሚቀበሉ ። ለምሥጢር ፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥርዓትና ፡ ትእዛዝ ፡ ኀይል ፡ አለው ፡ በሰው ፡ ክፋት ፡ የማይጠፋ ።

ያስ ፡ ሳይቅር ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተግሣጽ ፡ ይገባል ፡ ስለ ፡ ክፎች ፡ አገልጋዮች ፡ ይመረምሩ ፡ ዘንድ ። እርሳቸውም ፡ መበደላቸውን ፡ በሚያውቁ ፡ ሰዎች ፡ ይከሰሱ ፡ ዘንድ ፡ መበደላቸውም ፡ እውነት ፡ ሁኖ ፡ በተገኘ ፡ ጊዜ ፡ በቅን ፡ ፍርድ ፡ ከሹመታቸው ፡ ይሻሩ ፡ ዘንድ ።

---

### ፷፯፡ ስለ ፡ ጥምቀት ።

ጥምቀት ፡ የሃይማኖት ፡ ማስታወቅ ፡ ክርስቲያንም ፡ ካልተጠመቀ ፡ ሰው ፡ የሚለይበት ፡ የመለየት ፡ ምልክት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ የሁለተኛ ፡ ልደታችንም ፡ ምልክት ፡ ነው ፡ እንጂ ። ጥምቀትን ፡ የሚቀበሉ ፡ በርሱ ፡ በምትታይ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይተከላሉ ። ለኀጢአትም ፡ ስርየት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልጅነታችን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የተሰጠች ፡ ትስፈ ፡ ላይን ፡ ትመለከትበታለች ፡ ታተማለችም ። ሃይማኖትም ፡ ይጸናበታል ። የእግዚአብሔርም ፡ ጸጋ ፡ በጸሎት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይበዛል ።

የሕፃናትን ፡ ጥምቀት ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንጠብቃለን ፡ ከክርስቶስ ፡ ሥርዓት ፡ ጋራ ፡ ይገጥማልና ።

---

### ፷፰፡ ስለ ፡ ጌታችን ፡ እራት ፡ ቍርባን ፡ የሚባል ።

የጌታችን ፡ እራት ፡ ክርስቲያን ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ሊሆንላቸው ፡ ለሚገባ ፡ ፍቅር ፡ ምልክት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ በክርስቶስ ፡ ሞት ፡ የሆነ ፡ የመድኀኒታችን ፡ ምሥጢር ፡ ነው ፡ እንጂ ። በቅንና ፡ በሃይማኖት ፡ እንደሚገባም ፡ ለሚቀ

በሉት ፡ የምንቈርሰው ፡ እንጀራ ፡ የክርስቶስ ፡ የሥጋው ፡ አንድነት ፡ ነው ፡ የበረከቱም ፡ ጽዋ ፡ የክርስቶስ ፡ የደሙ ፡ አንድነት ፡ ነው ::

የንጀራና ፡ የወይን ፡ ፀጅ ፡ ባሕሪ ፡ በጌታችን ፡ እራት ፡ እንደ ፡ ለወጥ ፡ ባሕርያቸው ፡ ተሽሮ ፡ የክርስቶስ ፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ እንዲሆኑ ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ አይገለጽም ፡ ይህችም ፡ ትምርት ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ከቁም ፡ ነገሬ ፡ ጋራ ፡ ትጸላለች :: ያምሥጢርንም ፡ ነገር ፡ ታጠፋለች :: ብዙም ፡ አሰተኛ ፡ ሃይማኖት ፡ ከርሱ ፡ ተነሣ ::

የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ በራቱ ፡ በሰማያዊ ፡ በመንፈሳዊም ፡ መንገድ ፡ ብቻ ፡ እንሰጣለን ፡ እንቀበለውማለን ፡ እንበላውማለን :: የክርስቶስንም ፡ ሥጋ ፡ በራቱ ፡ የምንቀበልበት ፡ የምንበላበትም ፡ መያዣ ፡ የነፍስ ፡ አፍ ፡ እርሱ ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ::

---

## ፳፱፡ ዐመፀኞች ፡ በጌታችን ፡ እራት ፡ የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ አይበሉም ::

ዐመፀኞች ፡ ሕያው ፡ ሃይማኖትም ፡ የሌላቸው ፡ የክርስቶስ ፡ የሥጋውንና ፡ የደሙን ፡ ምሥጢር ፡ በሥጋና ፡ ለማየት ፡ ባፈቸው ፡ ሲቀበሉት ፡ ሲበሉትም ፡ ሲጠጡትም ፡ ቅዱስ ፡ አውጉስቲኑስ ፡ እንዳለ ፡ ክርስቶስን ፡ በውነት ፡ አይቀበሉትም :: የዚህ ፡ የከበረ ፡ ምሥጢር ፡ መብልና ፡ መጠጥ ፡ ለኩነኔያቸው ፡ ይሆንባቸዋል ፡ እንጂ ::

---

## ፴፡ ስለ ፡ ሁለት ፡ መልኩ ::

የጌታው ፡ ጽዋ ፡ ከሕዝብ ፡ መከለከል ፡ አይገባም :: በክርስቶስ ፡ ሥርዓትና ፡ ትእዛዝ ፡ ቀሳውስት ፡ ታዘዋልና ፡ የጌታውን ፡ የራቱን ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ እርሳቸውም ፡ የጌታው ፡ እንጀራና ፡ ጽዋው ፡ ለክርስቲያን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ::

---

## ፴፩፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ በመስቀል ፡ ስለ ፡ ተፈጸመ ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ምሥዋዕቱ ::



እርሱ ፡ የክርስቶስ ፡ ምሥዋዕት ፡ በመስቀል ፡ ላይ ፡ ሁኖ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ የፈጸመው ፡ እርሱ ፡ ፍጹም ፡ ማደን ፡ ማስታረቅም ፡ካሳም ፡ ሆነ ፡ ስለ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሚወለድበት ፡ ስለ ፡ ሚያደርገውም :: ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ ሌላ ፡ ካሳ ፡ የለም ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ::

ስለዚህም ፡ የቍርባን ፡ ምሥዋዕት ፡ ሮማውያን ፡ ስለሚናገሩ ፡ ቄስ ፡ በርሱ ፡ ክርስቶስን ፡ ምሥዋዕት ፡ ሁኖ ፡ እንዲያቀርብበት ፡ ስለ ፡ ሕያዋንና ፡ ስለ ፡ ሙታን ፡ ኃጢአታቸውና ፡ መቅሠፍታቸው ፡ ይፈታላቸው ፡ ዘንድ ፡ ብለው ፡ ስድብና ፡ አሰት ፡ ነበረ ::

---

## ፴፪፡ ስለ ፡ ቀሳውስት ፡ መጋባት ::

ጳጳሳት ፡ ቀሳውስትም ፡ ዲያቆናትም ፡ በብችኑት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ወይስ ፡ ስለቱን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ወይስ ፡ ከመጋባት ፡ ይከለከሉ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ አልታዘዙም :: ስለዚህ ፡ እርሳቸው ፡ ቢወዱ ፡ እንደ ፡ ሌሎች ፡ ክርስቲያኖች ፡ ለመጋባት ፡ ይገቡ ፡ ለበጎ ፡ አካሔዳቸው ፡ እንዲጠቅም ፡ ቢመስላቸው ::

---

## ፴፫፡ ስለ ፡ ተገዘቱ ፡ ሰዎች ::

በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በግልጽ ፡ በቅን ፡ ፍርድዋ ፡ በሥርዓትም ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አንድነት ፡ የተቈረጠውን ፡ የተገዘተውንም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የምእምናን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ አረማዊ ፡ እንደ ፡ አጣሪም ፡ ይቍጠሩት ፡ ንስሓ ፡ በመግባት ፡ በግልጽ ፡ እስኪታረቅ ፡ ድረስ ፡ ሥልጣንም ፡ ባለው ፡ ፈራጅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መልሳ ፡ እስክትቀበለው ፡ ድረስ ::

---

## ፴፬፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሥርዓት ::

የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የማምለክዋ ፡ ሥርዓት ፡ በስፍራ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በጣምም ፡ በሁሉ ፡ ይሰማማ ፡ ዘንድ ፡ በግድ ፡ አይፈለግም :: በዘመን ፡ ሁሉ ፡ ልዩ ፡

ልዩ ፡ ነበረና ። ምድርም ፡ ዘመንም ፡ የሰውም ፡ ልማድ ፡ እንደ ሊለዩ ፡ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ይለወጥ ፡ አንደኛ ፡ ባይሰራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ላይ ፡ የሚሆን ። ማንም ፡ በራሱ ፡ ፍርድ ፡ በማሰብና ፡ በፈቃዱ ፡ በግልጽም ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ የማይጻላውን ፡ ሥርዓት ፡ በሥልጣንም ፡ የተሰራውን ፡ የተቀበሉትንም ፡ የሚያፈርሰው ፡ በግልጽ ፡ ይገሠጽ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሥርዓት ፡ በድልዋልና ፡ የመኰንንም ፡ ሥልጣን ፡ ጐድትዋል ። የደከሙትንም ፡ የወንድሞቹን ፡ ልብ ፡ አሳዘነ ። ሌላ ፡ ሰው ፡ ከመከተሉ ፡ ይፈራ ፡ ዘንድ ።

በያገርም ፡ በየሕዝብም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሰው ፡ ብቻ ፡ የተሰራውን ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሥርዓት ፡ ትሰራ ፡ ትለውጥም ፡ ትሽርም ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ አላት ። ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለመስራት ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ።

---

## ፴፭፡ ስለ ፡ ስብከት ።

የስብከት ፡ ሁለተኛ ፡ መጽሐፍ ፡ አርእስቶቹን ፡ በታች ፡ የሰጠነ ፡ ደህና ፡ የሚገባም ፡ ስለ ፡ ዘመናችንም ፡ የሚፈልግ ፡ ትምህርት ፡ ይገኝበታል ። እንዲሁም ፡ በሐፄ ፡ ኤድዋርድ ፡ በስድስተኛ ፡ ዘመን ፡ የተሰጠ ፡ የስብከት ፡ መጀመርያ ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ እልያ ፡ ስብከቶች ፡ ባብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ አገልጋዮች ፡ ጨክነውና ፡ ደህና ፡ አሰምተው ፡ ያነብዋቸው ፡ ዘንድ ፡ ጉባኤዮች ፡ ሊያስተውልዋቸው ፡ እንፈርደለን ።

የስብከቶች ፡ አርእስት ።

፩፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ደህና ፡ አድርገው ፡ ስለ ፡ መርባት ።
፪፡ ለጣዖታት ፡ ከመስገድ ፡ ስለ ፡ መጠነቀቅ ።
፫፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናትን ፡ ስለ ፡ ማብጀትና ፡ ማንጸት ።
፬፡ ስለ ፡ በጎ ፡ ስራ ። በመጀመርያም ፡ ስለ ፡ ጾም ።
፭፡ በመሆልሆልና ፡ በስካር ፡ ላይ ።
፮፡ የልብስን ፡ ሽልም ፡ በማብዛት ፡ ላይ ።
፯፡ ስለ ፡ ጸሎት ።



፰፡ ስለ ፡ ጸሎት ፡ ስፍራና ፡ ጊዜ ።
፱፡ የጉባኤ ፡ ጸሎትና ፡ የምሥጢራት ፡ ማገልገል ፡ በታወቀች ፡ ቋንቋ ፡ ይሆን ፡ ዘንል ፡ እንደ ፡ ፈለግ ።
፲፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ማክበር ።
፲፩፡ ስለ ፡ መምጸወት ።
፲፪፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ልደት ።
፲፫፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ሕማማት ።
፲፬፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ትንሣኤ ።
፲፭፡ የክርስቶስ ፡ የሥጋውንና ፡ የደሙን ፡ ምሥጢር ፡ እንደሚገባ ፡ ስለ ፡ መቀበል ።
፲፮፡ ስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስጥወታ ።
፲፯፡ ሮጋትዮን ፡ ለሚባል ፡ ዘመን ።
፲፰፡ ስለ ፡ መጋባት ፡ ንብረት ።
፲፱፡ ስለ ፡ ንስሓ ።
፳፡ በሀኬት ፡ ላይ ።
፳፩፡ ባመፃ ፡ ላይ ።

---

## ፴፮፡ ስለ ፡ ኤጲስቆጶሳትና ፡ ስለ ፡ አገልጋዮች ፡ ቅደሴ ።

ቀድሞ ፡ ባፄ ፡ ኤድዋርድ ፡ በስድስተኛ ፡ ዘመን ፡ የወጣ ፡ የጳርለመንትንም ፡ ሥልጣን ፡ ተቀብሎ ፡ የጸና ፡ የጳጳሳት ፡ የኤጲስቆጶሳትም ፡ የቀሳውስትና ፡ የዲያቆናትም ፡ የቅደስያቸው ፡ መጽሐፍ ፡ እንደዚህ ፡ ላለች ፡ ቅደሴና ፡ ሥርዓት ፡ የሚፈለግ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይገኝበታል ፡ እንዲያውም ፡ ያሰተኛ ፡ ሃይማኖት ፡ የማይገባም ፡ ነገር ፡ የለበትም ። ስለዚህም ፡ ከአፄ ፡ ኤድዋርደ ፡ ዘመን ፡ ከመንግሥታቸው ፡ ከሁለተኛ ፡ አመታቸው ፡ ወዲህ ፡ እንደዚያ ፡ መጽሐፍ ፡ ሥርዓት ፡ የተሾመና ፡ የተቀደሰ ፡ ከንጊዲህ ፡ ወዲህም ፡ እንደዚያች ፡ ሥርዓት ፡ የሚሾምና ፡ የሚቀደስ ፡ ሁሉ ፡ በቅን ፡ በሥርዓትም ፡ በሕግም ፡ እንደ ፡ ተቀደሰና ፡ እንደ ፡ ተሾመ ፡ ብለን ፡ እናዛለን ።

---

## ፴፯፡ ስለ ፡ አገር ፡ መኳንንት ።

ንግሥት ፡ እመቤታችን ፡ መጀመርያ ፡ ከሁሉም ፡ የሚበል

ጥ : ሥልጣን : አላት : በዚህ : በንግልጣር : ምድር : በሌላ : መግዛትዋም : ሁሉ :: የቤተ : ክርስቲያንም : ያገርም : መግዛት : ሁሉ : በነገር : ሁሉ : ለርስዋ : ነው :: በሌላ : አገርም ፤ ላለ : መኰንን : በዚህች : መንግሥት : ሥልጣን : የለውም :: በዚህ : ነገር : ግን : ለነገሥታታችን : አይገባም : የእግዚአብሔርን : ቃል : በቤተ : ክርስቲያን : ይሰብኩ : ዘንድ : ወይስ : ምሥጢራትን : ያገለግሉ : ዘንድ :: እንዲሁም : በኤልሳቤጥ : በንግሥታችን : ዘመን : ታዘዘ :: ይህች : ሥልጣን : አንድ : እግዚአብሔርን : የፈሩት : መኳንንት : ወትሮ : ከእግዚአብሔር : የተቀበሉት : መጽሐፈ : ቅዱስ : እንደሌ : መንግሥታቸውን : በየክፍልዋ : ከእግዚአብሔር : ዘንድ : እንደ : ታመኑባት :: ለመቅደስና : ላገር : ባለው : ይገዙ : ዘንድ : ዐመፀኞችንም : ክፉ : አድራጎችንም : ባገር : ሰይፍ : ይከለክሉ : ዘንድ ::

የሮም : ጳጳስም : በንግልጣር : መንግሥት : መግዛት : ወይስ : ሥልጣን : የለውም : ከቶ ::

የመንግሥት : ሕግ : ክርስቲያንን : ስለ : ታላቅ : መበደል : በሞት : መቅሠፍ : ይችላል ::

ለክርስቲያን : ይገባል : በመኰንን : ትእዛዝ : ጋሻ : ጦርን : ይወስድ : ዘንድ : በዘምቻም : ያገለግል : ዘንድ : የመንግሥት : ጉደይ : ሲፈልገው ::

---

## ፴፰፡ ስለ : ገንዘብ ::

የክርስቲያን : ሰው : ባለጠግነትና : ገንዘብ : ቅኑና : መግዛት : የጉባኤ : አይደለም : አያሌ : መናፈቃን : እንደ : ሐለሙ :: ይህ : ግን : ሳይቀር : ለሰው : ሁሉ : ይገባል : እግዚአብሔር : ከሰጠው : ገንዘብና : መግዛት : ለድኆች : ለበጎ : መክንያትም : ሁሉ : እንደ : ችሎቱ : ይሰጥ : ዘንድ ::

---

## ፴፱፡ ስለ : ክርስቲያን : ሰው : መሐላ ::

በከንቱ : ከሚደረግ : ከቃሊልም : መማል : ክርስቲያን : ሁሉ : ተከለከለ : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : በሐዋርያውም : በያዕቆብ : ቃል :: ነገር : ግን : የክርስቲያን : ሃይማኖት : ሰውን : ከመማል : ሁሉ : እንዲያው : አይከለክልም : መኰንን : ቢፈልገው : በሃይማኖትና : በፍቅርም : መክንያት : ነቢይ : እንዲያዘው : ቢሆን : በቅን : በፍርድም : በውነትም ::

---

ተጨረሱ : የእንግሊዝ : ቤት : ክርስቲያን : ፴፱፡ ቃላት ::

---

# የዝምድና፡ታቡላ፡

## እንደ፡መጽሐፍ፡ቅዱስ፡እንደ፡ሕጋችንም፡

## መጋባት፡የተከለከለባት።

---

ለወንድ፡ለመጋባት፡ተከለከለች።

፩፡ አያቲቱ፡
፪፡ ያያቱ፡ምሽት፡
፫፡ የምሽቱ፡አያቲቱ።
፬፡ ያባቱ፡እት፡
፭፡ የናቱ፡እት፡
፮፡ ያባቱ፡ወንድም፡ምሽት፡
፯፡ የናቱ፡ወንድም፡ምሽት፡
፰፡ የምሽቱ፡አባት፡እቱ፡
፱፡ የምሽቱ፡እናት፡እትዋ፡
፲፡ እናት፡
፲፩፡ ያባቱ፡ምሽት፡
፲፪፡ የምሽቱ፡እናት፡
፲፫፡ ልጂቱ፡
፲፬፡ የምሽቱ፡ልጅ፡
፲፭፡ የልጁ፡ምሽት፡
፲፮፡ እቱ፡
፲፯፡ የምሽቱ፡እት፡
፲፰፡ የወንድሙ፡ምሽት፡
፲፱፡ የልጁ፡ልጂቱ፡
፳፡ የሴት፡ልጁ፡ልጅ፡
፳፩፡ የልጅ፡ልጁ፡ምሽት፡
፳፪፡ የሴት፡ልጁ፡የልጅዋ፡ምሽት፡
፳፫፡ የምሽቱ፡የወንድ፡ልጅዋ፡ልጅ፡
፳፬፡ የምሽቱ፡የሴት፡ልጅዋ፡ልጅ፡
፳፭፡ የወንድሙ፡ልጅ፡
፳፮፡ የቱ፡ልጅ፡
፳፯፡ የወንድሙ፡ልጅ፡ምሽቱ፡
፳፰፡ የቱ፡ልጅ፡ምሽቱ፡
፳፱፡ የምሽቱ፡ወንድም፡ልጅቱ፡
፴፡ የምሽቱ፡እት፡ልጅዋ።

ለሴት፡ለመጋባት፡ተከለከለ፡

፩፡ አያትዋ፡
፪፡ ያያትዋ፡ባል፡
፫፡ የባልዋ፡አያት፡
፬፡ ያባትዋ፡ወንድም፡
፭፡ የናትዋ፡ወንድም፡
፮፡ ያባትዋ፡እት፡ባልዋ፡
፯፡ የናትዋ፡እት፡ባልዋ፡
፰፡ የባልዋ፡አባት፡ወንድሙ፡
፱፡ የባልዋ፡እናት፡ወንድም፡
፲፡ አባትዋ፡
፲፩፡ የናትዋ፡ባል፡
፲፪፡ የባልዋ፡አባት፡
፲፫፡ ልጅዋ፡
፲፬፡ የባልዋ፡ልጅ፡
፲፭፡ የልጅዋ፡ባል፡
፲፮፡ ወንድምዋ፡
፲፯፡ የባልዋ፡ወንድም፡
፲፰፡ የትዋ፡ባል፡
፲፱፡ የወንድ፡ልጅዋ፡ልጅ፡
፳፡ የሴት፡ልጅዋ፡ልጅ፡
፳፩፡ የወንድ፡ልጅዋ፡የልጁ፡ባል
፳፪፡ የሴት፡ልጅዋ፡የልጅዋ፡ባል
፳፫፡ የባልዋ፡ልጅ፡ልጁ፡
፳፬፡ የባልዋ፡የልጂቱ፡ባል፡
፳፭፡ የወንድምዋ፡ልጅ፡
፳፮፡ የትዋ፡ልጅ፡
፳፯፡ የወንድምዋ፡ልጅ፡ባልዋ፡
፳፰፡ የትዋ፡ልጅ፡ባልዋ፡
፳፱፡ የባልዋ፡ወንድም፡ልጁ፡
፴፡ የባልዋ፡እት፡ልጅዋ።

---

# የኤጲስቆጶሳት፡የቀሳውስትም፡የዲያቆናትም፡የቅደስያቸው፡ሥርዓት፡በእንግሊዝ፡ቤተ፡ክርስቲያን፡እንደሚቀደሱ።

## መቀደም።

መጽሐፍ፡ቅዱስንና፡የቀደሙትን፡አባቶች፡መጻሕፍት፡ደህና፡የሚያነቡት፡ሰዎች፡ከሐዋርያት፡ዘመን፡ጀምሮ፡በክርስቶስ፡ቤተ፡ክርስቲያን፡እሌህ፡ሶስት፡መዓርግ፡የኤጲስቆጶሳት፡የቀሳውስትም፡የዲያቆናትም፡መዓርግ፡እንደ፡ነበሩ፡አይጠራጠሩም። እሌህ፡መዓርግም፡ወትሮ፡የከበሩ፡ነበሩ፡ሰውም፡ያንዱን፡መዓርግ፡ስራ፡ከማድረግ፡ተከለከለ፡በቀደም፡ካልተጸራ፡ካልተፈተነም፡ካልተመረመረም፡የሚፈለግለትም፡አገባብ፡ካልተገኘበት፡በጉባኤም፡ጸሎት፡በጅም፡መጫን፡ሥልጣንን፡ተቀብሎ፡ካልገባበት። ስለዚህም፡ይህች፡ሥርዓት፡በእንግሊዝ፡ቤተ፡ክርስቲያን፡ትኖር፡ዘንድ፡በክብርም፡ትደረግና፡ትረጋ፡ዘንድ፡ከቶ፡ሰው፡በሕግ፡ኤጲስቆጶስ፡ወይስ፡ቄስ፡ወይስ፡ዲያቆን፡በንግሊዝ፡ቤተ፡ክርስቲያን፡ሁኖ፡አይቈጠር፡የሌሀ፡መዓርግንም፡ስራ፡አያድርግ፡ከዚህ፡እንደሚከተል፡ሥርዓት፡ካልተጸራ፡ካልተፈተነም፡ካልተመረመረም፡ካልገባበትም፡በቀደም፡የኤጲስቆጶስን፡ቅደሴ፡ተቀብሎ፡ቢሆን፡እንጅ።

ማንም፡ዲቁናን፡አይግባ፡ዕድሜው፡ሀያ፡ሶስት፡አመት፡ሳይሆን፡የውቀትን፡መዓርግ፡ያገኘ፡እንጅ። ወደቅስናም፡የሚገባ፡ዕድሜው፡ከሀያ፡አራት፡አመት፡አይጉደል። ለጳጳስናም፡ይቀደስ፡ዘንድ፡የሚሻ፡ሁሉ፡ሠላሳ፡አመት፡የፈጸመ፡ይሁን።

ኤጲስቆጶስም፡ወይስ፡እንዲያው፡ወይስ፡በደህና፡ምስክር፡ማንንም፡አካሔዱ፡ደህና፡ያለ፡ነወርም፡እንደሆን፡በፈተናም፡በምርምርም፡በላቲና፡ቋንቋ፡አዋቂ፡በመጽሐፍ፡ቅዱስም፡የጸና፡ሰው፡ሁኖ፡ቢያገኘው፡

በቃናና ፡ በተቈረጠ ፡ ጊዜ ፡ ወይስ ፡ ጉዳዩ ፡ ቢነዘንዘው ፡ በሌላ ፡ እሁድ ፡ ወይስ ፡ በዓል ፡ በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ከዚህ ፡ በምትከተል ፡ ሥርዓት ፡ ለዲቁና ፡ ያግባው ።

---

## የዲቁና ፡ ቅዳሴ ፡ ሥርዓት ።

* ኤጲስቆጶስ ፡ ለቅዳሴ ፡ ባደረገ ፡ ቀን ፡ ከጽዋት ፡ ጸሎት ፡ በኋላ ፡ ስብከት ፡ ትከተል ፡ የዲቁናውን ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ የዚች ፡ ሥርዓትም ፡ አገባብ ፡ በክርስቶስ ፡ ማኅበር ፡ የሚገለጽባት ፡ ጉባኤንም ፡ የተሾሙላትን ፡ ሰዎች ፡ ደህና ፡ አድርገው ፡ እንዲያከብሩ ፡ የምትመክራቸው ።

በመጀመርያም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በወንበሩ ፡ በጌታ ፡ ሳድቃ ፡ አጠገብ ፡ ተቀምጦ ፡ የዲያቆናት ፡ አለቃ ፡ ወይስ ፡ መድኅኑ ፡ ለዲቁና ፡ ደገቡ ፡ ዘንድ ፡ የሚሹትን ፡ ሰዎች ፡ (ሁላቸውም ፡ የሚገባውን ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡) ያድርስለት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ።

በእግዚአብሔር ፡ የከበሩ ፡ አባቴ ፡ እሌህን ፡ ሰዎች ፡ አደርስለዋለሁ ፡ ለዲቁና ፡ ለመግባት ።

### ኤጲስቆጶስ ።

ተጠንቀቁ ፡ የምታደርሱልን ፡ ሰዎች ፡ በውቃታቸውና ፡ በደህና ፡ አምልኳቸው ፡ ባካሒደቸውም ፡ የተበጁ ፡ የሚጨክኑም ፡ እንዲሆኑ ፡ ሹመታቸውን ፡ እንደሚገባቸው ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያኑም ፡ መሥሪት ።

የዲያቆናት ፡ አለቃም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይመልስ ።

ጠየቅሁባቸው ፡ ፈተንኋቸውም ፡ ደህናም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ይመስሉኛል ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለሕዝብ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።

ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ከላንተ ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ በማንም ፡



ከሌህ ፡ የዲቁናውን ፡ ሹመት ፡ ከሚሹት ፡ ሰዎች ፡ ክልካይን ፡ ወይስ ፡ የታወቀውን ፡ የሚከለክለውንም ፡ ኃጢአት ፡ የሚያውቅ ፡ እርሱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይምጣ ፡ ይህነንም ፡ ክልካይስ ፡ ኃጢአትስ ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ ያስይን ።

ታላቅ ፡ ኃጢአትም ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ የሚከለክል ፡ ነገር ፡ ቢገኝ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የተከሰሰውን ፡ ሰው ፡ አይቅደስ ፡ ከዚያ ፡ ኃጢአቱ ፡ ንጹሕ ፡ ሁና ፡ እስኪገኝ ፡ ድረስ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለዲቁና ፡ ደህና ፡ ሁነው ፡ ለተገኙት ፡ የጉባኤን ፡ ጸሎት ፡ ይለምንላቸው ፡ ከተሰበሰቡም ፡ ካህናትና ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ የሊጣኒያን ፡ ጸሎት ፡ ይጸልይ ፡ እንዲህ ።

### ሊጣኒያና ፡ ልመና ።

እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ወልድ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ ወልድ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ፡ ከአብና ፡ ከወልድ ፡ የምትወጣ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ፡ ከአብና ፡ ከወልድ ፡ የምትወጣ ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

ቅዱስ ፡ ቡሩክም ፡ ምስጉንም ፡ ሥላሴ ፡ ሆይ ። ሶስት ፡ አካላት ፡ አንድ ፡ አምላክም ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

ቅዱስ ፡ ቡሩክም ፡ ምስጉንም ፡ ሥላሴ ፡ ሆይ ። ሶስት ፡ አካላት ፡ አንድ ፡ አምላክም ። ማረን ፡ ችጋረኞችን ፡ ኃጢአተኞችንም ።

በደላችንን ፡ አታስብ ፡ አቤቱ ፡ ያባቶቻችንንም ፡ በደል ፡፡ ኃጢአታችንንም ፡ አትበቀል ፡፡ እዘንልን ፡ አቤቱ ፡፡ እጅግ ፡ በከበረ ፡ በደምህ ፡ ለተበጀሃት ፡ ሕዝብህ ፡ እዘን ፡፡ ለዘላለምም ፡ አትቊጣብን ፡፡

እዘንልን ፡ አቤቱ ፡፡

ከክፉት ፡ ከመጐደትም ፡ ሁሉ ፡፡ ከሰይጣንም ፡ ትንኰልና ፡ ከመፈተኑም ፡፡ ከቊጣህም ፡፡ ከዘላለምም ፡ ኲነኔ ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

ከልብ ፡ ዕውርነት ፡ ሁሉ ፡፡ ከትዕቢትም ፡፡ ክብርንም ፡ ከመመኘት ፡፡ ከግብዝነትም ፡፡ ከቅናትም ፡፡ ከጸላትነትም ፡ ከክፋትም ፡፡ ከፍቅርም ፡ መጐደል ፡ ሁሉ ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

ከዝሙት ፡ ከሌላም ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ከሚያደርስ ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡፡ ከዓለምም ፡ ከሥጋችንም ፡ ከዲያብሎስም ፡ ማሳት ፡ ሁሉ ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

በመብረቅና ፡ በዓውሎ ፡ ከሚመጣ ፡ መጐደት ፡፡ ከቸነፈርም ፡፡ ከራብም ፡፡ ከሰልፍም ፡፡ ከመገደልም ፡፡ ሳንዘጋጀም ፡ በድንገት ፡ ከሚመጣብን ፡ ሞት ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

ከሁከት ፡ ሁሉ ፡፡ በበጎ ፡ ሥርዓትም ፡ ላይ ፡ በስውር ፡ ከሚደረግ ፡ መባበር ፡፡ ከሽፍጥም ፡ ሁሉ ፡፡ ካሰትም ፡ ትምህርት ፡፡ ከንፉቄም ፡፡ ከመለየትም ፡፡ ከልብም ፡ ድንዛዜ ፡፡ ቃልህንም ፡ ትእዛዛትህንም ፡ ከመናቅ ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

በተቀደሰ ፡ ሥጋ ፡ መልበስህ ፡፡ በተቀደሰችም ፡ ልደትህ ፡ በመገዘርህም ፡፡ በመጠመቅህም ፡፡ በመጾምህም ፡፡ በመፈተንህም ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

በመጋደልህ ፡፡ ደምም ፡ በመሰለ ፡ ወዝህ ፡፡ በመሰቀልህም ፡፡ በሕማማትህም ፡፡ በከበረ ፡ ሞትህም ፡፡ በመቀበርህ



ም ፡፡ በተመሰገነችም ፡ ትንሣኤህ ፡፡ በዕርገትህም ፡፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ መምጣት ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

በመከራችን ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡፡ በደኅንነታችንም ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡፡ በሞትም ፡ ሰዓት ፡፡ በፍርድም ፡ ቀን ፡

አድነን ፡ አቤቱ ፡፡

እኛ ፡ ኃጢአተኞች ፡ እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ እንድትወድም ፡ ቅድስትና ፡ ኩቶሊካዊት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያንህን ፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ ትመራት ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ በውነተኛ ፡ ሃይማኖት ፡ በቅን ፡ ማምለክህም ፡ በሕይወትዋም ፡ ጽድቅ ፡ በቅድስናም ፡ ባርያህን ፡ ቢክቶርያን ፡ እመቤታችንና ፡ ንግሥታችንን ፡ ታቀናት ፡ ዘንድ ፡ ታጸናትም ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቃትም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ልብዋን ፡ በሃይማኖትህ ፡ በፍርሃትህም ፡ በውድህም ፡ ትገዛ ፡ ዘንድ ፡ እርስዋ ፡ ሁለግዜ ፡ ባንተ ፡ እንድታምን ፡ ሁለግዜም ፡ ምስጋናህን ፡ ክብርህንም ፡ እንድትሻ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ትጠብቃት ፡ ዘንድ ፡፡ በጸላቶቹዋም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ድል ፡ ትሰጣት ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ኢቴጌ ፡ አድለይድን ፡ ገዢ ፡ አልበርትንም ፡ የዌልስንም ፡ ገዢ ፡ አልበርትን ፡፡ የንግሥትንም ፡ ዘመዶች ፡ ሁሉ ፡ ትባርካቸው ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቃቸውም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ ጳጳሳትን ፡ ቀሳውስትንም ፡ ዲያቆናትንም ፡ በቃልህ ፡ በውነተኛ ፡ ዕውቀቱ ፡ በማስተዋሉም ፡ ታበራቸው ፡ ዘንድ ፡፡ እርሳቸው ፡ በስብከታቸውና ፡ በሕይወታቸው ፡ ይገልጹት ፡ ዘንድ ፡ ያከብሩትም ፡ ዘንድ ፡፡

እንለምንሃለን ፡ ስማን ፡ አቤቱ ፡፡

እንድትወድ ፡ እሌህን ፡ ባሮችህ ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ዲያቆና

ት ፡ (ወይስ ፡ ቀሳውስት ፡) ሹመት ፡ መግባት ፡ የሚሹትን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህንም ፡ ታወርድላቸው ፡ ዘንድ ፡ መል እክታቸውን ፡ ደህና ፡ እንዲፈጽሙ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ መሥራት ፡ ለቅዱስ ፡ ስምህም ፡ ምስጋና ።

እንለምንሃለን ፡ ስምን ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ የንግሥትን ፡ ሊቃውንትና ፡ አካበሮችን ፡ ሁ ሉ ፡ ጸጋውን ፡ ጥበብንም ፡ ማስተዋልንም ፡ ታለብሳቸው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማና ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ሹማምትን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ትጠብቅም ፡ ዘንድ ። ቅንን ፡ ሊሰሩ ። እውነትንም ፡ ሊጠብቁ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ሕዝብህን ፡ ሁሉን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ትጠ ብቅም ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ላሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አንድነትን ፡ ዕርቅንም ፡ ፍቅርንም ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ የውድህን ፡ የፍርሃትህንም ፡ ልብ ፡ ትሰጠ ን ፡ ዘንድ ። በኃይላችንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ትእዛዛትህ ፡ እንኖ ር ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ለሕዝብህ ፡ ሁሉ ፡ የጸጋህን ፡ መጨመርያ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ቃልህን ፡ በየውሃት ፡ እንዲሰሙ ። በንጹሕ ፡ ፍቅርም ፡ እንዲቀበሉት ። የመንፈስንም ፡ ፍሬ ፡ እንዲያ ፈሩ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ የሳቱትን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እውነት ፡ መንገድ ፡ ትመልሳቸው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ የሚቆሙትን ፡ ታበርታቸው ፡ ዘንድ ። በል ባቸውም ፡ የደከሙትን ፡ ታጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ ትረዳቸውም ፡



ዘንድ ። የሚወድቁትንም ፡ ታስነሣቸው ፡ ዘንድ ። ሰይጣን ንም ፡ በመጨረሻ ፡ ከግሬችን ፡ በታች ፡ ትቀጠቅጠው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንደትወድ ፡ በፈተና ፡ በድንትም ፡ በመከራም ፡ ያሉት ን ፡ ሁሉ ፡ ትረዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ታጸናቸውም ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ በምድር ፡ ወይስ ፡ በባሕር ፡ የሚሔዱትን ፡ ሁሉ ፡ የጸነሱትንም ፡ ሴቶች ። የታመሙትንመ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ። ታናሾችንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ። በግዞ ትም ፡ የሚቀመጡትን ፡ ሁሉ ፡ ትምሬቸው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የሌላቸውን ፡ ልጆች ። ባ ልቴቶችንም ፡ ባሕታውያንንም ፡ ነዲያንንም ፡ ትጠብቃቸ ው ፡ ዘንድ ፡ ትመግባቸውም ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ሰውን ፡ ሁሉን ፡ ትምረው ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ ለጸላቶቻችን ፡ ላሳደጆቻችንም ፡ ለሰደቦቻ ችንም ፡ ትሰርይላቸው ፡ ዘንድ ። ልባቸውንም ፡ ትመልስ ፡ ዘንድ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ የምድርን ፡ ፍሬ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ። ለመቀበ ላችንም ፡ ትጠብቀው ፡ ዘንድ ። በየጊዜው ፡ እስክንበላው ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

እንድትወድ ፡ እውነተኛ ፡ ንስሓ ፡ መግባትን ፡ ትሰጠን ፡ ዘ ንድ ። ኃጢአታችንንም ፡ ሀኬታችንንም ፡ አለማወቃችንን ም ፡ ታስቀርልን ፡ ዘንድ ። የመንፈስ ፡ ቅዱስህንም ፡ ጸጋ ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ሕይወታችንን ፡ እንደ ፡ ቅዱስ ፡ ቃልህ ፡ እ ንድንለውጥ ።

እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ፡ አቤቱ ።

የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ሆይ ። እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ።

የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ እንለምንሃለን ፡ ስማኔ ።

የእግዚአብሔር ፡ በግ ፡ ሆይ ፡ ያለምን ፡ ኃጢአት ፡ ያስወግድሀው ፡፡

ሰላምህን ፡ ስጠነ ፡፡

የእግዚአብሔር ፡ በግ ፡ ሆይ ፡ ያለምን ፡ ኃጢአት ፡ ያስወግድሀው ፡፡

ማረነ ፡፡

ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ስማነ ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ስማነ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረነ ፡፡
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ማረነ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡
አቤቱ ፡ ማረነ ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁላቸው ፡ የጌታችነን ፡ ጸሎት ፡ ባንድ ፡ ይጸልዩ ፡፡

አባታችን ፡ ሆይ ፡ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡፡ ስምህ ፡ ይቀደስ ፡፡ መንግሥትህ ፡ ትምጻ ፡፡ ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ትሁን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በሰማይ ፡፡ እንጀራችነን ፡ የሚበቃነን ፡ ስጠነ ፡ ዛሬ ፡፡ ይቅር ፡ በለነ ፡ በኛ ፡ ያለውን ፡፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይቅር ፡ እንደምንል ፡ ልኛ ፡ የለባቸውን ፡፡ ወደ ፡ ፈተናም ፡ አታግባን ፡፡ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጅ ፡ አሜን ፡፡

ቁስ ፡፡ እንደ ፡ ኃጢአታችን ፡ በኛ ፡ አትስራ ፡ አቤቱ ፡፡
ም ፡፡ እንደ ፡ በደላችንም ፡ አትክፈልልን ፡፡

እንጸልይ ፡፡

እግዚአብሔር ፡ መሐሪ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ የተደቀሰውን ፡ ልብ ፡ ልመና ፡ የሚያዝኑትንም ፡ መሻት ፡ አትንቅምና ፡፡ በመከራችንና ፡ በጭንቀታችን ፡ ጊዜ ፡ በፊትህ ፡ በምናደርገው ፡ በጸሎታችን ፡ እርደነ ፡፡ በጸጋም ፡ ስማነ ፡፡ የሰይጣን ፡ ወይስ ፡ የሰው ፡ ብልሐትና ፡ ትንኰል ፡ የሚሰሩብን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይሻር ፡ ዘንድ ፡፡ በቸርነትህም ፡ መጠበቅ ፡ ይበትን ፡ ዘንድ ፡፡ እኛም ፡ ባሮችህ ፡ መሰደድ ፡ ሳይጉዳነ ፡ በቅድስ



ት ፡ ቤት ፡ ክርስቲያንህ ፡ እናመሰግንህ ፡ ዘንድ ፡ ሁልግዜ ፡፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡

ም ፡፡ አቤቱ ፡ ተነሣ ፡ እርደነም ፡ አድነንም ፡ ስለ ፡ ስምህ ፡ መክንያት ፡፡
ቁ ፡፡ አቤቱ ፡ በጆሮቻችን ፡ ሰማነ ፡፡ አባቶቻችንም ፡ ነገሩነ ፡፡ በዘመናቸው ፡ በድሮ ፡ ዘመንም ፡ የሰራሀውን ፡ የከበረውንም ፡ ስራ ፡፡
ም ፡፡ አቤቱ ፡ ተነሣ ፡ እርደነም ፡፡ ስለ ፡ ክብርህም ፡ አድነን ፡፡
ቁ ፡፡ መስጋና ፡ ይሁን ፡ የሚቀርም ፡፡
ም ፡፡ በመጀመርያ ፡ የሚቀርም ፡፡
ቁ ፡፡ ከጸላቶቻችን ፡ አድነን ፡ ክርስቶስ ፡፡
ም ፡፡ በጸጋ ፡ ወደ ፡ መከራችን ፡ ተመለከት ፡፡
ቁ ፡፡ በርኅራኄ ፡ የልባችነን ፡ ኣሳብ ፡ እይ ፡፡
ም ፡፡ የሕዝብህን ፡ ኃጢአት ፡ በምሕረትህ ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፡፡
ቁ ፡፡ በፍቅር ፡ በምህረትም ፡ ጸሎታችነን ፡ ስማ ፡፡
ም ፡፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ ማረነ ፡፡
ቁስ ፡፡ አሁንና ፡ ወትሮ ፡ ፈቀድ ፡ ትሰማን ፡ ዘንድ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡፡
ም ፡፡ በጸጋ ፡ ስማነ ፡ ክርስቶስ ፡፡ በጸጋ ፡ ስማነ ፡ ጌታ ፡ ክርስቶስ ፡፡
ቁስ ፡፡ አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ ትገለጽልን ፡፡
ም ፡፡ ባንተ ፡ እንደ ፡ አመነ ፡፡

ቁ ፡፡ እንጸልይ ፡፡

በትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ በምሕረት ፡ ወደ ፡ ድካማችን ፡ እንድታይ ፡፡ ስለ ፡ ስምህም ፡ ምስጋና ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ በቅን ፡ የሚገባነውን ፡ ከኛ ፡ አርቀው ፡፡ ጸጋም ፡ ስጠነ ፡ በመከራችን ፡ ሁሉ ፡ ማመናችነን ፡ ተስፋችነንም ፡ ሁሉ ፡ ምሕረትህን ፡ እናደርግ ፡ ዘንድ ፡፡ ሁልግዜም ፡ እንገዛልህ ፡ ዘንድ ፡ በቅድስና ፡ በሕይወትም ፡ ንጽሕና ፡ ለክብርህ ፡ ለምስጋናህም ፡፡ ባንድ ፡ መኻከለኛችን ፡

በጰራቅሊጦሳችንም ፡፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የቍርባን ፡ ሥርዓት ፡ ትከተል ፡ ከልመና ፡ ከመልእክት ፡ ክፍልም ፡ ከወንጌል ፡ ክፍልም ፡ ጋራ ፡ እንደዚህ ፡፡

ልመና ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ባምላካዊት ፡ ምክርህ ፡ ልዩ ፡ ልዩን ፡ ያገልጋዮችህን ፡ ሥርዓት ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ሠርተሃልና ፡ ለሐዋርያትህም ፡ መንፈስህን ፡ ሰጥተሃልና ፡ ለዲቁና ፡ ሥርዓት ፡ መጀመርያውን ፡ ሰማዕት ፡ ቅዱስ ፡ እስጢፋኖስን ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ ይመርጹ ፡ ዘንድ ፡፡ እሌህንም ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ዲቁና ፡ ሹመትና ፡ መልእክት ፡ የተጸሩትን ፡ ባሮችህ ፡ በምህረት ፡ እይ ፡ በትምህርትህም ፡ እውነት ፡ እንደዚህ ፡ ምላቸው ፡ በሕይወትም ፡ ንጽሕና ፡ አስጊጻቸው ፡ እርሳቸው ፡ በቃልና ፡ በበጎ ፡ ምሳሌ ፡ በዚህች ፡ ሹመት ፡ ታምነው ፡ እንዲያገለግሉህ ፡ ለስምህ ፡ ምስጋና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህም ፡ መሥራት ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ምግባር ፡፡ እርሱ ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ኑርዋልና ፡ ገዝቶማልና ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡
፩፡ ጢሞቴዎስ ፡ ፫፡ ፰፡፡

ዲያቆናትም ፡ ደግሞ ፡ የጸኑ ፡ ይሁኑ ፡፡ ባለ ፡ ሁለት ፡ ነገርም ፡ አይሁኑ ፡፡ እጅግ ፡ ጸጅ ፡ ወደ ፡ መጠጣትም ፡ አይዘንብሉ ፡፡ ርኩስ ፡ ትርፍም ፡ አይውደዱ ፡፡ የሃይማኖት ፡ ምሥጢር ፡ ይሁንላቸው ፡ እንጅ ፡ በንጹሕ ፡ ሕሊና ፡፡ እሌኽም ፡ አስቀድመው ፡ ይፈተኑ ፡፡ ከዚያ ፡ በኋላም ፡ ነውር ፡ ከሌለባቸው ፡ ያገልግሉ ፡፡ ሴቶችም ፡ ደግሞ ፡ የጸኑ ፡ ይሁኑ ፡፡ ሰደቦች ፡ ያይደሉ ፡፡ ለስካርና ፡ እጅግ ፡ ለመብላት ፡ ያልተሰጡ ፡፡ በሁሉም ፡ የታመኑ ፡፡ ዲያቆናትም ፡ ያንዲት ፡ ሴት ፡ ባሎች ፡ ይሁኑ ፡፡ የልጆቻቸውንና ፡ የቤታቸውን ፡ ሥርዓት ፡ ያሳምሩ ፡፡ መልካሙን ፡ ማገልገል ፡ የሚያገለግሉ ፡ መልካሙን ፡ መዓርግ ፡ ለራሳቸው ፡ ያደርጋሉና ፡ ብዙ ፡ ድፍረትንም ፡ በክርስቶስ ፡ የሱስ ፡ ሃይማኖት ፡፡



ወይስ ፡ ይህ ፡፡
የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፮፡ ፪፡፡

አሥራ ፡ ሁለቱም ፡ የደቀ ፡ መዛሙርትን ፡ ወገን ፡ ጸሩ ፡ አሉም ፡፡ እኛ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ትተን ፡ በማዕድ ፡ እናገለግል ፡ ዘንድ ፡ አይገባም ፡፡ አሁንም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ሰባት ፡ በጎች ፡ ከላንት ፡ ፈልጉ ፡ በመልካም ፡ የተመሰከረላቸው ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስና ፡ ጥበብም ፡ የመላባቸው ፡፡ ለዚኽም ፡ ጉዳይ ፡ እንሾማቸዋለን ፡፡ እኛ ፡ ግን ፡ ለጸሎት ፡ ነገሩንም ፡ ለማስተማር ፡ ልንጸመድ ፡፡ ነገሩም ፡ በጉባዔው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ተወደደ ፡፡ እስጢፋኖስንም ፡ መረጡ ፡፡ ሃይማኖት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ የመላበትን ፡ ሰው ፡፡ ፊልጶስንም ፡፡ አጵሮኮሮስንም ፡፡ ኒቃኖርንም ፡፡ ጢሞንንም ፡፡ ጰርሜናስንም ፡፡ ኒቆላዎስንም ፡ መጻተኛውን ፡ አገሩም ፡ አንጾኪያ ፡፡ በሐዋርያትም ፡ ፊት ፡ አቆምዋቸው ፡፡ በጸለዩም ፡ ጊዜ ፡ እጃቸውን ፡ ጫኑባቸው ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ነገር ፡ በዛ ፡፡ የደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ቍጥር ፡ በየሩሳሌም ፡ እጅግ ፡ በዛ ፡፡ እጅግ ፡ ሰዎችም ፡ ከካህናት ፡ ወገን ፡ ለሃይማኖት ፡ ተገዙ ፡፡

የወንጌል ፡ ክፍልም ፡ ሳይነበብ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በወንበሩ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ዲቁና ፡ የሚገቡትን ፡ ሁሉ ፡ ኢያንዳንዱን ፡ የንግሥትን ፡ አለቅነት ፡ መሐላ ፡ በንግዷ ፡ ሥልጣናት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያስምላቸው ፡፡ ኢያንዳንዳቸው ፡ እንደዚህ ፡ ሲል ፡፡

እኔ ፡ እምላለሁ ፡ ከልቤ ፡ እንድትሰቀኝ ፡ እንድጸላም ፡ እንድክድም ፡ ያች ፡ ርግምት ፡ ትምህርት ፡ እንደዚህ ፡ የምትል ፡ "በሮምያ ፡ ጳጳስ ፡ ወይስ ፡ በርሱ ፡ ወገን ፡ ሥልጣናት ፡ የተገዘቱ ፡ የተወገዙም ፡ ገዦች ፡ በሚገዙላቸው ፡ ሰዎች ፡ ወይስ ፡ በሌላ ፡ ሰው ፡ ቢሻሩ ፡ ቢገደሉም ፡ ይገባቸዋል" ፡፡ እንግዲም ፡ ሁሉ ፡ ገዢ ፡ ቢሆን ፡ ሰውም ፡ ቢሆን ፡

ጳጳስም ፡ ቢሆን ፡ መንግሥትስ ፡ ንጉሥስ ፡ በዚች ፡ መንግ ሥት ፡ ከቶ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ላይ ፡ ወይስ ፡ በሰው ፡ ነፍ ስ ፡ ላይ ፡ ፍርድ ፡ ኃይልም ፡ ብልጥም ፡ መቅደምም ፡ ሥል ጣንም ፡ እንደለው ፡ እክደለሁ ፡ እግዚአሔርም፤ ደርደኝ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የሚቀደሱትን ፡ ሁ ሉ ፡ በግልጽ ፡ በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ይመርመር ፡ እንዴ ህ ፡ ሲል ።

እላንት ፡ ይህችን ፡ ሹመትና ፡ መልእክት ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ለክብሩ ፡ መዝረጋትና ፡ ለቤተ ፡ ክርስ ቲያኑ ፡ ለመሥሪት ፡ ትገዙ ፡ ዘንድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በው ሥጣችሁ ፡ እንደ ፡ አነቃችሁን ፡ ይመስላችኋል ።

ምላሽ ። ይመስለኛል ።

ኤጲስቆጶስ ።

በውነት ፡ እንደ ፡ ጌታችን ፡ እንደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ፈ ቃድ ፡ እንደዚች ፡ መንግሥትም ፡ ሥርዓት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክር ስቲያን ፡ መልእክት ፡ ተጸሬነ ፡ ትላላችሁን ።

ም ። እላለሁ ።

ኤጲስቆጶስ ።

የብሉይና ፡ ያዲስ ፡ ኪዳን ፡ የቃናና ፡ መጻሕፍት ፡ በውነት ን ፡ ታምንዋቸዋላችሁ ።

ም ። አምናቸዋለሁ ።

ኤጲስቆጶስ ።

ታገለግሉባት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ተጸራችሁባት ፡ ቤተ ፡ ክርስ ቲያን ፡ ለተሰበሰቡ ፡ ሕዝብን ፡ ጨክናችሁን ፡ ታነብዋቸው ፡ ዘንድ ፡ ትፈቅዳላችሁ ።

ም ፡ እፈቅዳለሁ ።

ኤጲስቆጶስ ።

ወደ ፡ ዲቁና ፡ ሹመት ፡ ደህ ፡ ይገባል ። ዲያቆን ፡ ያገለግልባ ት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ተጸራባት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቄስን ፡ በ ማምለክ ፡ እንዲያግዝ ፡ ይልቁንም ፡ የጌታውን ፡ እራት ፡ በማገልገልና ፡ በመክፈፈሉ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስና ፡ ሆሚልያ



ንም ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንዲያነብ ፡ አሽከሮችንም ፡ በ ክቴኪስሞስ ፡ እንዲያስተምር ፡ ቄስም ፡ ቢታጣ ፡ ሕፃናት ን ፡ እንዲያጠምቅ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ ሥልጣን ፡ ቢሰጠው ፡ እንዲሰብክ ። ደግሞም ፡ ሥርዓቱ ፡ እንዴህ ፡ ወደ ፡ ተደረገ ችባት ፡ ለዲያቆን ፡ ይገባል ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ጉልት ፡ የ ተቀመጡትን ፡ ድውያን ፡ ድኆችንም ፡ ደካሞችንም ፡ እን ዲጠይቅ ፡ ንብረታቸውንም ፡ ስማቸውንም ፡ መኖርያቸው ንም ፡ ለቄሱ ፡ እንዲያመለክትለት ፡ እልያ ፡ በምክሩ ፡ በጉ ልተኞች ፡ ወይስ ፡ በሌሎች ፡ ምጽዋት ፡ ይደገፉ ፡ ዘንድ ። ይ ህነን ፡ በደስታና ፡ በሸታ ፡ ለማድረግ ፡ ትፈቅዳላችሁን ።

ም ። እፈቅዳለሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዴት ።

ኤጲስቆጶስ ።

በኃይላችሁን ፡ ሁሉ ፡ ትጋደላላችሁ ፡ ሕይወታችሁን ፡ የቤ ተ ፡ ሰቦቻችሁንም ፡ ሕይወት ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ትምህርት ፡ ታቀኑ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ችሎታችሁም ፡ በየስፍራችሁ ፡ ራሳ ችሁንና ፡ እርሳቸውን ፡ ለክርስቶስ ፡ መንጋ ፡ ደህና ፡ ምሳሎ ች ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ።

ም ። እጋደላለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ረጅ ፡ ሁኖ ።

ኤጲስቆጶስ ።

በላያችሁም ፡ ለተሾመን ፡ ቄስ ፡ ለሌሎችም ፡ ለቤተ ፡ ክ ርስቲያን ፡ ታላቆች ፡ አገልጋዮች ፡ በላያችሁም ፡ ለተሾሙ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አከብራችሁ ፡ ትታዘዛላችሁን ፡ እሺና ፡ ደስ ብላችሁም ፡ ደህናውን ፡ ምክራቸውን ፡ ትከተላላችሁን ።

ም ። እግዚአብሔር ፡ ቢረደኝ ፡ አደርገዋለሁ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢያንዳንዳቸው ፡ ወደ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ይቅረብ ፡ በኤጲስቆጶስ ፡ ፊትም ፡ በ ጉልበቱ ፡ ይምበርከክ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ እጁን ፡ በየራሳቸው ፡ ላይ ፡ ይጫን ፡ እንደህም ፡ ይበል ።

ሥልጣንን ፡ ተቀበል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ፡ የዲያ ቆንን ፡ ሹመት ፡ ትፈጽም ፡ ዘንድ ፡ የተሰጠቸሀውን ፡ በአ ብ ፡ በወልድም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ። አሜን ።

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለያንዳንዳቸው ፡
ያደስ ፡ ኪዳንን ፡ መጽሐፍ ፡ ይስጥ ፡ እንዲህ ፡
ሲል ።

ሥልጣንን ፡ ተቀበል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ፡ ወንጌ
ልን ፡ ታነብ ፡ ዘንድ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ ቢያዝህ ፡ ትሰብክባ
ት ፡ ዘንድ ።

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ከርሳቸው ፡ አንድ ፡ ኤጲስቆጶ
ስ ፡ የፈቀደው ፡ ያንብብ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ሉቃስ ፡ ፲፪ ፡ ፴፭ ።

ወገባችሁ ፡ የታጠቀ ፡ ይሁን ። መብራታችሁም ፡ የበራ ።
እላንተም ፡ ጌታቸውን ፡ ከሰርግ ፡ እስኪመለስ ፡ የሚጠብቁ
ን ፡ ሰዎች ፡ መስላችሁ ። በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ደጅም ፡ በመታ ፡ ጊ
ዜ ፡ ቶሎ ፡ ይከፍቱለት ፡ ዘንድ ። ምስጋና ፡ ይገባቸዋል ፡ ለ
ለዚያ ፡ ባሮች ፡ ጌታቸው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ነቅተው ፡ የሚያ
ገኛቸው ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ። ወገቡን ፡ ታጥቆ ፡ እንዲ
ያስቀምጣቸው ። ተነሥቶም ፡ እንዲያገለግላቸው ። በሁለ
ተኛውም ፡ ሰዓት ፡ ቢመጣ ፡ በሦስተኛውም ፡ ሰዓት ፡ ቢመ
ጣ ፡ እንዲሁም ፡ ቢያገኛቸው ። እለዚያ ፡ ባሮች ፡ የተመሰ
ገኑ ፡ ናቸው ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የቍርባንን ፡ ቅዳ
ሴ ፡ ይፈጽም ፡ የተቀደሱም ፡ ይኑሩ ፡ ከኤጲስቆጶ
ስም ፡ ጋራ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ይቍረቡ ።
ቍርባንም ፡ ከተጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ከኋለኛ ፡ ልመና
ም ፡ በኋላ ፡ ከበረከትም ፡ በፊት ፡ እለዚህ ፡ ል
መናች ፡ ይከተሉ ።

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የበጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
ሰጭ ። አንተ ፡ በታላቅ ፡ ቸርነትህ ፡ እለዚህን ፡ ባሮችህ ፡ ለ
ዲቁና ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡ ፈቅደሃልና ፡
አድርጋቸው ፡ እንለምንሃለን ፡ አቤቱ ፡ በየሹመታቸው ፡ ገ
ሮች ፡ ትሑታንም ፡ ጽኑዓንም ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ መንፈሳዊት



ንም ፡ ሥርዓትና ፡ ተግሣጽ ፡ ሁሉ ፡ ለመጠበቅ ፡ እሽታ ፡ ይ
ሆንላቸው ፡ ዘንድ ፡ የበጎ ፡ ሕሊና ፡ ምስክር ፡ ወትሮ ፡ እን
ዲሆንላቸው ። እርሳቸውም ፡ በዚች ፡ ታችኛ ፡ መዓርግ ፡ ወ
ትሮ ፡ ጸንተውና ፡ በርትተው ፡ ሲኖሩ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡
ወደሚበልጡ ፡ ሹመቶች ፡ ለመጸሪት ፡ የታመኑ ፡ ሁነው ፡
ይገኙ ፡ ዘንድ ፡ በልጅህ ፡ በመድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስ
ቶስ ። ለርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ምስጋ
ናና ፡ ክብር ፡ ይሁን ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

በምናደርገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ቅደምን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ በምህረ
ትና ፡ በጸጋ ። በምትዘወትርም ፡ ረዲትህ ፡ ምራን ። በስራች
ን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ የምንጀምረው ፡ የምንጨምረውም ፡
የምንጨርሰውም ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናከብር ፡ ዘንድ ።
በመጨረሻም ፡ በምህረትህ ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እን
ቀበል ፡ ዘንድ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

ከአእምሮ ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰላም ።
ልባችሁንና ፡ መንፈሳችሁን ፡ ይጠብቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡
በልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በውቀቱና ፡ በ
ውዴ ። ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ የእግዚአብሔር ፡ የአብ ፡
የወልድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በረከት ፡ በመካከላች
ሁ ፡ ይሁን ። ከላንት ፡ ጋራም ፡ ይኑር ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

ለዲያቆንም ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ አመት ፡ በሹመቱ ፡ ሊኖ
ር ፡ ያስታውቁት ፡ ይህነን ፡ ዘመን ፡ ለመቍረጥ ፡ ደ
ህና ፡ መክንያት ፡ ባይገኝ ። እርሱ ፡ በቤተ ፡ ክርስ
ቲያን ፡ ወደ ፡ ማገልገል ፡ በሚገባ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
ይለምድና ፡ ይፈጸምበት ፡ ዘንድ ። ይህነንም ፡ በ
ማድረግ ፡ እሙንና ፡ ጨካኝ ፡ ሁኖ ፡ ቢገኝ ፡ በቃ
ኖና ፡ በተደረገ ፡ ወሬት ፡ ወይስ ፡ መክንያት ፡ ቢሆ
ን ፡ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ በእሁድ ፡ ወይስ ፡ በበዓል ፡ ኤ
ጲስቆጶስ ፡ ወደ ፡ ቅስና ፡ መዓርግ ፡ ያድርሰው ፡
በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ከዚህም ፡ በሚከተል ፡ ምሳሌ ።

## የቅስና ፡ ቅደሴ ፡ ሥርዓት ፡፡

*ኤጲስቆጶስ ፡ ለቅደሴ ፡ ባደረገ ፡ ቀን ፡ ከጽዋት ፡ ጸሎት ፡ በኋላ ፡ ስብከት ፡ ትከተል ፡ የቅስናውን ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ የዚኽ ፡ ሥርዓትም ፡ አገባብ ፡ በክርስቶስ ፡ ማኅበር ፡ የሚገለጽባት ፡ ጉባኤንም ፡ የተሾሙላትን ፡ ሰዎች ፡ ደህና ፡ አድርገው ፡ እንዲያከብሩ ፡ የምትመክራቸው ፡፡

በመጀመርያም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በወንበሩ ፡ በጌታ ፡ ሳድቃ ፡ አጠገብ ፡ ተቀምጦ ፡ የዲያቆናት ፡ አለቃ ፡ ወይስ ፡ መድኅኑ ፡ ለቅስና ፡ ደገኩ ፡ ዘንድ ፡ የሚሹትን ፡ ሰዎች ፡ (ሁላቸውም ፡ የሚገባውን ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡) ያድርስለት ፡ እንደዩህ ፡ ሲል ፡፡

በእግዚአብሔር ፡ የከበሩ ፡ አባቴ ፡ እሌህን ፡ ሰዎች ፡ አደርስለዋለሁ ፡ ለቅስና ፡ ለመግባት ፡፡

ኤጴስቆጶስ ፡፡

ተጠንቀቁ ፡ የምታደርሱልን ፡ ሰዎች ፡ በውቃታቸውና ፡ በደህና ፡ አምልኳቸው ፡ ባካሔደቸውም ፡ የተበጁ ፡ የሚጨክኑም ፡ እንዲሆኑ ፡ ሹመታቸውን ፡ እንደሚገባቸው ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያኑም ፡ መሥራት ፡፡

የዲያቆናት ፡ አለቃም ፡ እንደዩህ ፡ ሲል ፡ ይመልስ ፡፡

ጠየቅሁባቸው ፡ ፈተንኋቸውም ፡ ደህናም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ይመስሉኛል ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሕዝብን ፡ ይንገር ፡ እንደዩህ ፡ ሲል ፡፡

ወደጆቼ ፡ ሆይ ፡፡ ዛሬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ወደ ፡ ተቀደሰች ፡ ወደ ፡ ቅስና ፡ ሹመት ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ፡ የምንሻቸው ፡ እለዚህ ፡ ናቸው ፡፡ ደህና ፡ አድርገን ፡ ከመረመርናቸው ፡ በኋላ ፡ አንደችን ፡ የሚከለክላቸውን ፡ ነገር ፡ አላገኘነባቸውም ፡ ለሹመታቸውና ፡ ለመልእክታቸው ፡ በሕግ ፡ እንደ ፡ ተጸፈ ፡ ለርስዋም ፡ በጅ ፡ የሚሉ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አገኘናቸው ፡ እንጅ ፡፡ ደሮ ፡ ገና ፡ ከላንት ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ በማንም ፡ ከርሳቸው ፡ የታወቀውን ፡ ኃጢአት ፡ ወይስ ፡ ሌላውን ፡ ነገር ፡ የሚያውቅ ፡ ወደዚኽ ፡ ቅድስት ፡ ሹመት ፡ ከመግባት ፡ የሚከለክለውን ፡ እርሱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይምጣ ፡ ይቸንም ፡ ኃጢአት ፡ ወይስ ፡ ክልካይ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያስይኔ ፡፡



ታላቅ ፡ ኃጢአትም ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ የሚከለክል ፡ ነገር ፡ ቢገኝ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የተከሰሰውን ፡ ሰው ፡ አይቀድስ ፡ ከዚያ ፡ ኃጢአቱ ፡ ንጹሕ ፡ ሁኖ ፡ እስኪገኝ ፡ ድረስ ፡፡

ያዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለቅስና ፡ ደህና ፡ ሁነው ፡ የተገኙት ፡ ሰዎች ፡ የጉባኤን ፡ ጸሎት ፡ ደለምንላቸው ፡ ከተሰበሰቡም ፡ ካህናትና ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ ሊጣኒያን ፡ ይጸልይ ፡ በዲያቆናት ፡ ቅደሴም ፡ እንደለ ፡ ለቅስና ፡ በሚገባ ፡ ስፍራ ፡ እንጅ ፡ በርሱም ፡ "ዲያቆናት ፡" ቀርቶ ፡ "ቀሳውስት ፡" ይባል ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የቍርባን ፡ ሥርዓት ፡ ከልመና ፡ ከመልእክትም ፡ ከወንጌልም ፡ ክፍል ፡ ጋራ ፡ ትከተል ፡ እንደዩህ ፡፡

### ልመና ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የበጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰጭ ፡ አንተ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ ልዩን ፡ ልዩንም ፡ ሥርዓት ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አገልጋዮች ፡ አድርገሃልና ፡ እሌህን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ቅስና ፡ ሹመት ፡ የተጸሩትን ፡ ባሮችህ ፡ በምህረትህ ፡ እያቸው ፡ የውነትህንም ፡ ትምርት ፡ ምላባቸው ፡ በሕይወትም ፡ ንጽሕና ፡ አስጊጻቸው ፡ እርሳቸው ፡ በቃልና ፡ በበጎ ፡ ምሳሌ ፡ በዚኽ ፡ ሹመት ፡ ታምነው ፡ ደገዙልህ ፡ ዘንድ ፡ ለስምህ ፡ ምስጋና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህም ፡ መሥራት ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በመድኃኒታችን ፡ ምግባር ፡ እርሱም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ደኖራል ፡ ደገዛልም ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡ ኤፌሶን ፡ ፬፤ ፯፡፡

ለያንዳንዳችን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ስጦታ ፡ መጠን ፡ ጸጋ ፡ ተሰጠችን ፡፡ ስለዚኽም ፡ ተባለ ፡፡ ወደ ፡ ከፍታ ፡ ወጣ ፡ ምርኮንም ፡ ማረከ ፡፡ ለሰዎችም ፡ ስጦታ ፡ ሰጠ ፡፡ መውጣቱ ፡ ግን ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ምድር ፡ ስለ ፡ ወረደ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡፡ የወረደም ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ ከሰማያት ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ የወጣው ፡ ሁሉን ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱም ፡ ሰጠ ፡ ኢያሌን ፡ ሐዋርያት ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ አያሌንምም ፡ ነቢያት ፡፡ ሌሎችንም ፡ ሰባኮች ፡፡ ሌሎችንም ፡ ጠባቆች ፡ አስተማሮችም ፡፡ ቅዱሳን ፡ ለማገልገል ፡ ስራ ፡ ይበጁ ፡ ዘንድ ፡፡ የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ ለመሥራት ፡፡ ሁላችን ፡ ወደ ፡ ሃይማኖት ፡ አንድነት ፡ እስክንደርስ ፡ ድረስ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡፡ እስከ ፡ ፍጹም ፡ ጕልማስነት ፡ ድረስ ፡፡ እስከ ፡ ክርስቶስም ፡ እስከ ፡ ዕድሜው ፡ ፍጻሜ ፡ ልክ ፡ ድረስ ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ የወንጌል ፡ ክፍል ፡፡

ማቴዎስ ፡ ፱፤ ፴፯፡፡

ብዙ ፡ የተከማቹም ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አዘነላቸው ፡፡ ደክመው ፡ ነበሩና ፡ ቅብዝብዝም ፡ ብለው ፡ ነበሩና ፡ ጠባቂ ፡ እንደ ፡ ሌላቸው ፡ በጎች ፡፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ አላቸው ፡፡ መከሩ ፡ እጅግ ፡ ነው ፡ ሰራተኞች ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ናቸው ፡፡ እንኪያስ ፡ የመከሩን ፡ ባለ ፡ ቤት ፡ ለምኑት ፡ ሰራተኞችን ፡ ለመከሩ ፡ ያወፃ ፡ ዘንድ ፡፡

ወይስ ፡ ይህ ፡፡

ዮሐንስ ፡ ፲፤ ፩፡፡

እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ በደጅ ፡ ያልገባ ፡ ወደ ፡ በጎች ፡ በረት ፡ በሌላ ፡ ስፍራ ፡ የሚገባ ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ ሌባና ፡ ወንበዴ ፡ ነው ፡፡ በደጅ ፡ ግን ፡ የሚገባ ፡ እርሱ ፡ የበጎች ፡ ጠባቂ ፡ ነው ፡፡ ለርሱም ፡ በረኛው ፡ ይከፍታል ፡ በጎችም ፡ ቃሉን ፡ ይሰማሉ ፡፡ እርሱም ፡ የርሱን ፡ በጎች ፡ በየስማቸው ፡ ይጠራቸዋል ፡ ያወጣቸዋልም ፡፡ የርሱንም ፡ በጎች ፡ ሲያወጣ ፡ ጊዜ ፡ በፊታቸው ፡ ይሔዳል ፡፡ በጎችም ፡ ይከተሉታል ፡፡ ድምጹን ፡ ያውቃሉና ፡፡ ሌላውን ፡ ግን ፡ አይከተሉም ፡፡ ከርሱ ፡ ይሸሻሉ ፡ እንጂ ፡፡ የሌሎችን ፡ ድምጽ ፡ አያውቁምና ፡፡ ይህነን ፡ ምሳሌ ፡ አላቸው ፡ የሱስ ፡፡ እርሳቸው ፡ ግን ፡ የነገራቸውን ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላስተዋሉም ፡፡ የሱስም ፡ ደግሞ ፡ አላቸው ፡፡ እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡፡ እኔ ፡ የበጎች ፡ ደጅ ፡ ነኝ ፡፡ ከኔ ፡ በፊት ፡ የመጡ ፡ ሁሉ ፡ እርሳቸው ፡ ሌቦችና ፡ ወንበደች ፡ ናቸው ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ በጎች ፡ አልሰምዋቸውም ፡፡ ደጁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡፡ ማንም ፡ በኔ ፡ ቢገባ ፡ ይድናል ፡፡ ይገባልም ፡ ይወጣልም ፡ መሰማርያውንም ፡ ያገኛል ፡፡ ሌባው ፡ አይመጣም ፡ ሊሰርቅ ፡ እንጂ ፡ ሊገልም ፡ ሊያጠፋም ፡፡ እኔ ፡ መጣሁ ፡ ሕይወት ፡ ሊሆንላቸው ፡ እጅግ ፡ ጽጋብም ፡ እንዲሆንላቸው ፡፡ እኔ ፡ በጎ ፡ ጠባቂ ፡ ነኝ ፡፡ በጎ ፡ ጠባቂ ፡ ራሱን ፡ ስለ ፡ በጎቹ ፡ ይለውጣል ፡፡ ብንደኛ ፡ ግን ፡ ጠባቂም ፡ ያይደለ ፡ በጎቹም ፡ የርሱ ፡ ያይደሉ ፡፡ ተኵላ ፡ ሲመጣ ፡ ያያል ፡ በጎችንም ፡ ትቶ ፡ ይሸሻል ፡፡ ተኵላም ፡ ይነጥቃቸዋል ፡ በጎችንም ፡ ይበትናል ፡፡ ብንደኛ ፡ ግን ፡ ብንድኛ ፡ ነውና ፡ ይሸሻል ፡ ለበጎችም ፡ አያዝንም ፡፡ እኔ ፡ በጎ ፡ ጠባቂ ፡ ነኝ ፡፡ በጎቼንም ፡ አውቃለሁ ፡ በጎቼም ፡ ያውቁኛል ፡፡ አብ ፡ እኔን ፡ እንዲያውቀኝ ፡ እኔም ፡ አብን ፡ እንዳውቅ ፡፡ ራሴንም ፡ ስለ ፡ በጎች ፡ እለውጣለሁ ፡፡ ደግሞም ፡ ሌሎች ፡ በጎች ፡ አሉኝ ፡ ከዚኽ ፡ በረት ፡ ያይደሉ ፡፡ እርሳቸውንም ፡ አመጻቸው ፡ ዘንድ ፡ ጊዜ ፡ አለኝ ፡፡ ቃሌንም ፡ ይሰማሉ ፡፡ አንዲት ፡ መንጋም ፡ አንድ ፡ ጠባቂም ፡ ይሆናል ፡፡



የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በወንበሩ ፡ ተቀምጦ ፡ ኢያንዳንዳቸውን ፡ የንግሥትን ፡ አለቅነት ፡ መሐላ ፡ ያስምላቸው ፡ በዲቁና ፡ ቅዳሴ ፡ እንዳለ ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ እንደይህ ፡ ሲል ፡ ይንገራቸው ፡፡

እላንት ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ በቀደም ፡ ብቻችሁ ፡ በተመረመራችሁ ፡ ጊዜ ፡ አሁንም ፡ በተሰበከላችሁ ፡ ምክር ፡ ከወንጌልና ፡ ከመልእክትም ፡ ክፍል ፡ የተጸራችሁበትን ፡ ሹመት ፡ ታላቅነትና ፡ ክብርዋን ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደሌ ፡ ሰማ

ችሁ ። አሁንም ፡ ደግመን ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ የተጸራችሁለትን ፡ የሹመታችሁን ፡ ክብርና ፡ ባሕሪይ ፡ ታስቡ ፡ ዘንድ ፡ እንመክራችኋለን ። ሹመታችሁ ፡ ይህ ፡ ነውና ፡ መለክተኞች ፡ ጠባቆችም ፡ መጋቦችም ፡ ለጌታ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ታስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ ትመክሩም ፡ ዘንድ ፡ የጌታውንም ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ ትመግቡ ፡ ዘንድ ፡ በምድረ ፡ በደም ፡ የተበተኑትን ፡ የክርስቶስን ፡ በጎች ፡ በዚህም ፡ በክፉ ፡ በሚኖር ፡ ዓለም ፡ ያሉትን ፡ ልጆቹ ፡ ትፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ እርሳቸው ፡ ለዘላለም ፡ በክርስቶስ ፡ እንዲድኑ ።

ስለዚህም ፡ አደራ ፡ የተሰጣችሁት ፡ መዝገብ ፡ ታላቅነቱ ፡ ወትሮ ፡ ባሳባችሁ ፡ የተተከለ ፡ ይኑር ። እርሳቸው ፡ ክርስቶስ ፡ በሞቱ ፡ የተዋጃቸው ፡ ደሙንም ፡ ያፈሰሰላቸው ፡ በጎቹ ፡ ናቸውና ። እላንትም ፡ የምታገለግሉላት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ ጉባኤ ፡ የርሱ ፡ሙሽራ ፡ የርሱም ፡ ሥጋ ፡ ናትና ። ቢሆንም ፡ ያች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወይስ ፡ ማንም ፡ ብልትዋ ፡ ያለ ፡ ቸል ፡ በማለታችሁ ፡ ቢጉደ ፡ ቢቸገርም ፡ እላንት ፡ የበደልን ፡ ታላቅነት ፡ የመቅሠፍቱንም ፡ ክብድ ፡ ታውቃላችሁ ፡ የሚመጣባችሁትን ። ስለዚህም ፡ የሹመታችሁን ፡ ፍጻሜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ክርስቶስም ፡ ሙሽራና ፡ ሥጋ ፡ በነፍሳችሁ ፡ በጣም ፡ አስቡ ፡ ድካማችሁንም ፡ ትካዜያችሁንም ፡ መጨከናችሁንም ፡ ከቶ ፡ አታላሉ ፡ የታመናችሁባቸውን ፡ የምትታምኑባቸውንም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እውቀትና ፡ ሃይማኖት ፡ እንደህ ፡ ለመስማማት ፡ ወደ ፡ ዕድሜም ፡ ጉልማስነትና ፡ ፍጻሜ ፡ በክርስቶስ ፡ ለማድረሳቸው ፡ ለስሕተት ፡ ባምልኮ ፡ ለክፋትም ፡ በሕይወት ፡ በመኻከላችሁ ፡ ስፍራ ፡ እንዲያኖር ፡ በኃይላችሁ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ የሚገባችሁትንም ፡ ሁሉ ፡ እስክትፈጽሙ ፡ ድረስ ።

ሹመታችሁስ ፡ እንኪያ ፡ እንደህ ፡ ከብሬለችና ፡ እንደሁም ፡ ቸግሬለችና ፡ እንዴት ፡ እጅግ ፡ አሳብና ፡ ድካም ፡ ይገባችኋል ፡ እንደህ ፡ ወደለቸውን ፡ ታላቅ ፡ ክብር ፡ ከፍ ፡ ያደረጋችሁትን ፡ ጌታ ፡ ታመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ እላንትም ፡ እንደት ፡



ድሉ ፡ ለሌሎትም ፡ ለመበደል ፡ እንቅፋት ፡ እንደትሰጡ ፡ ትጠነቀቁ ፡ ዘንድ ። ደሮ ፡ እንደህ ፡ የለ ፡ ልቡና ፡ ከራሳችሁ ፡ የላችሁም ። ያች ፡ ፈቃድና ፡ ችሎት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ትሰጣለች ፡ እንጅ ። ስለዚህም ፡ ስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ከለልባችሁ ፡ ትጸልዩ ፡ ዘንድ ፡ ይገባችኋልና ፡ ያሻችኋል ። ወደ ፡ ሰውም ፡ መድኃኒት ፡ የሚያደርሰውን ፡ ታላቅ ፡ ስራችሁን ፡ በሌላ ፡ ነገር ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ በመነጨች ፡ ትምህርትና ፡ ምክር ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ በምትሰማማ ፡ ሕይወት ፡ እንጅ ፡ ትፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡ እንደይቻላችሁ ፡ ታያላችሁና ፡ እንደት ፡ እጅግ ፡ ልትጋደሉ ፡ ናችሁ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስን ፡ በማንበብ ፡ የላንትንና ፡ የሰዎቻችሁንም ፡ አካሔድ ፡ በመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ልክ ፡ በማቅናት ፡ ስለዚህም ፡ መክንያት ፡ ያለም ፡ አሳብና ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ችሎታችሁ ፡ ታሰነብቱ ፡ ዘንድ ፡ እንዲገባችሁ ።

እኛም ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በነፍሳችሁ ፡ ቀድሞ ፡ እንደሰባችሁ ፡ ልብንም ፡ እንደደረጋችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ለዚች ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደርስዋ ፡ ይጸራችሁ ፡ ዘንድ ፡ ለፈቀደ ፡ ሹመት ፡ ነፍሳችሁን ፡ በጣም ፡ ትሰጡ ፡ ዘንድ ፡ በመጠናችሁም ፡ በነፍሳችሁ ፡ ሁሉ ፡ በጣም ፡ ለዚች ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ትጣበቁ ፡ ዘንድ ፡ አሳባችሁንና ፡ ድካማችሁንም ፡ ሁሉ ፡ ወደርስዋ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ። እላንትም ፡ ወትሮ ፡ ባንድ ፡ መድኃኒታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መኻከለኝነት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ሰማያዊት ፡ ረዴት ፡ እንድትለምኑ ፡ እላንት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስን ፡ ደግማችሁና ፡ በልባችሁ ፡ ይዛዋችሁ ፡ በሹመታችሁ ፡ ታድጉ ፡ ዘንድ ፡ ትበስሉም ፡ ዘንድ ፡ ትበረቱም ፡ ዘንድ ፡ እላንትም ፡ እንደህ ፡ አድርጋችሁ ፡ ሕይወታችሁንና ፡ የሰዎቻችሁን ፡ ሕይወት ፡ ወትሮ ፡ ታቀኑ ፡ ዘንድ ፡ እንደሁም ፡ ለጉባኤ ፡ ደህና ፡ ምሳሎች ፡ ለመመሰል ፡ ትሆኑላቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ እናደርጋለን ።

አሁንም ፡ ከዚህ ፡ የተሰበሰበች ፡ የክርስቶስ ፡ ጉባኤ ፡ ደግማ ፡ ልባችሁንና ፡ ፈቃደችሁን ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ታስታውል ፡

ዘንድ : ስለታችሁም : ተግባራችሁን : ለመፈጸም : ያነቃችሁ : ዘንድ : እኛ : በእግዚአብሔርና : በቤተ : ክርስቲያኑ : ስም : ለምንጠይቃችሁት : ነገር : እላንት : በቁም : ነገር : ምላሽን : መልሱልን ::

እላንት : በልባችሁ : በውነት : በጌታችን : በየሱስ : ክርስቶስ : ፈቃድ : በዚችም : ለእንግልጣርና : ለኢርላንድ : ባለች : በተዋሐደች : ቤተ : ክርስቲያን : ሥርዓት : ወደ : ቅስና : ሹመትና : ሥርዓት : ተጸራነ : ትላለችሁን ::

ም :: እንደሆ : እላለሁ ::

ኤጲስቆጶስ ::

ለዘላለም : መድኀኒት : በሃይማኖት : በየሱስ : ክርስቶስ : በግድ : የሚሻ : ትምህርት : ሁሉ : በመጽሐፍ : ቅዱስ : በቀቶ : ደገኛል : ትላላችሁን : አደራም : የተሰጥዋችሁትን : ሕዝብ : በመጽሐፍ : ቅዱስ : እንድታስተምርዋቸው : ሌላ : ነገርንም : በግድ : ለዘላለም : መድኀኒት : ይፈለጋል : ብላችሁ : እንደታስተምሩ : ከመጽሐፍ : ቅዱስ : ይወጣልና : ይመሰከርለታል : ያምትሉት : እንጅ : ፈቃዳችሁ : ነውን ::

ም :: እንደሆ : እላለሁ : በእግዚአብሔርም : ጸጋ : ፈቃዴ : እንደሆ : ነው ::

ኤጲስቆጶስ ::

እንጊደህም : በክርስቶስ : ትምህርትና : በምሥጢራቱ : በተግሣጹም : እግዚአብሔር : እንደዘዘው : ይህችም : ቤተ : ክርስቲያንና : መንግሥት : እንደ : ተቀበለችው : እንደ : እግዚአብሔር : ትእዛዛት : ወትሮ : ታምናችሁን : ለማገልገል : ትጨክኑ : ዘንድ :: ለመጠበቃችሁም : አደራ : የተሰጣችኋተን : ሕዝብ : በኃይላቸው : ሁሉ : ትጠብቁት : ዘንድ : ማስተማራቸው : እንድትችሉ : ፈቃዳችሁን : ነው ::

ም :: በእግዚአብሔር : ረደት : እንደሆ : አደርጋለሁ ::

ኤጲስቆጶስ ::

ከእግዚአብሔር : ቃል : ጋራ : የሚጸላውን : የስሕተትን : ትምርት : ሁሉ : እንደ : ኃይላችሁ : ትከለክሉ : ዘንድ : ትሽረትም : ዘንድ : በግልጽና : በስውርም : ድውያንና : ባለ



ጤናዎችንም : በጉልታችሁ : ያሉትን : እንደ : ጉዳያቸው : እንደ : ጊዜም : ትመክርዋቸው : ዘንድ : የተዘጋጃችሁን : ትሆናላችሁ ::

ም :: እሆናለሁ : እግዚአብሔር : ቢረደኝ ::

ኤጲስቆጶስ ::

የዓለምንና : የሥጋውን : መማር : ትታችሁ : በጸሎትና : መጽሐፍ : ቅዱስን : በማንበብ : የርሱንም : ዕውቀት : በሚፈታው : መማር : ትቸኩላላችሁን ::

ም :: እቸኩልበት : ዘንድ : እጋደላለሁ : እግዚአብሔር : ረዳ : ቢሆን ::

ኤጲስቆጶስ ::

ነፍሳችሁንና : ቤቶቻችሁን : እንደ : ክርስቶስ : ትምርት : ታቀኑ : ዘንድ : ነፍሳችሁንና : እርሳቸውንም : እንደ : ኃይላችሁ : ለክርስቶስ : መንጋ : ደህና : ምሳሎች : ታደርጉ : ዘንድ : ትጋደላላችሁን ::

ም :: እግዚአብሔር : ቢረደኝ : እጋደልበታለሁ ::

ኤጲስቆጶስ ::

በክርስቲያን : ሁሉ : መኻከል : ይልቁንም : ለመጠበቃችሁ : አደራ : በተሰጥዋችሁ : ወይስ : አደራ : በሚሰጥዋችሁ : መኻከል : ጭምትን : ዕርቅንም : ፍቅርንም : ትጠብቃላችሁን : ትዘርጉታላችሁምን ::

ም :: እግዚአብሔር : ቢረደኝ : አደርገዋለሁ ::

ኤጲስቆጶስ ::

በላያችሁን : ለተሾመ : ቄስ : ለሌሎችም : ለቤተ : ክርስቲያን : ታላቆች : አገልጋዮች : በላያችሁ : ለተሾሙ : አከብራችሁ : ትታዘዛላችሁን : እሺና : ደስም : ብላችሁ : ደህና : ምክራቸውን : ተከትላችሁን : ለደህና : ፍርዳቸውም : ታዛችሁን ::

ም :: እግዚአብሔር : ቢረደኝ : አደርገዋለሁ ::

የዚያን : ጊዜም : ኤጲስቆጶስ : ተነሥቶ : እንደሆ : ይበል ::

ሁሉን : የሚችል : እግዚአብሔር : ይህነን : ነገር : ሁሉ :

ለማድረግ ፡ ፈቃድን ፡ የሰጣችሁ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ እንድታ ደርጉት ፡ ኃይልና ፡ ችሎትን ፡ ይስጣችሁ ፡ በውሥጣችሁ ፡ የ ጀመረውን ፡ ስራው ፡ እስኪፈጽም ፡ ድረስ ፡ በየሱስ ፡ ክር ስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ጉባኤ ፡ በልባቸው ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ይለምኑላቸው ፡ ለዚች ም ፡ ልመና ፡ ዝምታ ፡ ይሁን ።

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ለቅስና ፡ የሚቀደሱ ፡ ሁሉ ፡ ተ ምበርክከው፡ኤጲስቆጶስና፡የሚቀሰሱም፡ይህች ን ፡ ዝማሬ ፡ አዝምረው ፡ ወይስ ፡ ነግረው ፡ እንዲ ህ ፡ ይበሉ ።

፩፤ ና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፈጣሪ ፡
የመንፈስ ፡ ቅቤን ፡ ቀባኢ ።
አንተ ፡ ልባችነን ፡ አብራ ፡
ሰባቱን ፡ ሀብትህ ፡ ስጠነ ።

---

፪፤ ያንተ ፡ ቡሩክ ፡ ከላይ ፡ መቅባት ፡
መጽናት ፡ ሕይወት ፡ የፍቅር ፡ እሳት ፡
ያብራልነ ፡ ለኛ ፡ ለዕውራን ፡
ዓይኖችነን ፡ ባንተ ፡ ብርሃን ።

---

፫፤ ርኩስት ፡ ፊታችነን ፡ ቀብተህ ፡
አብራ ፡ በጸጋ ፡ መላትህ ፡
ጸላት ፡ ይሸሽ ፡ ይጽና ፡ ሰላም ፡
ብትመራን ፡ ክፉ ፡ አይመጣም ።

---

፬፤ አብ ፡ ወልድም ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ባንድ ፡
አስታውቀን ፡ በሥላሴ ፡ አንድ ፡
እንዲህ ፡ ለወትሮ ፡ ዝማሬ ፡
ከኛ ፡ ይዘመር ፡ ለሥላሴ ፡

---

ላብ ፡ ለወልድ ፡ ለቅዱስ ፡ መንፈስ ፡
ኃይል ፡ ክብርም ፡ ምስጋናም ፡ ይድረስ ።



ወይስ ፡ ይህ ።

፩፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሕያው ፡ አምላክ ፡
ሠራጺ ፡ ከበላይ ፡
ከአብ ፡ ከወልድም ፡ ጋራ ፡ አምላክ ፡
ለውድ ፡ ለዕርቅም ፡ ና ።

---

፪፤ ጉበኛን ፡ በልባችን ፡ ስጥ ፡
ሰማዊት ፡ ጸጋህን ፡
በኃይልህ ፡ ቸኩለን ፡ እስክንርጥ ፡
የእውነት ፡ መንገድህን ።

---

፫፤ ባዘን ፡ ሁሉ ፡ በመከራ ፡
የምታጸናን ፡ አንተ ፡ ነህ ፡
የልዑል ፡ አምላክ ፡ ስጦወታ ፡
መላስ ፡ ያልደረሰህ ።

---

፬፤ ሕያው ፡ ምንጭ ፡ ለሰማይ ፡ ሕሴት ፡
ያቃጠልህም ፡ እሳት ፡
የውድ ፡ በርሃን ፡ በኃጢአት ፡ ሌት ፡
የመንፈስም ፡ መቅባት ።

---

፭፤ በሀብትህ ፡ ልዩነት ፡ ተነሣች ፡
የክርስቶስ ፡ ቤተክስያን ፡
ሕግህ ፡ በጻትህ ፡ ተጻፈች ፡
በልብ ፡ ለምእምናን ።

---

፮፤ ነገርን ፡ በሞገስ ፡ ስጠን ፡
አፈችነን ፡ ክፈት ፡
በኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡
በጸጋው ፡ ታላቅነት ።

---

፯፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብርሃንህን ፡ ስጥ ፡
ልባችን ፡ ሊነድልን ፡
ላምላክ ፡ መገዛትን ፡ ልንሰጥ ፡
በሌትና ፡ በቀን ።

---

፰፡ ድካማችነን ፡ አውቀሃል ፡
አበርትተህ ፡ አጽናን ፡
ባይሆን ፡ በኛ ፡ ድል ፡ ይነሣል ፡
ሥጋ ፡ ዓለም ፡ ሰይጣን ፡፡

---

፱፡ ጸላታችነን ፡ ምታልን ፡
የአምላክን ፡ ሰላም ፡
ወደ ፡ ልባችን ፡ አውረድልን ፡
ከሁሉ ፡ ደህ ፡ መልካም ፡፡

---

፲፡ አንተም ፡ አቤቱ ፡ መርተህን ፡
ከክፉ ፡ ጠብቀን ፡
ከቅን ፡ መንገድህ ፡ ወጥተን ፡
ካንተ ፡ እንደትጥለን ፡፡

---

፲፩፡ እንደህ ፡ ያለውን ፡ የጸጋህን ፡
ልክ ፡ አቤቱ ፡ ስጠን ፡
ትሆን ፡ ዘንድ ፡ የሚያጸናን ፡
ኋላ ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡፡

---

፲፪፡ ጸላትነት ፡ ክርክርንም ፡ አጥፋ ፡
በክርስቲያን ፡ ሁሉ ፡ አገር ፡
የዕርቅ ፡ የፍቅርም ፡ ማሠርያ ፡
ያገኛ ፡ ሁሉን ፡ ነገር ፡፡

---

፲፫፡ በጸጋህም ፡ አስታውቀን ፡
ኃይል ፡ ሁሉ ፡ ያለውን ፡ አብ ፡
በውድም ፡ ልጁ ፡ አንድንድን ፡
ደስ ፡ ብሎን ፡ ያላሳብ ፡፡

---

፲፬፡ ማመን ፡ ከልብ ፡ በአፍ ፡ ደፍሰስ ፡
እንታመንህ ፡ ዘንድ ፡ ባንድ ፡
የአብና ፡ የወልድ ፡ መንፈስ ፡
ሶስት ፡ አካል ፡ አምላክ ፡ አንድ ፡፡

---



፲፭፡ ለእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ምስጋናው ፡
ለቡሩክ ፡ ወልደም ፡ ደሁን ፡
ለመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ለጸጋው ፡
ሶስት ፡ ፈጽመው ፡ አንድ ፡ ምስጉን ፡፡

---

፲፮፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ስደድ ፡ መንፈስህን ፡
ያንተን ፡ የሥላሴን ፡
ስም ፡ ላወቁ ፡ ደይ ፡ ክብርህን ፡
ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

---

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ኢጺስቀጾስ ፡ ይጸልይ ፡ እንደህ ፡ ሲል ፡፡
እንጸልይ ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ የሰማዩ ፡ አባታችን ፡ ሆ
ይ ፡፡ ወደኛ ፡ ባለችህ ፡ ባልተወሰነች ፡ ፍቅርና ፡ ቸርነትህ ፡ አን
ደን ፡ ከሁሉም ፡ የተወደደውን ፡ ልጅህ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ
ን ፡ ማድኃኛችንና ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ፈጣርያችን ፡ ይሆ
ን ፡ ዘንድ ፡ ሰጥተሃልና ፡፡ እርሱም ፡ የመድኃኒታችነን ፡ ስ
ራ ፡ በሞቱ ፡ ከፈጸመ ፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ሐ
ዋርያቱን ፡ ነቢያቱንም ፡ ወንጌላውያኑንም ፡ መምህራኑን
ም ፡ ጠባቆቹንም ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ሰድዋልና ፡፡ በርሳ
ቸውም ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ የቅዱስ ፡ ስም
ህን ፡ የዘላለም ፡ ክብረን ፡ ደገልጹ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ መንጋ
ውን ፡ ሰብስብዋልና ፡፡ ስለዚች ፡ ስለ ፡ ታላቅ ፡ ምህረትህ ፡
በረከት ፡ እሌህንም ፡ ባሮችህ ፡ ከዚህ ፡ ላሉትን ፡ ወደዚች ፡
ለሰው ፡ ዘላለም ፡ ደህንነት ፡ ወደ ፡ ሠራሃት ፡ ሹመት ፡ ስለ ፡
ጸራሃቸው ፡ ከለልባችን ፡ እናመሰግንሃለን ፡ እናከብርህማ
ለን ፡ እናመልክህማለን ፡፡ ደግሞም ፡ በተባረከ ፡ ልጅህ ፡ በ
ትሕትና ፡ እንለምንሃለን ፡ ከዚህና ፡ በሌላ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡
በስምህ ፡ ለምንጸራ ፡ ሁሉ ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ስለዚችና ፡
ስለ ፡ ሌላ ፡ በረከትህ ፡ ሁሉ ፡ ለዘወተር ፡ እናመሰግንህ ፡ ዘ
ንድ ፡ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ ባንተና ፡ በልጅህ ፡ እውቀት ፡ በመ
ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ኃይል ፡ በዝተን ፡ እናድግ ፡ ዘንድ ፡፡ እንደሁ

ም ፡ በሌህ ፡ ባሮችህ ፡ እርሳቸውም ፡ በላያቸው ፡ በሚኾሙ ፡ ሰዎች ፡ ቅዱስ ፡ ስምህ ፡ ለዘላለም ፡ ይክበር ፡ የተባረከችም ፡ መንግሥትህ ፡ ትስፋ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አንድነት ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ በሚኖር ፡ በሚገዛም ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

ይህችም ፡ ጸሎት ፡ ከተጨረሰች ፡ በኋላ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከዚያ ፡ ካሉ ፡ ቀሳውስት ፡ ጋራ ፡ ቅስናውን ፡ ይቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ ለመጡ ፡ ለያንዳንዳቸው ፡ እጃቸውን ፡ በየራሶ ፡ ላይ ፡ ይጫኑ ፡ ተቀባዩም ፡ ሁሉ ፡ ኢየመጣ ፡ በጉልበቱ ፡ ይንበርክክ ፡ እጲስቆጶስም ፡ እንዲህ ፡ ይበል ።

መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተቀበል ፡ አሁን ፡ እጃችን ፡ በመጫን ፡ ለተሰጠችህ ፡ ለቅስና ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ። ኃጢአቱን ፡ የምትተውለት ፡ ተተወለት ፡ የምታኖርበትም ፡ ይኖርበታል ። አንተም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃልና ፡ የቅዱሳት ፡ ምሥጢራቱ ፡ የታመነህ ፡ ከፋፋይ ፡ ሁን ፡ በአብ ፡ በወልድም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ። አሜን ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለያንዳንዳቸው ፡ ገና ፡ በጉልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡ ሳለ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስን ፡ በጁ ፡ ይስጥለት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ።

ሥልጣንን ፡ ተቀበል ፡ በሥርዓት ፡ ወደምትሾምባት ፡ ጉባኤ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ለመስበክ ፡ ቅዱሳት ፡ ምሥጢራትንም ፡ ለመከፋፈል ።

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ የኒቅያ ፡ ስምቦሎን ፡ ተዝምሮ ፡ ወይስ ፡ ተንግሮ ፡ ይባል ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የቍርባንን ፡ ማገልገል ፡ ይፍጸም ፡ የተቀደሱም ፡ ይኑሩ ፡ ሁላቸው ፡ እስኪቍርቡ ፡ ድረስ ። ከቍርባንም ፡ በኋላ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ጭራሽ ፡ በረከትን ፡ ሳይል ፡ እሌህን ፡ ልመናች ፡ ይበል ።

በሁሉ ፡ መሓሪ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ በሌ



ህ ፡ ባሮችህ ፡ ላይ ፡ ሰማያዊት ፡ በረከትህን ፡ እንድታፈስ ፡ እርሳቸው ፡ ጽድቅን ፡ ይለብሱ ፡ ዘንድ ፡ ካፋቸውም ፡ የሚወጣ ፡ ቃልህ ፡ ይበጅ ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ በከንቱ ፡ እንዳይባል ። ልኛም ፡ ጸጋህን ፡ ስጠኝ ፡ እርሳቸው ፡ ከቅዱስ ፡ ቃልህ ፡ ቲዘ ፡ ወይስ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ገጽሞ ፡ የሚነግሩን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ደህንነታችን ፡ እንዲመራኝ ፡ እኛ ፡ በቃልና ፡ በስራ ፡ ያንተን ፡ ክብር ፡ የመንግሥትህንም ፡ መብዛት ፡ እንሻ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ። አሜን ።

በምናደርገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ቅደምን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ በመህረትና ፡ በጸጋ ። በምትዘወትርም ፡ረዲትህ ፡ ምራን ። በስራችን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ የምንጀምረው ፡ የምንጨምረውም ፡ የምንጨርሰውም ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናከብር ፡ ዘንድ ። በመጨረሻም ፡ በምህረትህ ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ። በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ። አሜን ።

ከአእምሮ ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰላም ። ልባችሁንና ፡ መንፈሳችሁን ፡ ይጠብቅ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በልጁ ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በውቀቱና ፡ በውዴ ። ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ የእግዚአብሔር ፡ የአብ ፡ የወልድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በረከት ፡ በመኻከላችሁ ፡ ይሁን ። ከላንት ፡ ጋራም ፡ ይኑር ፡ ለዘላለም ። አሜን ።

በዚያ ፡ ቀንም ፡ እያሌ ፡ የዲቁናን ፡ እያሌም ፡ የቅስናን ፡ ቅደሴ ፡ ቢቀበሉ ፡ ዲያቆናት ፡ ይቅደሙ ፡ ቀሳውስትም ፡ ይከተሉ ። ሊጣኒያም ፡ ለሁላቸው ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ቢደገም ፡ ይበቃል ። የዲያቆናትም ፡ ልመና ፡ ይቅደም ፡ የቀሳውስትም ፡ ይከተል ። የመልእክት ፡ ክፍል ፡ ኤፌሶን ፡ ፩፤ ፯፤—፲፫፤ ይሁን ። ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ዲያቆናት ፡ የንግሥትን ፡ አለቅነት ፡ መሐላ ፡ ይምሉ ፡ ይመረመሩም ፡ ይቀደሱም ። ከርሳቸውም ፡ አንድ ፡ የወንጌልን ፡ ክፍል ፡ ማቴዎስ ፡ ፮፤ ፳፯፤—፴፫፤ ወደ

ስ ፡ ሉቃስ ፡ ፲፪፡ ፴፫፡—፴፰፡ ይድገም ፡ በዲቁና ፡ በቅስና ፡ ቅደሴ ፡ ሥርዓት ፡ እንደ ፡ ተመለከተ ፡፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ቀሳውስት ፡ የንግሥትን ፡ አለቅነት ፡ መሐላ ፡ ይማሉ ፡ ይፈተኑም ፡ ይቀሰሱም ፡ በዚች ፡ መሳሌ ፡ እንደ ፡ ተመለከተ ፡፡

---

የሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ወይስ ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ ቅደሴ ፡ ወትሮ ፡ በእሁድ ፡ ወይስ ፡ በበዓል ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ የሚሻ ፡፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡ ከተጨረሰ ፡ በኋላ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥርዓት ፡ በተዘጋጀ ፡ ጊዜ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ወይስ ፡ በርሶ ፡ ፈንታ ፡ የተደረገ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የቍርባንን ፡ ማገልገል ፡ ይጀምር ፡ በርሶም ፡ ይህቺ ፡ ልመና ፡ ትሁን ፡፡

ልመና ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡ አንተ ፡ በልጅህ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ለቅዱሳን ፡ ሐዋርያትህ ፡ ብዙ ፡ የከበረውንም ፡ ስጥወታ ፡ ሰጥተህ ፡ መንጋህን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸዋልና ፡፡ ለኤጲስቆጶሳት ፡ ሁሉ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ጠባቆች ፡ ስጥ ፡ እንለምንሃለን ፡ እርሳቸው ፡ ጨክነው ፡ በቃልህ ፡ እንዲሰብኩ ፡ የምትወደውንም ፡ ትግሣጹን ፡ እንደሚገባ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ጉባኤም ፡ እሺ ፡ ብለው ፡ ይከተሉት ፡ ዘንድ ፡ ስጣቸው ፡፡ ሁላቸው ፡ የዘላለምን ፡ ክብር ፡ አክሊል ፡ ይቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

ሌላ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ የመልእክትን ፡ ክፍል ፡ ያንብብ ፡፡

የመልእክት ፡ ክፍል ፡፡ ፩፡ ጢሞቴዎስ ፡ ፫፡ ፩፡ —፯ ፡፡

ነገሩ ፡ እውነት ፡ ነው ፡፡ ማንም ፡ ጳጳስናውን ፡ ቢሻ ፡ መልካሙን ፡ ነገር ፡ ይሻል ፡፡ ጳጳስም ፡ ነውር ፡ እንዳይገኝበት ፡ ይገባዋል ፡፡ ያንዲት ፡ ምሽትም ፡ ባል ፡ ያለ ፡፡ የሚተጋም ፡፡



የነብረቱንም ፡ ልክ ፡ የሚጠብቅ ፡፡ ገርም ፡ ያለ ፡፡ እንግዶችንም ፡ የሚወድ ፡፡ አስተማሪም ፡፡ የጾጅም ፡ ሰካሪ ፡ ያይደለ ፡፡ የማይማታም ፡፡ የረከሰውንም ፡ ረብ ፡ የማይሻ ፡፡ ታጋሽ ፡ እንጅ ፡፡ የማይጣላም ፡፡ የብር ፡ ወዳጅም ፡ ያይደለ ፡፡ የርሶንም ፡ ቤት ፡ ሥርዓት ፡ ያሳመረ ፡፡ የታዘዙለትም ፡ ልጆች ፡ ያሉት ፡ በክብድና ፡ ሁሉ ፡፡ ሰው ፡ ግን ፡ የርሶን ፡ ቤት ፡ ለመግዛት ፡ ባያውቅ ፡፡ እንዴት ፡ ይቻለዋል ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡፡ አዲስ ፡ ተክልም ፡ በሃይማኖት ፡ አይሁን ፡ ልቡ ፡ እንዲይታበይ ፡ ወደ ፡ ዲያብሎስ ፡ ፍርድም ፡ እንዲይወድቅ ፡፡ ደግሞም ፡ ደህና ፡ ምስክር ፡ በሜዳ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ ይሆንለት ፡ ዘንድ ፡ ይፈለግበታል ፡ ወደ ፡ ስድብ ፡ እንዲይወድቅ ፡ ወደ ፡ ዲያብሎስም ፡ ወጽመድ ፡፡

ወይስ ፡ ይህ ፡፡

በመልእክት ፡ ፈንታ ፡፡ የሐዋርያት ፡ ስራ ፡ ፳፡ ፲፯፡ — ፴፰፡፡

ከመሊጡስም ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ላከ ፡፡ የቤተ ፡ ክርስቲያኒቱንም ፡ ሽማግሎች ፡ ጸራ ፡፡ ወደርሱም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ አላቸው ፡፡ እላንተ ፡ ታውቃላችሁ ፡ ወደ ፡ እስያ ፡ ከገባሁበት ፡ ከመጀመርያ ፡ ቀን ፡ ጀምሬ ፡ እንዴት ፡ ነበርሁ ፡ በላንተ ፡ ዘንድ ፡፡ እግዚአብሔርን ፡ አገለግል ፡ ነበርሁና ፡ በትሕትና ፡ ሁሉ ፡፡ በብዙ ፡ እንብም ፡ በደረሰብኝም ፡ ፈተና ፡ አይሁድ ፡ ሲሸምቁብኝ ፡፡ ከሚጠቅማችሁም ፡ ነገር ፡ አንዳች ፡ አልከለከልሁባችሁም ፡ ነገርኋችሁ ፡ እንጅ ፡፡ በጉባዔም ፡ በየቤታችሁም ፡ አስተማርኋችሁ ፡ ለአይሁድና ፡ ለአረማውያን ፡ ስመሰክር ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመመለስ ፡ በጌታችንም ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በማመን ፡፡ አሁንም ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ በመንፈስ ፡ ታሥሬ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም ፡ እሔዳለሁ ፡ በርስዋ ፡ ምን ፡ የሚሆንብኝን ፡ ሳላውቅ ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በያገሩ ፡ እንዲመስክርብኝ ፡ እንጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡ እሥራትና ፡ መከራ ፡ ይቈይኻል ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይኸነን ፡ ሁሉ ፡ ምክንያት ፡ አድርጌ ፡ አልቈጥረውም ፡፡ ነፍሴም ፡ እንኳ ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ የከበረች ፡ አይደለችም ፡ ሩጫዬን ፡ በደስታ ፡

አፈጽም ፡ ዘንድ ። ከጌታም ፡ ከየሱስ ፡ የተቀበልኋትን ፡ መልክቴን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የጸጋውን ፡ ወንጌል ፡ እመሰክር ፡ ዘንድ ። አሁንም ፡ እነሆ ፡ እላንተ ፡ ሁላችሁ ፡ በመኻከላችሁ ፡ ዙሬ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ያስተማርሁላችሁ ፡ እንጊዲህ ፡ ደግሞ ፡ ፊቴን ፡ እንደታዩ ፡ እኔ ፡ አውቃለሁ ። ስለዚኽም ፡ እኔ ፡ በዚኽ ፡ ቀን ፡ ከሁላችሁ ፡ ደም ፡ ንጹሕ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እመሰክርባችኋለሁ ። የእግዚአብሔርን ፡ ምክር ፡ ሁሉ ፡ እላንትን ፡ ከማስተማር ፡ እምቢ ፡ አላልሁምና ። አሁንም ፡ ለራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፡ ለመንጋውም ፡ ሁሉ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በማኽልዋ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ አድርጎ ፡ የሾማችሁ ። የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እርሱ ፡ በደሙ ፡ የዋጃትን ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ። ይኽነን ፡ እኔ ፡ አውቃለሁና ፡ ከሔድሁ ፡ በኋላ ፡ ክፎች ፡ ተኵላዎች ፡ እንደገቡባችሁ ፡ ለመንጎች ፡ የማያዝኑ ። ከላንትም ፡ እንኳ ፡ በመኻከላችሁ ፡ ሰዎች ፡ አሉ ፡ ተነሥተው ፡ ጠማማ ፡ ነገርንም ፡ ነግረው ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትን ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይስቡ ፡ ዘንድ ፡ ጊዜ ፡ ያላቸው ። ስለዚኽም ፡ ንቁ ፡ ሦስት ፡ አመትም ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ በንብ ፡ ከላንት ፡ ኢያንደንዷችሁን ፡ ከማስተማር ፡ እንደልተውሁ ፡ አስቡ ። አሁንም ፡ ወንድሞቼ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለጸጋውም ፡ ነገር ፡ አደራ ፡ ሰጥቻችኋለሁ ። ይሠራችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከቅዱሳንም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ርስትን ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ። ወርቅ ፡ ግን ፡ ብርም ፡ ልብስም ፡ ከማንም ፡ አልሻሁም ። እላንትም ፡ ታውቃላችሁ ፡ እሌኽ ፡ እጆቼ ፡ ለምሻው ፡ ነገር ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ላሉትም ፡ ጕደይ ፡ እንደገለገሉ ። ሁሉንም ፡ ገለጥሁላችሁ ። እንዲሁም ፡ እንዲገባችሁ ፡ ትደክሙ ፡ ዘንድ ፡ ደካሞችንም ፡ በፍቅር ፡ ትቀባበሉ ፡ ዘንድ ፡ የጌታን ፡ የየሱስን ፡ ቃል ፡ አስባችሁ ። እርሱ ፡ ብልዋልና ። መስጠት ፡ ከመውሰድ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ሌላ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ያንብብ ።

የወንጌል ፡ ክፍል ። ዮሐንስ ፡ ፳፩፡ ፲፭—፲፯።

ምሳቸውንም ፡ ከበሉ ፡ በኋላ ፡ የሱስ ፡ ሲሞን ፡ ጴጥሮስን ፡ አለው ። ሲሞን ፡ ሆይ ፡ የዮና ፡ ልጅ ፡ ከለዚኽ ፡ ይልቅ ፡ ትወደኛለኽን ። አለውም ። አዎን ፡ አቤቱ ። አንተ ፡ እንድወድኽ ፡ ታውቃለኽ ። አለውም ። ጥቦቶቼን ፡ ጠብቅ ። ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ አለው ። ሲሞን ፡ ሆይ ፡ የዮና ፡ ልጅ ፡ ትወደኛለኽን ። አለውም ፡ አዎን ፡ አቤቱ ። አንተ ፡ እንድወድኽ ፡ ታውቃለኽ ። እርሱም ፡ አለው ። በጎቼን ፡ ጠብቅ ። ሦስተኛ ፡ ጊዜም ፡ አለው ። ሲሞን ፡ ሆይ ፡ የዮና ፡ ልጅ ፡ ትወደኛለኽን ። ጴጥሮስም ፡ ሦስተኛ ፡ ጊዜ ፡ ትወደኛለኽን ፡ ስላለው ፡ አዘነ ። አለውም ። አቤቱ ፡ አንተ ፡ ሁሉን ፡ ታውቃለኽ ። አንተም ፡ እንድወድኽ ፡ ታውቃለኽ ። የሱስም ። በጎቼን ፡ ጠብቅ ፡ አለው ።



ወይስ ፡ ይህ ።

ዮሐንስ ፡ ፳፡ ፲፱—፳፫፡

ያም ፡ ቀን ፡ እርሱም ፡ የሰንበት ፡ መጀመርያ ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ወደ ፡ ተከማቹበት ፡ ደጁ ፡ ተቈልፎ ፡ ሳለ ፡ አይሁድን ፡ ስለ ፡ ፈሩ ። መጣ ፡ የሱስ ፡ በማኸላቸውም ፡ ቆመ ፡ አላቸውም ። ሰላም ፡ ይሁንላችሁ ። ይህነንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እጁንና ፡ ጐኑን ፡ አሳያቸው ። ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ጌታን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። የሱስም ፡ ደግሞ ፡ አላቸው ። ሰላም ፡ ይሁንላችሁ ። አብ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ እንዲሁም ፡ እኔ ፡ እልካችኋለሁ ። ይህነንም ፡ ብሎ ፡ እፍ ፡ አለባቸው ፡ አላቸውም ። መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተቀበሉ ። ኀጢአቱን ፡ የምታስቀሩለት ፡ ቀረችለት ፡ የምታኖሩበትም ፡ ሰው ፡ ትኖርበታለች ።

ወይስ ፡ ይህ ።

ማቴዎስ ፡ ፳፰፡ ፲፰—፳።

የሱስም ፡ መጣና ፡ ተናገራቸው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ሥልጣን ፡ ሁሉ ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ተሰጠኝ ። እንጊዲህም ፡ ሒዱና ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አስተምሩ ። በአብና ፡ በወልድም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ አጥምቋቸው ። ያዘዝኋችሁትንም ፡ ሁሉ ፡ መጠበቅ ፡ አስተምርዋቸው ። እኔም ፡ እነሆ ፡ ከላንት ፡ ጋራ ፡ ነኝ ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ። አሜን ።

ወንጌልም ፡ የኒቅያ ፡ ስምቦሎንም ፡ ስብከትም ፡
ካለቀ ፡ በኋላ ፡ የተመረጸ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሮኙት ፡
የሚባለውን ፡ የኤጲስቆጶስን ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡
ሁለት ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ይዘውት ፡ በሊቀ ፡ ጳጳስ ፡
ፊት ፡ ወይስ ፡ በርሱ ፡ ፈንታ ፡ በተደረገ ፡ ኤጲስቆጶ
ስ ፡ ፊት ፡ ያቁሙት ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስም ፡ በወንበሩ ፡
በጌታ ፡ ሳድቃ ፡ አጠገብ ፡ ተቀምጦ ፡ የሚያደር
ሱት ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ እንዲህ ፡ ይበሉ ፡፡

በእግዚአብሔር ፡ እጅግ ፡ የከበሩ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ ይህነን ፡ ጻድቅና ፡ አዋቂውን ፡ ሰው ፡ እናደርስለዋለን ፡ ለኤጲስቆጶስና ፡ ይቀደስ ፡ ዘንድ ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ የንግሥትን ፡ ትእ
ዛዝ ፡ ስለዚች ፡ ቅዳሴ ፡ ይጠይቅ ፡ ያስነብበውም ፡፡
የተመረጸ ፡ ኤጲስቆጶስም ፡ የንግሥት ፡ አለቅነ
ትን ፡ መሐላ ፡ ይማል ፡ በዲያቆናት ፡ ቅዳሴ ፡ ሥ
ርዓት ፡ እንዳለ ፡፡ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ የሊቀ ፡ ጳ
ጳስ ፡ መታዘዝ ፡ መሐላ ፡ ይከተል ፡ እንዲህ ፡፡

ለሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ መታዘዝ ፡ መሐላ ፡፡

በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አሜን ፡፡ እኔ ፡ ፡ ለ ፡ ቤት ፡ ክርስቲያንና ፡ ግዛት ፡ የተመረጽሁ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ለተከታዮቻቸውም ፡ የሚገባውን ፡ ክብርና ፡ መታዘዝ ፡ እምልላቸዋለሁ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ይርደኝ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ግን ፡ ቢቀደስ ፡ ይህች ፡ መሐላ ፡ አት
ማል ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ የተሰበሰበችን ፡
ጉባኤ ፡ ልመና ፡ ይፈልግ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡

ወንድሞቴ ፡ ሆይ ፡ በሉቃስ ፡ ወንጌል ፡ መድኃኛችን ፡ ክርስቶስ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሐዋርያቱን ፡ መርጸው ፡ ሳይሰደቸው ፡ የዚያችን ፡ ሌት ፡ ሁሉ ፡ በጸሎት ፡ እንደ ፡ አደረ ፡ ይገኘል ፡ ደግሞም ፡ በሐዋርያት ፡ ስራ ፡ በአንጾኪያ ፡ የነበሩ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ለጳውሎስና ፡ ለበርናበስ ፡ እጃቸውን ፡ ጫኑው ፡ ሳይልኳቸው ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጾሙ ፡ እንደ ፡ ጸለዩም ፡ እናገኘለን ፡፡ ስለዚህም ፡ እኛ ፡ ደግመን ፡ ይህነን ፡ አሁን ፡ የደረሰልነውን ፡ ሰው ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንዲመስለን ፡ ለ ጸሬበቱ ፡ ስራ ፡ ሳንቀድስና ፡ ሳንልከው ፡ የመድኃኛችን ፡ የ ክርስቶስ ፡ የሐዋርያቱንም ፡ ምሳሌ ፡ ተከትለን ፡ እንጸልይ ፡፡



ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ በዲቁና ፡ ቅዳሴ ፡ እንዳለ ፡ ሊጣ
ኒያ ፡ ትከተል ፡ በዲያቆናት ፡ ልመና ፡ ፈንታ ፡ ግን ፡
ይህች ፡ ትለመን ፡፡

እንድትወድ ፡ ይህነን ፡ የተመረጸውን ፡ ወንድማችን ፡ ትባርክ ፡ ዘንድ ፡ ጸጋህንም ፡ ታወርድለት ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ የተጸራለቱን ፡ ሹመት ፡ እንደሚገባው ፡ እንዲፈጽም ፡ ለ ቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ መሠራት ፡ ለስምህም ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡፡

ምላሽ ፡፡ እንለምንሃለን ፡ ስማኒ ፡ አቤቱ ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ይህች ፡ ልመና ፡ ትከተል ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ የበጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰጭ ፡፡ አንተ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስህ ፡ ልዩን ፡ ልዩን ፡ ሥርዓት ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ አገልጋዮች ፡ አደርገሃልና ፡፡ ይህነን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ኤጲስቆጶስና ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ የተጸራውን ፡ ባርያህ ፡ በምህረት ፡ እየው ፡ የውነትህንም ፡ ትምርት ፡ እንዲህ ፡ ምላበት ፡ በሕይወቱም ፡ ንጽሕና ፡ አስጊጸው ፡ እርሱ ፡ በቃልና ፡ በስራ ፡ በዚች ፡ ሹመት ፡ ታምኖ ፡ ያገለግልህ ፡ ዘንድ ፡ ለስምህ ፡ ምስጋና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያንህም ፡ መሠሪትና ፡ መግዛት ፡ በማድኃኛችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ምግባር ፡ እርሱ ፡ የሚኖር ፡ የሚገዛም ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ በወንበሩ ፡ ተቀ
መጦ ፡ ለቅዳሴ ፡ የሚቀርበውን ፡ እንዲህ ፡ ይበል ፡፡

ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስና ፡ የድሮ ፡ ቃኖኖች ፡ ክርስቶስ ፡ የከበረውን ፡ ደሙን ፡ ዋጋ ፡ አድርጎ ፡ በተበጀት ፡

በቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ለመግዛት ፡ ሰውን ፡ እጃችንን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ጭነን ፡ እንቀድስ ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ እንደንፈጥን ፡ አዘናልና ፡፡ እኔ ፡ ወደዚች ፡ ሹመት ፡ ሳላገባወ ፡ ባንደንድ ፡ ነገር ፡ ለመርምረወ ፡ ይህች ፡ ጉባኤ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ትመሰክርም ፡ ዘንድ ፡ ልበወ ፡ ፈቃደወም ፡ እንዴት ፡ እንደለ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለመመላለስ ፡፡

እርሰወም ፡ በውነት ፡ እንደ ፡ ጌታችን ፡ እንደ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ፈቃድ ፡ እንደዚች ፡ መንግሥትም ፡ ወግ ፡ ለዚች ፡ ሹመትን ፡ የተጸሩ ፡ መሰለወ ፡፡

ም ፡፡ እንዴህ ፡ መሰለኝ ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ ለዘላለም ፡ መድኃኒት ፡ በሃይማኖት ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በግድ ፡ የሚሻ ፡ ትምህርት ፡ ሁሉ ፡ በመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ በቅቶ ፡ ይገኛል ፡ ይላሉን ፡፡ አደራም ፡ የተሰጥወን ፡ ሕዝብ ፡ በመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ እንዲያስተምሩ ፡ ሌላ ፡ ነገርንም ፡ በግድ ፡ ለዘላለም ፡ መድኃኒት ፡ ይፈለጋል ፡ ብለው ፡ እንዲያስተምሩ ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ይወጣልና ፡ በርሱ ፡ ይመሰከርለታል ፡ የሚሉት ፡ እንጅ ፡ ፈቃደወን ፡ ነው ፡፡

ም ፡፡ እንዴህ ፡ እላለሁ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ጸጋ ፡ ፈቃዴ ፡ እንዴህ ፡ ነው ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ እንኪያስ ፡ እርሰወን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ታምነው ፡ ይመረምራሉን ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲፈታለወን ፡ ይለምኑታልን ፡ እርሰወ ፡ የመድኃኒትን ፡ ትምህርት ፡ ያስተምሩበት ፡ ዘንድ ፡ ይመክሩበትም ፡ ዘንድ ፡ አሰተኞችንም ፡ መመህራን ፡ ይቃወሙበት ፡ ዘንድ ፡ ያሸንፏቸውም ፡ ዘንድ ፡፡

ም ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዴት ፡ እንዴህ ፡ አደርጋለሁ ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ የሚጸላውን ፡ እንግዳ ፡ ትምህርትና ፡ ስሕተት ፡ ሁሉ ፡ ይከለክሉና ፡ ይሸሩ ፡ ዘንድ ፡ ሌሎችንም ፡ እንደዚህ ፡ ለማድረግ ፡ በግልጽና ፡ በስውር ፡ ልብን ፡ ያደርጉላቸው ፡ ዘንድ ፡ በኃይለወ ፡ ሁሉ ፡ ታምነው ፡ ለመድከም ፡ የተዘጋጁ ፡ ነወን ፡፡

ም ፡፡ እግዚአብሔር ፡ ቢረደኝ ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ፡፡



ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ አለማምለክና ፡ የዓለምን ፡ ፍትወት ፡ ሁሉ ፡ ይክዷሉን ፡ በዚችም ፡ ዓለም ፡ በገርነት ፡ በጽድቅም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፍርሃትም ፡ ይኖራሉን ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ለሌሎች ፡ የበጎ ፡ ስራ ፡ ምሳሌ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ጸላትን ፡ ለማሳፈር ፡ የሚሰድቡበወን ፡ ነውር ፡ ባያገኝ ፡፡

ም ፡፡ እንዴህ ፡ አደርጋለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚረደኝ ፡ ቢሆን ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ በኃይለወም ፡ ሁሉ ፡ ጭምቱን ፡ ፍቅርንም ፡ ዕርቅንም ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ መኻከል ፡ ይገልጻሉን ፡ ሁከተኞችንም ፡ እምቢተኞችንም ፡ ሴሰኞችንም ፡ በጉልተወ ፡ ያሉትን ፡ ይጻየፏሉን ፡ ይገሥጻሉምን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃልና ፡ በዚች ፡ መንግሥት ፡ ሥርዓት ፡ እንደ ፡ ተቀበሉ ፡ ሥልጣን ፡፡

ም ፡፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዴት ፡ እንዴህ ፡ አደርጋለሁ ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ ሌሎችንም ፡ በመቅደስ ፡ እጅም ፡ ጭነው ፡ በመላካቸው ፡ የታመኑ ፡ ይሆናሉን ፡፡

ም ፡፡ እሆናለሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዴት ፡፡

ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡፡ ለድኆችና ፡ ለነደያን ፡ ረዴትም ፡ ለሌላቸው ፡ እንግዶች ፡ በክርስቶስ ፡ መክንያት ፡ ገርና ፡ መሓሪ ፡ ይሆናሉን ፡፡

ም ፡፡ እሆናለሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረዴት ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ተነሥቶ ፡ እንዴህ ፡ ይበል ፡፡

ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማያዊ ፡ አባታችን ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለማድረግ ፡ ፈቃድን ፡ የሰጠወ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ያደርጉት ፡ ዘንድ ፡ ኃይልና ፡ ችሎትን ፡ ይስጠወ ፡ በውሥጠወ ፡ የጀመረውን ፡ ስራ ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድ ፡ እርሰወ ፡ በኋለኛ ፡ ቀን ፡ ፍጹምና ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ሁነው ፡ ይገኙ ፡ ዘንድ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የተመረጸ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የቀረውን ፡ የኤጲስጶስን ፡ ልብስ ፡ ይልበስ ፡ እርሱም ፡

በኊልበቱ ፡ ሲንበረክክ ፡ ያች ፡ ዝማሬ ፡ "ና ፡ መ
ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፈጣሪ" ፡ አሁን ፡ ትዘመር ፡ በሊ
ቀ ፡ ጳጳስና ፡ በቀሩ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡፡

ወይስ ፡ ይች ፡፡

"መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሕያው ፡ አምላክ" ፡ የሚቀርም ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ሊቀጳጳስ ፡ እንዲህ ፡ ይበል ፡፡

አቤቱ ፡ ጸሎታችንን ፡ ስማ ፡፡
ም ፡፡ ጩኸታችንም ፡ መደንተ ፡ ይድረስ ፡፡

እንጸልይ ፡፡

ሁሉን ፡ የምትችል ፡ እግዚአብሔር ፡ በሁሉም ፡ መሐሪ ፡
አባታችን ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ወሰን ፡ በሌላት ፡ በቸርነትህ ፡ አን
ደን ፡ ከሁሉም ፡ የተወደደውን ፡ ልጅህ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶ
ስን ፡ ማድኀናችንና ፡ የዘላለም ፡ ሕይወታችን ፡ ፈጣሪ ፡ ይሆ
ንልን ፡ ዘንድ ፡ ሰጥተሃልና ፡፡ እርሱም ፡ መድኀኒታችንን ፡ በ
ሞቱ ፡ ከፈጸመ ፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ የስጥወ
ታውን ፡ ምላት ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ አፈስዋልና ፡ አያሌን ፡ ሐዋር
ያት ፡ አያሌንም ፡ ነቢያት ፡ አያሌንም ፡ ወንጌላውያን ፡ አያ
ሌንም ፡ ጠባቆችና ፡ መምህራን ፡ አድርጎ ፡ ኾመ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲ
ያኑን ፡ ለመሥራትና ፡ ለመፈጸም ፡፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ለ
ዚህ ፡ ባርያህ ፡ ጸጋህን ፡ ስጥ ፡ እርሱ ፡ ወትሮ ፡ ወንጌልህን ፡ የሰ
ውን ፡ መታረቅ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ የምታወራውን ፡ የምስራች ፡ አ
ዋጅ ፡ ለመንገር ፡ የተዘጋጀ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡፡ የተሰጠቸው
ንም ፡ ሥልጣን ፡ ለማጥፋት ፡ አይደለም ፡ ለማደን ፡ እንጅ ፡
ለመጉዳትም ፡ አይደለም ፡ ለመጥቀም ፡ እንጅ ፡ ይረባ ፡ ዘ
ንድ ፡ እንደ ፡ ጠቢብና ፡ እንደ ፡ ታመነ ፡ መጋቢ ፡ ለቤተ ፡ ሰቦ
ችህ ፡ ፈንታቸውን ፡ በየጊዜያቸው ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ በመጨ
ረሻም ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ደስታ ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡፡ በየሱስ ፡ ክ
ርስቶስ ፡ በጌታችን ፡ ካንተና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ የ
ሚኖር ፡ የሚገዛም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ የተመረጸ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በሊቀ ፡
ጳጳስና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ባሉ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ በፊ



ታቸው ፡ በኊልበቱ ፡ ተምበርክኮ ፡ ሲሆን ፡ እርሳ
ቸው ፡ እጃቸውን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይጫኑ ፡ ሊቀ ፡ ጳ
ጳስም ፡ እንደዚህ ፡ ይበለው ፡፡

መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተቀበል ፡ አሁን ፡ እጃችን ፡ በመጫን ፡ ለተ
ሰጠችህ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ሹመትና ፡ ስራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማ
ኅበር ፡፡ በአብ ፡ በወልድም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡፡
አሜን ፡፡ አሁንም ፡ እጃችን ፡ በመጫን ፡ የተሰጠችህን ፡ የ
እግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ በልብህ ፡ ታነቃ ፡ ዘንድ ፡ አስብ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የፍርሃትን ፡ መንፈስ ፡ አልሰጠነምና ፡ የኃይል
ን ፡ እንጅ ፡ የፍቅርንም ፡ የጭምትንም ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስ
ን ፡ ይስጠው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡፡

በንባብ ፡ አዘውትር ፡ በምክርም ፡ በማስተማርም ፡፡ በዚ
ህ ፡ መጽሐፍ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ አስብ ፡ ነፍስህንም ፡ ሁሉ ፡
ሰጥተህ ፡ አድርገው ፡ ከርሱ ፡ የሚወጣ ፡ ጥቃሜ ፡ ለሰው ፡
ሁሉ ፡ ይገለጽ ፡ ዘንድ ፡፡ ራስህን ፡ ጠብቅ ፡ ትምህርትንም ፡
በርስዋም ፡ ጽና ፡፡ ይህን ፡ ብታደርግ ፡ ነፍስህን ፡ ታድናለህ
ና ፡ የሚሰሙህንም ፡፡ ለክርስቶስም ፡ መንጋ ፡ ተኵላ ፡ አት
ሁን ፡ ጠባቂ ፡ እንጅ ፡፡ አሳምራቸው ፡ አትብላቸውም ፡፡ ደካ
ሞችን ፡ ደግፍ ፡፡ የታመሙትንም ፡ ፈውስ ፡፡ የተሰበሩትን
ም ፡ ጠግን ፡፡ የተጣሉትንም ፡ መልስ ፡፡ የጠፉትንም ፡ ፈልግ ፡፡
መሐሪም ፡ ስትሆን ፡ አትላላ ፡፡ ተግሣጽንም ፡ ብታደርግ ፡ ምሕ
ህረትን ፡ አትርሳ ፡፡ የጠባቆች ፡ አለቃ ፡ ሲገለጽ ፡ ጊዜ ፡ ከቶ ፡
የማይረግፈውን ፡ የክብርን ፡ አክሊል ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡ በ
የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌታችን ፡፡ አሜን ፡፡

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ የቍርባንን ፡ ማገ
ልገል ፡ ይፈጽም ፡ አሁንም ፡ የተቀደሰ ፡ ኤጲስቆጶ
ስ ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ ይቍረብ ፡፡

ከቍርባንም ፡ በኋላ ፡ ከጭራሽ ፡ በረከትም ፡ በፊ
ት ፡ እሌህ ፡ ልመናች ፡ ይባሉ ፡፡

በሁሉ ፡ መሐሪ ፡ አባት ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ እንለምንሃለን ፡ ለዚ

ህ ፡ ባርያህ ፡ ሰማያዊት ፡ በረከትህን ፡ ታወርድለት ፡ ዘንድ ፡፡ መንፈስ ፡ ቅዱስህንም ፡ እንደሁ ፡ አልብሰው ፡ እርሱ ፡ በቃልህ ፡ ሰብኮ ፡ ከለልቡ ፡ በትዕግሥትና ፡ በትምርት ፡ ሁሉ ፡ እንዲገሥጽ ፡ እንዲመክርም ፡ እንዲጸየፉም ፡፡ በቃልም ፡ ባካሔድም ፡ በፍቅር ፡ በሃይማኖትም ፡ በንጽሕናም ፡ በቅንነትም ፡ ለምእምናን ፡ ደህና ፡ ምሳሌ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡፡ እርሱ ፡ ሩጫውን ፡ ታምኖ ፡ ሲፈጽም ፡ ጊዜ ፡ በኋለኛ ፡ ቀን ፡ ጌታው ፡ ያ ፡ ጻድቅ ፡ ፈራጅ ፡ የሚጠብቀውን ፡ የጽድቅን ፡ አክሊል ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ከርሱ ፡ ከአብና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ሁኖ ፡ ከሚኖርና ፡ ከሚገዛ ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

በምናደርገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ቅደምን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፡ በመሀረትና ፡ በጸጋ ፡፡ በምትዘወትርም ፡ ረዴትህ ፡ ምራን ፡፡ በስራችን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ የምንጀምረው ፡ የምንጨምረውም ፡ የምንጨርሰውም ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናከብር ፡ ዘንድ ፡፡ በመጨረሻም ፡ በምህረትህ ፡ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንቀበል ፡ ዘንድ ፡፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡፡ አሜን ፡፡

ከአእምሮ ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰላም ፡፡ ልባችሁንና ፡ መንፈሳችሁን ፡ ይጠብቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ በልጁም ፡ በጌታችን ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በውቀቱና ፡ በውዴ ፡፡ ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ የእግዚአብሔር ፡ የአብ ፡ የወልድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በረከት ፡ በመኻከላችሁ ፡ ይሁን ፡፡ ከላንት ፡ ጋራም ፡ ይኑር ፡ ለዘላለም ፡፡ አሜን ፡፡

---

የጉባኤ ፡ ጸሎት ፡ መጽሐፍ ፡
መጨረሻ ፡፡

---

# የዳዊት ፡ መዝሙራት ፡፡

## መጀመርያ ፡ ቀን ፡፡

### የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

### መዝሙር ፡ ፩፡

፩፡ ምስጉን ፡ ነው ፡ በክፎች ፡ ምክር ፡ ያልሔደ ፡ ሰው ፡
በኃጢአተኞችም ፡ መንገድ ፡ ያልቆመ ፡
በዋዘኞችም ፡ ወንበር ፡ ያልተቀመጠ ፡፡
፪፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ደስ ፡ የሚለው ፡ እንጅ ፡
ነፍሱንም ፡ ወደ ፡ ሕጉ ፡ የሚያደርግ ፡ በቀንና ፡ በሌት ፡፡
፫፡ እርሱ ፡ በውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ ዳር ፡ እንደ ፡ ተተከለች ፡ ዛፍ ፡
ይሆናል ፡
ፍሬዋን ፡ በየጊዜዋ ፡ እንደምትሰጥ ፡
ቅጸልዋም ፡ እንደማይረግፍ ፡፡
የሚሰራውንም ፡ ሁሉ ፡ በጅ ፡ ይለዋል ፡፡
፬፡ ክፎች ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አይደሉም ፡
ንፋስ ፡ ነፍሶ ፡ እንደሚወስደው ፡ ትቢያ ፡ እንጅ ፡፡
፭፡ ስለዚኽ ፡ ክፎች ፡ በፍርድ ፡ አይቆሙም ፡
ኃጢአተኞችም ፡ በጻድቃን ፡ ማኅበር ፡፡
፮፡ እግዚአብሔር ፡ የጻድቃንን ፡ መንገድ ፡ ያውቃልና ፡፡
የኃጢአተኞች ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ትጠፋለች ፡፡

### መዝሙር ፡ ፪፡

፩፡ ለምን ፡ ያብደሉ ፡ አሕዛብ ፡
ሰዎችም ፡ ከንቱ ፡ ይናገራሉ ፡፡
፪፡ ነገሥት ፡ ምድር ፡ ተነሡ ፡
መኳንንትም ፡ ባንድ ፡ ተማከሩ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ በመሢሑም ፡፡
፫፡ ማሰርያቸውን ፡ እንብጠስ ፡

ገመዷቸውንም ፡ ከኛ ፡ ዘንድ ፡ እንጣል ፡፡
፬፡ በሰማይ ፡ የሚኖር ፡ ግን ፡ ይስቅባቸዋል ፡፡
ጌታም ፡ ይሣለቅባቸዋል ፡፡
፭፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በቍጣው ፡ ይነግራቸዋል ፡
በመዓቱምም ፡ ያስፈራቸዋል ፡፡
፮፡ እኔም ፡ በፅዮን ፡ በተቀደሰ ፡ ተራራዬ ፡ ላይ ፡ ንጉሤን ፡ ሾ
ምሁ ፡፡
፯፡ በሕግ ፡ እናገራለሁ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ልጄ ፡ ነኽ ፡ አለኝ ፡፡
እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወለድሁኽ ፡፡
፰፡ ለምነኝ ፡ አሕዛብንም ፡ ለርስትኽ ፡ እሰጥኻለሁ ፡
የምድርንም ፡ ዳርቻ ፡ ለግዛትህ ፡፡
፱፡ በብረት ፡ ዘንግ ፡ ትጠብቃቸዋለኽ ፡፡
እንደ ፡ ሸክላ ፡ ሰሪ ፡ እቃም ፡ ትቀጠቅጣቸዋለኽ ፡፡
፲፡ አሁንም ፡ ነገሥት ፡ አስተውሉ ፡፡
ተገሠጹም ፡ ሁላችሁ ፡ የምድር ፡ መኳንንት ፡፡
፲፩፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፍርሃት ፡ ተገዙ ፡
በረዓድም ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡፡
፲፪፡ ልጁን ፡ ሳሙት ፡ እንዳይቈጣ ፡
በመንገድም ፡ ሳላችሁ ፡ እንዳትጠፉ ፡
ቍጣው ፡ ጥቂት ፡ ቍይታ ፡ ትነዳለችና ፡፡
በርሱ ፡ የሚታመኑ ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ፡፡

## መዝሙር ፡ ፫፡

፩፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ በዙ ፡ የሚያሳዝኑኝ ፡፡
በላዬም ፡ የቆሙ ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡፡
፪፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ነፍሴን ፡ አሉ ፡
ባምላኩ ፡ መድኃኒት ፡ የለውም ፡፡
፫፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ለኔ ፡ ለዋልታ ፡ ነኽ ፡፡
ክብሬም ፡ ራሴንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የምታረገው ፡ ነኽ ፡፡
፬፡ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮኻለሁ ፡
ከተቀደሰ ፡ ተራራውም ፡ ይሰማኛል ፡፡



፭፡ እኔ ፡ ተኛሁ ፡ አንቀላፋሁም ፡ ተነሣሁም ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ደግፎኛልና ፡፡
፮፡ ከሕዝብ ፡ አእላፋት ፡ ከሚከቡኝ ፡ አልፈራም ፡፡
፯፡ ተነሣ ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ አድነኝ ፡፡
አንተ ፡ የጸላቶቼን ፡ ሁሉ ፡ መንጋጋ ፡ መትተኻልና ፡፡
የክፎችን ፡ ጥርስ ፡ ሰብረሃልና ፡፡
፰፡ ማዳን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ፡
በሕዝብኽም ፡ ላይ ፡ በረከትኽ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፬፡

፩፡ ስጠራ ፡ ጊዜ ፡ መልስለኝ ፡ የጽድቄ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡
በጭንቀቴም ፡ አሰፋኽልኝ ፡፡
ማረኝ ፡ ጸሎቴንም ፡ ስማ ፡፡
፪፡ እላንት ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ክብሬን ፡ ታሳፍ
ራላችሁ ፡፡
ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ትወዳላችሁ ፡ ሐሰትንም ፡ ትሻላችሁ ፡፡
፫፡ እግዚአብሔር ፡ የሚወደውን ፡ እንደ ፡ መረጠለት ፡ እወቁ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ወደርሱ ፡ ስጠራ ፡ ጊዜ ፡ ይሰማል ፡፡
፬፡ ተቈጡ ፡ ኃጢአትንም ፡ አታድርጉ ፡፡
ልባችሁን ፡ በምኝታችሁ ፡ ሳላችሁ ፡ ንገሩ ፡ ዝምም ፡ በሉ ፡፡
፭፡ የጽድቅን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፡
ተስፈችሁንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አድርጉ ፡፡
፮፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡ በጎ ፡ ያለውን ፡ ማን ፡ ያሳየናል ፡ የሚሉ ፡፡
የፊትኽን ፡ ብርሃን ፡ በላያችን ፡ አንሣ ፡ አቤቱ ፡፡
፯፡ በልቤ ፡ ደስታ ፡ ሰጠኽ ፡
ስንዴያቸውና ፡ የወይን ፡ ጸጁቸው ፡ ከበዛ ፡ ጀምሮ ፡፡
፰፡ በሰላም ፡ ደግሞ ፡ እተኛለሁ ፡ አንቀላፋለሁም ፡፡
አንተ ፡ ብቻኽን ፡ አቤቱ ፡ በምነት ፡ አሳድረኸኛልና ፡፡

## መዝሙር ፡ ፭፡

፩፡ ቃሌን ፡ አድምፅ ፡ አቤቱ ፡ አሳቤንም ፡ አስተውል ፡፡
፪፡ የጩኸቴን ፡ ቃል ፡ አድምፅ ፡ ንጉሤና ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡፡

ወደንተ ፡ እጸልያለሁና ፡፡
፫፡ ማለዳ ፡ ድምፄን ፡ ትሰማለኸ ፡ አቤቱ ፡
ማልደ ፡ ልቤን ፡ ወደንተ ፡ አድርጌ ፡ እመለከታለሁ ፡፡
፬፡ ክፋትን ፡ የምትወድ ፡ አምላክ ፡ አንተ ፡ አይደለኸምና ፡፡
ባንተ ፡ ዘንድም ፡ ክፉ ፡ አያድርም ፡፡
፭፡ በከንቱ ፡ የሚመኩ ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ አይቆሙም ፡
ከንቱ ፡ አድራጎችንም ፡ ሁሉ ፡ ጸላኸ ፡፡
፮፡ አሰት ፡ የሚናገሩትን ፡ ታጠፋለኸ ፡፡
ደመኛውንና ፡ ሸንጋዩንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጸየፋዋል ፡፡
፯፡ እኔ ፡ ግን ፡ በምሕረትኸ ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ ቤትኸ ፡ እገባለሁ ፡
አንተንም ፡ ፈርቼ ፡ ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ መቅደስ ፡ እሰግዳለሁ ፡፡
፰፡ አቤቱ ፡ በጽድቅኸ ፡ ምራኝ ፡ ስለ ፡ ጸላቶቼ ፡፡
መንገድኸን ፡ በፊቴ ፡ አቅናልኝ ፡፡
፱፡ ባፋቸው ፡ እውነት ፡ የለምና ፡ ልባቸውም ፡ ማጥፊት ፡
ነውና ፡፡
ጉሮራቸውም ፡ የተከፈተ ፡ መቃብር ፡ ነው ፡
በመላሳቸውም ፡ ይሸነግላሉ ፡፡
፲፡ ፍረድባቸው ፡ አቤቱ ፡ በምክራቸም ፡ ይውደቁ ፡፡
እንደ ፡ ክፋታቸው ፡ ብዛት ፡ አሳደቸው ፡
እርሳቸው ፡ አምጸውብኻልና ፡፡
፲፩፡ ባንተ ፡ የሚታመኑ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡
ለዘላለሙ ፡ ይመኩ ፡ እርሳቸውን ፡ ትጠብቃለኸና ፡፡
ስምኸንም ፡ የሚወዱ ፡ ባንተ ፡ እልል ፡ ይበሉ ፡፡
፲፪፡ አንተ ፡ ጻድቁን ፡ ትባርካለኸና ፡ አቤቱ ፡፡
በጸጋም ፡ እንደ ፡ በጋሻ ፡ ትከበዋለህ ፡፡

---

## የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

## መዝሙር ፡ ፮፡

፩፡ አቤቱ ፡ በቍጣኸ ፡ አትዘልፈኝ ፡
በመዓትኸም ፡ አትገሥፀኝ ፡፡
፪፡ ማረኝ ፡ አቤቱ ፡ ድውይ ፡ ነኝና ፡፡



ፈውሰኝ ፡ አቤቱ ፡ አፅንቶቼ ፡ ታውከዋልና ፡፡
፫፡ ነፍሴም ፡ እጅግ ፡ ታወከች ፡፡
አንተም ፡ አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡፡
፬፡ ተመለስ ፡ አቤቱ ፡ ነፍሴንም ፡ ታደግ ፡፡
ስለ ፡ ምሕረትኸም ፡ አድነኝ ፡፡
፭፡ በሞት ፡ መታሰብኸ ፡ የለምና ፡
በሢኦልም ፡ የሚያመሰግንኸ ፡ ማነው ፡፡
፮፡ በልቅሶዬ ፡ ደክሞያለሁ ፡፡
ሌቱን ፡ ሁሉ ፡ አልጋዬን ፡ እነክራለሁ ፡፡
በንቤም ፡ ምንጣፌን ፡ አጠጣለሁ ፡፡
፯፡ ዓይኑ ፡ ባዘን ፡ ተበላሸች ፡
ስለ ፡ ጸላቶቼም ፡ ሁሉ ፡ አረጀች ፡፡
፰፡ ከኔ ፡ ራቁ ፡ ሸንግላውን ፡ የምትሰሩ ፡ ሁሉ ፡
እግዚአብሔር ፡ የልቅሶዬን ፡ ቃል ፡ ሰምትዋልና ፡፡
፱፡ እግዚአብሔር ፡ ማዘኔን ፡ ሰምትዋል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ጸሎቴን ፡ ይቀበላል ፡፡
፲፡ ይፈሩ ፡ እጅግም ፡ ይጉስቍሉ ፡ ጸላቶቼ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ይመለሱ ፡ ድንገትም ፡ ይፈሩ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፯፡

፩፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ባንተ ፡ አመንሁ ፡፡
ካሳደጀ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝና ፡ ታደገኝ ፡፡
፪፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ነፍሴን ፡ እንዳይነጥቅ ፡
አንደይቀደትም ፡ የሚታደግ ፡ ሳይኖር ፡፡
፫፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እንደይህስ ፡ ካደረግሁ ፡
ግፍም ፡ በጄ ፡ ቢኖር ፡፡
፬፡ ቸር ፡ በነበሩልኝ ፡ ክፉን ፡ ከመለስሁባቸው ፡
(በከንቱ ፡ የሚጠላኝን ፡ አደንሁ ፡ እንጅ ፡፡)
፭፡ ጸላት ፡ ነፍሴን ፡ ያሳድድ ፡ ያግኛትም ፡
ሕይወቴንም ፡ በምድር ፡ ጥሎ ፡ ይርገጣት ፡
ክብሬንም ፡ በመሬት ፡ ያጉስቍለው ፡፡

፮ ቁም ፡ አቤቱ ፡ በቍጣኽ ። በጸላቶቼም ፡ መዓት ፡ ላይ ፡
ተነሣ ።
ተነሣልኝም ፡ ባዘዝኸው ፡ ፍርድ ።
፯ የሰዎችም ፡ ጉባዔ ፡ ወደንተ ፡ ትሰበሰባለች ።
ስለዚኽም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ተመለስ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ አሕዛብን ፡ ይፈርዳል ።
ፍረድልኝ ፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ጽድቁ ፡ እንደ ፡ ቅንነቴም ።
፱ የኃጥአን ፡ ክፋት ፡ ይጥፋ ፡ ጻድቁን ፡ ግን ፡ አቅና ።
ጻድቅ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልቦችንና ፡ ኵላሊቶችን ፡ ይመረም
ራልና ።
፲ ጋሻዬ ፡ ልበ ፡ ቅኖችን ፡ በሚያድናቸው ፡
በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ፈራጅ ፡ ነው ።
ሁለግዜም ፡ የሚቈጣ ፡ አምላክ ፡ ነው ።
፲፪ ሰው ፡ ባይመለስ ፡ ሰይፉን ፡ ያስላል ፡
ቀስቱንም ፡ ገተረ ፡ ያቀናዋልም ፡
፲፫ የሞትንም ፡ እቃ ፡ አዘጋጀለት ፡
ፍላፆቹንም ፡ ሊያናድዱ ፡ አደረገ ።
፲፬ እነሆ ፡ ክፋትን ፡ አረገዘ ፡ ድካምንም ፡ ፀነሰ ፡
አሰትንም ፡ ይወልዳል ።
፲፭ ጕድጓድን ፡ ማሰና ፡ ቈፈረ ።
ባደረገውም ፡ አዘቅት ፡ ይወድቃል ።
፲፮ ድካሙ ፡ በራሱ ፡ ይመለሳል ፡
ባናቱ ፡ ላይም ፡ ግፉ ፡ ትወርዳለች ።
፲፯ እግዚአብሔርን ፡ እንደ ፡ ጽድቁ ፡ መጠን ፡ አመሰግናለሁ ።
ለልዑልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እዘምራለሁ ።

መዝሙር ፡ ፰

፩ አቤቱ ፡ ጌታችን ፡ ስምኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደገርማል ፡ በም
ድር ፡ ሁሉ ።
ምስጋናኽን ፡ በሰማዮች ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግኽ ።



፪ ከሕፃናት ፡ አፍ ፡ ከሚጠቡም ፡ ኃይልን ፡ አዘጋጀኽ ፡ ስ
ለ ፡ ጸላቶችኽ ።
ጸላትንና ፡ በቀለኛን ፡ ዝም ፡ ለማሰኘት ።
፫ ሰማዮችህን ፡ የጻቶችኽን ፡ ስራ ፡ አያለሁና ፡
ጨረቃውንም ፡ ከዋክብትንም ፡ አንተ ፡ የሠራኻቸውን ።
፬ ምንድር ፡ ነው ፡ ሰው ፡ ታስበው ፡ ዘንድ ፡
የሰው ፡ ልጅም ፡ ትጐበኘው ፡ ዘንድ ።
፭ እግዚአብሔርንም ፡ ጥቂት ፡ አሳጣኸው ፡
በክብርና ፡ በጌጽም ፡ ትከለዋለህ ።
፮ በጀችኽ ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሾመዋለህ ።
ከግሮቹ ፡ በታች ፡ ሁሉን ፡ አስገዛኽለት ፡
፯ በጎችን ፡ ላሞችን ፡ ሁሉ ፡
ደግሞም ፡ የምድረ ፡ በደውን ፡ እንስሶች ፡
፰ የሰማይንም ፡ ዎፎች ፡ የባሕርንም ፡ ዓሦች ፡
የባሕርንም ፡ መንገድ ፡ አላፊውን ፡ ሁሉ ።
፱ አቤቱ ፡ ጌታችን ፡ ስምኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደገርማል ፡ በም
ድር ፡ ሁሉ ።

ሁለተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፱

፩ እግዚአብሔርን ፡ በልቤ ፡ ሁሉ ፡ አመሰግናለሁ ፡
ተአምራትኽንም ፡ ሁሉ ፡ እነግራለሁ ።
፪ ባንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሐሤትም ፡ አደርጋለሁ ፡
ለስምኽም ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ እዘምራለሁ ።
፫ ጸላቶቼ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡
ይሰናከላሉ ፡ ከበፊትኽም ፡ ይጠፋሉ ።
፬ ፍርዴንና ፡ ቅኔን ፡ አድርገኽልኛልና ።
በዙፋንኽ ፡ ላይ ፡ ተቀመጥኽ ፡ የጽድቅ ፡ ፈራጅ ።
፭ አሕዛብን ፡ ዘለፍኽ ፡ ረሲዓንንም ፡ አጠፋኽ ።
ስማቸውንም ፡ ለዘላለም ፡ ፋቅህ ።

፮ ጸላት : ሆይ : ፈጽመኽን : ለማፍረስ : ጨረስኽ :
ከተሞችንም : አፈረስኽ ፡፡
ዝክራቸውም : ባንድ : ጠፋ ፡፡
፯ እግዚአብሔር : ግን : ለዘላለም : ይቀመጣል ፡፡
ዙፋኑንም : ለመፍረድ : አዘጋጀ ፡፡
፰ እርሱም : ዓለምን : በጽድቅ : ይፈርደል :
ሰዎችንም : በቅን : ይደኛል ፡፡
፱ እግዚአብሔርም : ለችጋረኞች : መጸጊ : ሆናቸው ፡፡
እርሱም : መጸጊቸው : ለመከራቸው : ጊዜ : ሁሉ ፡፡
፲ ስምኽን : የሚያውቁ : ባንተ : ያምናሉ ፡፡
የሚሹህን : አተዋቸውምና : አቤቱ ፡፡
፲፩ በፅዮን : ለሚኖር : ለእግዚአብሔር : ዝመሩ ፡፡
በአሕዛብም : አደራረጉን : ንገሩ ፡፡
፲፪ በሚመረምርበት : ጊዜ : ደማቸውን : አስብዋልና :
የችጋረኞችን : ጩኸት : አይረሳምና ፡፡
፲፫ እዘንልኝ : አቤቱ :
ጸላቶቼም : የሚያመጹብኝን : መከራ : እይ ፡፡
ከሞት : ደጅ : ከፍ : ከፍ : የምታደርገኝ ፡፡
፲፬ ምስጋናኽን፡ሁሉ፡በፅዮን፡ልጅ፡በደጅዋ፡እነግር፡ዘንድ ፡፡
፲፭ በማደንኽ : ደስ : ይለኛል ፡፡
ወደቁ : አሕዛብ : በሰሩት : ጉድጓድ :
በዚያችም : በሸሸጊት : ወጽመድ : እግራቸው : ተጸመደች ፡፡
፲፮ እግዚአብሔር : ፍርድን : በማደረግ : ይታወቃል ፡፡
በጆቹ : ስራ : ኃጢአተኛው : ተጸመደ ፡፡
፲፯ ወደ : ሲኦል : ይመለሳሉ : ረሲዓን :
እግዚአብሔርንም : የሚረሱ : አሕዛብ : ሁሉ ፡፡
፲፰ ችጋረኛ : ለዘላለም : አይረሳምና :
የደካሞችም : ተስፋ : ለዘላለም : አትጠፋም ፡፡
፲፱ ተነሣ : አቤቱ : ሰው : እንደይበረታ :
አሕዛብም : በፊትኽ : ይፈረድባቸው ፡፡
፳ ፍርሃትን : ስጣቸው : አቤቱ ፡፡
አሕዛብ : ሰዎች : እንደ : ሆኑ : ያውቁ : ዘንድ ፡፡



## መዝሙር : ፲

፩ ለምን : አቤቱ : ርቀኽ : ትቆማለኽ :
በመከራም : ጊዜ : ትሰወራለኽ ።
፪ በኃጢአተኛ : ትዕቢት : ችጋረኛ : ይቃጠላል ።
ባሰቡት : ተንኰላቸው : ይጸመዱ ።
፫ ኃጢአተኛ : በነፍሱ : ፈቃድ : ይመሰገናልና :
ግፈኛውንም : ባርኮ : እግዚአብሔርን : ናቀ ።
፬ ኃጢአተኛ : በትዕቢቱ : ቍጣ : አይጠይቅም :
እግዚአብሔርም : ባሳቡ : ሁሉ : የለም ።
፭ መንገዱ : ሁለጊዜ : የረከሰ : ነው :
ፍርድኽ : ከፍ : ከፍ : ብሎ : ከፊቱ : ተሰወረ :
ጸላቶቹንም : ሁሉ : ይንቃል :
፮ በልቡ : አልታወክም : ይላል :
ለልጅ : ልጅም : ክፉ : አያገኘኝም ።
፯ አፉ : መርገምና : ሽንግላ : ምሉ : ነው :
ከመላሱ : በታች : ድካምና : መከራ : ነው ።
፰ በመንደር : መሸመቅያ : ይቀመጣል :
በመሰወርዮችም : ንጹሑን : ይገድላል ።
ዓይኖቹም : ወደ : ችጋረኛ : ይመለከታሉ :
፱ በስውር : ይሸምቃል : እንደ : አንበሳ : በጉድጓዱ :
ችጋረኛን : ለመንጠቅ : ይሸምቃል :
ችጋረኛውንም : በወጽመዱ : ይነጥቀዋል ።
፲ ይጐበጣል : ይወድቃልም : በኃያላኑም : እጅ : በችጋረኞ
ች : ላይ : ይወድቃል ።
፲፩ በልቡም : እግዚአብሔር : ረሳ : ይላል ።
ፊቱን : ሰወረ : ከቶ : እንደያይ ።
፲፪ ተነሣ፡እግዚአብሔር፡አምላክ፡ሆይ፡እጅኽንም፡አንሣ።
ችጋረኞችንም : አትርሳ ።
፲፫ ኃጢአተኛ : ስለ : ምን : ናቀ : እግዚአብሔርን ።
በልቡ : አትመራመረውም : አለ ።
፲፬ አየኸው : አንተ : ክፋትንና : ቍጣውን : ታያለኽና : በ
ጅኽ : እንድትሰጠው ።

ባንተ ፡ ተጣለ ፡ ችጋረኛ ። አባት ፡ እናትም ፡ ለሌለው ፡ አን
ተ ፡ ረዷ ፡ ነህ ።
፲፭፤ የኃጢአተኛን ፡ የክፉንም ፡ ክንድ ፡ ስበር ።
የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኃጢአቱን ፡ ትመረምራለኽ ፡ አታገኝምም ።
፲፮፤ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ።
አሕዛብ ፡ ከምድሩ ፡ ጠፉ ።
፲፯፤ የችጋረኞችን ፡ መሻት ፡ ሰማኽ ፡ አቤቱ ፡
ልባቸውን ፡ ታቀናለኽ ፡ ጆሮኽም ፡ ታደምፃለች ፡
፲፰፤ አባት ፡ እናትም ፡ ለሌለው ፡ ፍርዲ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡
የምድር ፡ ሰው ፡ እንጊዴህ ፡ መኰራቱን ፡ እንዳይጨምር ።

መዝሙር ፡ ፲፩፤

፩፤ በእግዚአብሔር ፡ አመንሁ ።
እንዴት ፡ ነፍሴን ፡ ተቅበዝብዢ ፡ ትላላችሁ ።
እንደ ፡ ተራራችሁ ፡ ዎፍ ።
፪፤ ኃጢአተኞች ፡ እነሆ ፡ ቀስታቸውን ፡ ገትረዋልና ፡
ፍላፃቸውንም ፡ ባውታር ፡ አዘጋጅተዋልና ፡
ልበ ፡ ቅኖችን ፡ በስውር ፡ ይነድፉበት ፡ ዘንድ ።
፫፤ መሠረት ፡ ፈርሰዋልና ። ጻድቁም ፡ ምን ፡ ያደርጋል ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ በመቅደሱ ፡ ሀይከል ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ዙፋኑ ፡ በሰማይ ፡ ነው ። ዓይኖቹ ፡ ያያሉ ፡
ቅንድቦቹም ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ይመረምራሉ ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ ጻድቁን ፡ ይመረምራል ፡
ኃጥኡን ፡ ግን ፡ የግፉንም ፡ ወዳጅ ፡ ነፍሱ ፡ ጸላች ።
፮፤ በኃጥአን ፡ ላይ ፡ ወጽመድን ፡ ያዘንባል ፡
እሳትንም ፡ ዲንንምም ፡ ዓውሎ ፡ ንፋስንምም ፡ የጽዋቸ
ው ፡ ፈንታ ፡ ሊሆን ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ሁንዋልና ፡ ጽድቅን ፡ ይወዳል ።
ቅን ፡ ነገርን ፡ ፊቱ ፡ ትመለከታለች ።



የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፲፪፤

፩፤ አድን ፡ አቤቱ ፡ ቅዱስ ፡ አልቋልና ፡
ከሰው ፡ ልጆችም ፡ ምእምናን ፡ ተፈጅተዋልና ።
፪፤ እርሱ ፡ በርሳቸው ፡ ምናምን ፡ ይናገራሉ ፡
በሽንግላ ፡ ከንፈር ፡ ይናገራሉ ፡ የሁለት ፡ ልብም ፡ ሁነው ።
፫፤ የሽንግላን ፡ ከንፈር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቈርጣል ፡
ነገርንም ፡ ታላቅ ፡ የምታረገውን ፡ መላስ ።
፬፤ "በመላሳችን ፡ እንበርታ" ፡ የሚሉትን ። "ከንፈራችን ፡
የኛ ፡ ነውና ፡
ጌታችን ፡ ማነው" ፡ ብለው ።
፭፤ ስለ ፡ ችጋረኞች ፡ መጥፋት ፡ ስለ ፡ ድኆችም ፡ ልቅሶ ፡
ዛሬ ፡ እነሣለሁ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
በላዩ ፡ ከተነፈበትም ፡ መድኃኒትን ፡ አደርግለታለሁ ።
፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ቃላት ፡ የንጹ ፡ ቃላት ፡ ናቸው ፡
በምድር ፡ መቅለጫ ፡ እንደ ፡ ተፈተነ ፡ ብር ፡
ሰባት ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጸሬ ።
፯፤ አንተ ፡ አቤቱ ፡ ጠብቃቸው ፡
ከዚችም ፡ ትውልድ ፡ ለዘላለም ፡ ጠብቀው ።
፰፤ ክፎች ፡ በዙርያው ፡ ይመላለሳሉ ፡
የምናምን ፡ ልጆች ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ።

መዝሙር ፡ ፲፫፤

፩፤ እስከ ፡ መቸ ፡ አቤቱ ፡ ትረሳኛለኽ ። ለፍጻሜን ።
እስከ ፡ መቸ ፡ ፊትኽን ፡ ከኔ ፡ ትሰውራለኽ ።
፪፤ እስከ ፡ መቸ ፡ በነፍሴ ፡ እመካከራለሁ ፡
ጻዕርስ ፡ በልቤ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይሆናል ።
እስከ ፡ መቸ ፡ በላዬ ፡ ጸላቴ ፡ ይጓደዳል ።
፫፤ እየኝ ፡ ስማኝም ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ።
ዓይኖቼን ፡ አብራ ፡ ለሞት ፡ እንዳይተኙ ።
፬፤ ጸላቴም ፡ አሸነፍሁት ፡ እንዳይል ።
የሚያሳዝኑኝም ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፡ ብታወክ ።

፭፤ እኔስ ፡ በምሕረትኽ ፡ ታመንሁ ፡
ልቤም ፡ በመድኃኒትኽ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡፡
፮፤ ለእግዚአብሔርም ፡ እቀኛለሁ ፡ ምሕረት ፡ አድርጎልኛ
ልና ፡፡

መዝሙር ፡ ፲፬፤

፩፤ ሰነፍ ፡ በልቡ ፡ አምላክ ፡ የለም ፡ አለ ፡፡
ስራውን ፡ አጠፉ ፡ አረከሱም ፡
በጎ ፡ ነገር ፡ የሚሰራ ፡ የለም ፡፡
፪፤ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ተመለከተ ፡
የሚያስተውል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የሚሻ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡
ያይ ፡ ዘንድ ፡፡
፫፤ ሁሉ ፡ ዓመፁ ፡ ባንድም ፡ ረከሱ ፡፡
በጎን ፡ ሰሪ ፡ የለም ፡፡ የለም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡፡
፬፤ በውኑ ፡ አያስተውሉምን ፡ ግፍን ፡ አድራጎች ፡ ሁሉ ፡
ሕዝቤን ፡ እንደ ፡ እንጀራ ፡ የሚበሉ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ግን ፡ አልጸረኑትም ፡፡
፭፤ ከዚያ ፡ በታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ ፈሩ ፡
እግዚአብሔር ፡ በጻድቅ ፡ ትውልድ ፡ ነውና ፡፡
፮፤ የችጋረኛን ፡ ምክር ፡ አሳፈራችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ ተስፋው ፡ ነውና ፡፡
፯፤ ማን ፡ ይሰጣል ፡ መድኃኒት ፡ ከፅዮን ፡ ለእሥራኤል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ የሕዝቡን ፡ ምርኮ ፡ ሲመልስ ፡ ጊዜ ፡
ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ እሥራኤልም ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ፡፡

ሶስተኛ ፡ ቀን ፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፲፭፤

፩፤ አቤቱ ፡ በድንኳንኽ ፡ ማን ፡ ያድራል ፡
በተቀደሰም ፡ ተራራህ ፡ ማን ፡ ይኖራል ፡፡
፪፤ በቅንነት ፡ የሚሔድ ፡ ጽድቅንም ፡ የሚያደርግ ፡



በልቡም ፡ እውነት ፡ የሚናገር ፡፡
፫፤ በመላሱ ፡ ያልረገጠ ፡ በባልንጀራውም ፡ ክፉ ፡ ያላደረገ ፡
ዘመዱንም ፡ ያልሰደበ ፡፡
፬፤ ቸልተኛ ፡ በፊቱ ፡ የተናቀለት ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የሚ
ፈሩቱን ፡ የሚያከብር ፡፡
ለባልንጀራው ፡ ምሎ ፡ የማይከዳ ፡፡
፭፤ ብሩን ፡ ባራጻ ፡ ያላበደረ ፡
በንጹሕ ፡ ላይም ፡ መማለጃውን ፡ ያልተቀበለ ፡፡
እንዲህ ፡ የሚያደርግ ፡ ለዘላለም ፡ አይታወክም ፡፡

መዝሙር ፡ ፲፮፤

፩፤ ጠብቀኝ ፡ አቤቱ ፡ ባንተ ፡ ታምኛለሁና ፡፡
፪፤ ነፍሴ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አንተ ፡ ጌታዬ ፡ ነኽ ፡ አለች ፡
በጐነቴ ፡ ወደንተ ፡ አትደርስም ፡፡
፫፤ በምድር ፡ ባሉ ፡ በቅዱሳን ፡ በተመሰገኑም ፡
ፈቃዴ ፡ ሁሉ ፡ በርሳቸው ፡ ነው ፡፡
፬፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ ለሚፈጥኑ ፡ ድካማቸው ፡ ይብዛ ፡
የቍርባናቸውን ፡ ደም ፡ አላፈሰውም ፡
ስማቸውንም ፡ በከንፈሮቼ ፡ አልጠራም ፡፡
፭፤ እግዚአብሔር ፡ የጕልቴ ፡ ፈንታ ፡ ጽዋዬም ፡ ነው ፡፡
አንተ ፡ ዕፃዬን ፡ የምታጸና ፡ ነህ ፡፡
፮፤ ገመድ ፡ ባመረ ፡ ስፍራ ፡ ወደቀችልኝ ፡
ርስቴም ፡ ቀናችልኝ ፡፡
፯፤ የመከረኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አባርካለሁ ፡፡
ደግሞ ፡ ሌትም ፡ ይገሥጹኛል ፡ ኵላሊቶቼ ፡፡
፰፤ ሁለግዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፊቴ ፡ አኖርሁ ፡
በቀኜ ፡ ነውና ፡ አልታወክም ፡፡
፱፤ ስለዚህ ፡ ልቤ ፡ ደስ ፡ አለው ፡ክብሬም ፡ እልል ፡ አለች ፡
ሥጋዬም ፡ ደግሞ ፡ በምነት ፡ ታድራለች ፡፡
፲፤ ነፍሴን ፡ ለሢኦል ፡ አትተዋትምና ፡
ጻድቅኽንም ፡ ጥፋትን ፡ ለማየት ፡ አትሰጥምና ፡፡
፲፩፤ የሕይወትን ፡ መንገድ ፡ ታስታውቀኛለኽ ፡፡

በፊትኽ ፡ የደስታ ፡ ጽጋብ ፡ ነው ፡
ሥምረትም ፡ በቀኝኽ ፡ ለዘላለም ።

## መዝሙር ፡ ፲፯፡

፩፡ አቤቱ ፡ ጽድቅን ፡ ስማት ፡ ጩኸቴንም ፡ አድምፅ ።
ጸሎቴን ፡ አድምፀኝ ፡ በተንኰለኛ ፡ ከንፈር ፡ ያልሆነውን ።
፪፡ ከፊትኽ ፡ ፍርዴ ፡ ይውጣ ። ዓይኖችኽም ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ይዩ ።
፫፡ ልቤን ፡ ፈተንኸው ፡ በሌት ፡ ጐበኘኸው ፡
ነጠርሀኝ ፡ አታገኝብኝም ።
አፌ ፡ እንዳይተላለፍ ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ።
፬፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ስራ ፡ ሁሉ ፡ በከንፈርኽ ፡ ነገር ፡
እኔ ፡ ካጥፊ ፡ መንገድ ፡ ተጠበቅሁ ።
፭፡ ፍለጎቼን ፡ በመንገድኽ ፡ አጽና ፡ ሰኰናዬ ፡ እንዳይናወጥ ።
፮፡ እኔ ፡ ጸራሁኽ ፡ አቤቱ ፡ ሰምተኸኛልና ፡
ወደኔ ፡ ጆሮኽን ፡ ጣል ፡ ቃሌንም ፡ ስማኝ ።
፯፡ ምሕረትኽን ፡ ግለጸው ፡ የሚያምኑኽን ፡ የምታድናቸው ፡
ቀኝኽን ፡ ከሚቃወሙ ።
፰፡ እንደ ዐይን ፡ ብሌን ፡ ጠብቀኝ ።
በክንፎችኽ ፡ ጽላ ፡ ሰውረኝ ።
፱፡ ከሚያስጨንቁኝ ፡ ከኃጥኣን ፡ ፊት ።
ጸላቶቼ ፡ ሰውነቴን ፡ ይከብዋታል ።
፲፡ አንጀታቸውን ፡ በስብ ፡ ቋጸሩ ፡
አፈቸውም ፡ ትዕቢት ፡ ተናገረ ።
፲፩፡ አሁንም ፡ መሒጃችነን ፡ ከበቡ ።
ዓይናቸውን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረጉ ፡
፲፪፡ ለመንጠቅ ፡ እንደሚናፈቅ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
እንደንበሳም ፡ ደቦል ፡ ተሸምቆ ፡ እንደምኖር ።
፲፫፡ ተነሣ ፡ አቤቱ ፡ ቀድመህ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ጣለው ፡
ሰውነቴን ፡ ከኃጢአተኛ ፡ በሰይፍኽ ፡ አድናት ።
፲፬፡ አቤቱ ፡ ከጅኽ ፡ ሰዎች ፡ አድነኝ ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰዎች ፡ ፈንታቸው ፡ በሕይወታቸው ፡ ያለች ።
ከሰወርኸው ፡ ከብትኽ ፡ ሆደቸውን ፡ አጸገብኽ ።



ልጆቻቸው ፡ በዙ ። የተረፈቸውንም ፡ ለሕፃናታቸው ፡ ያተር
ፈሉ ።
፲፭፡ እኔ ፡ ግን ፡ በጽድቅ ፡ ፊትኽን ፡ አያለሁ ።
በምሳሌኽም ፡ ተነሥቼ ፡ እጸግባለሁ ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፲፰፡

፩፡ አቤቱ ፡ ጕልበቴ ፡ እወድኻለሁ ።
፪፡ እግዚአብሔር ፡ ደንጊያዬ ፡ አምባዬም ፡ መድኃኒቴም ፡
አምላኪም ፡ አምባዬም ፡ በርሶ ፡ ያምንሁ ፡
ጋሻዬም ፡ የረዴቴም ፡ ቀንድ ፡ መጸጃዬም ።
፫፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፡ እጸራውማለሁ ፡
ከጸላቶቼም ፡ እድናለሁ ።
፬፡ የሞት ፡ ማሠርያ ፡ ያዘኝ ፡ የብልያልም ፡ ፍሳሽ ፡ አወከኝ ።
፭፡ የሢኦልም ፡ ማሠርያ ፡ ከበበኝ ።
የሞትም ፡ ወጽመድ ፡ ደረሰብኝ ።
፮፡ በጨነቀኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጸራለሁ ፡
ወደ ፡ አምላኪም ፡ እጮኻለሁ ፡
ከመቅደሶም ፡ ቤት ፡ ቃሌን ፡ ይሰማል ፡
በፊቱም ፡ ጩኸቴ ፡ ወደ ፡ ጆሮው ፡ ይገባል ።
፯፡ ምድርም ፡ ተንቀጠቀጠች ፡ ተንበደበደችም ፡
የተራሮችም ፡ መሠረቶች ፡ ተነቀነቁ ፡
እግዚአብሔርም ፡ ተቈጥትዋልና ፡ ተንቀጠቀጡ ።
፰፡ ጢስ ፡ ካፍንጫው ፡ ወጣ ፡ ካፉም ፡ የሚበላ ፡ እሳት ፡
ፍምም ፡ ከርሶ ፡ ተፈጀ ።
፱፡ ሰማዮችን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረገ ፡ ወረደም ፡
ጽጋግም ፡ ከግሩ ፡ በታች ፡ ነበረ ።
፲፡ በኪሩቢልም ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ፡ በረረም ፡
በንፋስ ፡ ክንፍም ፡ ሰፈፈ ፡ አለ ።
፲፩፡ መሰወርያውን ፡ ጨለማ ፡ አደረገ ፡
በዙርያውም ፡ የነበረ ፡ ጎጆ ፡ የውኆች ፡ ጨለማ ፡ የሰማይ
ም ፡ ደመናት ፡ ነበር ።

፲፪ ከፊቱ ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፡ ደመናት ፡ አለፉ ፡፡
በረደም ፡ የሳትም ፡ ፍም ፡፡
፲፫ እግዚአብሔርም ፡ በሰማዮች ፡ አንጐደጐደ ፡
ልዑልም ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ፡
በረደውንም ፡ የሳትንም ፡ ፍም ፡፡
፲፬ ፍላፃውንም ፡ ሰደደ ፡ በተናቸውም ፡
መብረቆችን ፡ አበዛ ፡ አወካቸውም ፡፡
፲፭ የውኆችም ፡ ፈሳሾች ፡ ታዩ ፡
የዓለምም ፡ መሠረቶች ፡ ተገለጹ ፡
ከዘለፋኽ ፡ የተነሣ ፡ አቤቱ ፡ ከመዓትኽም ፡ መንፈስ ፡ እስ
ትንፋስ ፡፡
፲፮ ከከፍታውም ፡ ሰደደ ፡ ወሰደኝም ፡
ከብዙ ፡ ውኆችም ፡ አወጣኝ ፡፡
፲፯ ከብርቱ ፡ ጸላቴ ፡ አደነኝ ፡
ከሚጸሉኝም ፡፡ በርትተውብኛልና ፡፡
፲፰ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ቀደሙኝ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ መድገፊያዬ ፡ ሆነኝ ፡፡
፲፱ ወደ ፡ ሰፊ ፡ ስፍራም ፡ አወጣኝ ፡፡ ወዶኝማልና ፡ረዳኝ ፡፡
፳ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ይከፍልለኛል ፡
እንደ ፡ እጄ ፡ ንጽሕናም ፡ ይመልስልኛል ፡፡
፳፩ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ጠብቂያለሁና ፡
በአምላኬም ፡ አላመፃሁም ፡፡
፳፪ ፍርዱ ፡ ሁሉ ፡ በፊቴ ፡ ነውና ፡
ትእዛዛቱንም ፡ ከኔ ፡ አላርቅም ፡፡
፳፫ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ቀናሁ ፡
ከኃጢአቴም ፡ ተጠበቅሁ ፡፡
፳፬ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ይመልስለኛል ፡
እንደ ፡ እጄም ፡ ንጽሕና ፡ ባይኖቹ ፡ ፊት ፡፡
፳፭ ከቅዱሳን ፡ ጋራ ፡ ቅዱስ ፡ ነኽ ፡
ከቀና ፡ ሰውም ፡ ጋራ ፡ ትቀናለህ ፡፡
፳፮ ከንጹሕም ፡ ጋራ ፡ ንጹሕ ፡ ነኽ ፡
ከጠማማም ፡ ጋራ ፡ ትጠመዝዛለኽ ፡፡



፳፯ አንተ ፡ የተጠቃን ፡ ሕዝብ ፡ ታድናለኽና ፡
የትዕቢተኞችን ፡ ዓይኖች ፡ ግን ፡ ታዋርዳለኽ ፡፡
፳፰ አንተ ፡ መብራቴን ፡ ታበራለኽና ፡
እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ጨለማዬን ፡ ያበራል ፡፡
፳፱ ባንተ ፡ ጭፍራን ፡ አሸንፋለሁና ፡
በአምላኬም ፡ ግድግደን ፡ እዘላለሁ ፡፡
፴ ያምላክ ፡ መንገድ ፡ የቀና ፡ ነው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
በእሳት ፡ ጸሪ ፡፡
እርሱን ፡ ለሚታመኑ ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ጋሻ ፡ ነው ፡፡
፴፩ ማነው ፡ አምላክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡
መጸጊስ ፡ ማነው ፡ አምላካችን ፡ እንጂ ፡፡
፴፪ ኃይል ፡ የሚያስታጥቀኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
መንገዴንም ፡ የሚያቀና ፡
፴፫ እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ብሆር ፡ እግሮች ፡ የሚያቀና ፡
በኮረፍቶቼም ፡ የሚያቆመኝ ፡፡
፴፬ እጆቼን ፡ ሰልፍን ፡ ያስተምራል ፡
በክንዴም ፡ የናስ ፡ ቀስት ፡ ተሰብርዋል ፡፡
፴፭ የመድኃኒትኽንም ፡ ጋሻ ፡ ሰጠኸኝ ፡
ቀኝኽም ፡ ታጸናኛለች ፡ ምሕረትኽም ፡ ታበዛኛለች ፡፡
፴፮ አርጋገጤን ፡ በታቼ ፡ ታሰፋለኽ ፡
ቍርጭምጭሚቴ ፡ እንዳይናወጥ ፡፡
፴፯ ጸላቶቼን ፡ እከተላለሁ ፡ እይዛቸውማለሁ ፡
ሳልፈጃቸውም ፡ አልመለስም ፡፡
፴፰ እስጨንቃቸዋለሁ ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ፡፡
፴፱ ከግሬ ፡ በታች ፡ ይወድቃሉ ፡፡
ኃይልን ፡ ታስታጥቀኛለኽና ፡ ለዘምቻ ፡፡
በላዬ ፡ የቆሙትን ፡ ሁሉ ፡ በታቼ ፡ ትጥላለህ ፡፡
፵ የጸላቶቼንም ፡ ጀርባ ፡ ሰጠኸኝ ፡
የሚጸሉኝንም ፡ ዝም ፡ አሰኛቸዋለሁ ፡፡
፵፩ ይጮሃሉ ፡ የሚረዳቸውም ፡ የለም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ አይሰማቸውምም ፡፡
፵፪ እንደ ፡ መሬት ፡ በነፋስ ፡ ፊት ፡ እፈጫቸዋለሁ ፡

እንደደባባይም ፡ ጭቃ ፡ አረግጻቸዋለሁ ።
፵፫፡ ከሕዝብ ፡ ክርክር ፡ ታድነኛለኽ ፡
የአሕዛብንም ፡ ራስ ፡ አድርገኽ ፡ ትሾመኛለኽ ።
የማላውቃት ፡ ሕዝብም ፡ ትገዛልኛለች ።
፵፬፡ በጆሮ ፡ መስማት ፡ ተገዙልኝ ።
የልዩ ፡ ልጆች ፡ ባሰት ፡ ተናገሩኝ ።
፵፭፡ የልዩ ፡ ልጆች ፡ ደከሙ ፡
ከተቈለፈችምም ፡ ከተማቸው ፡ ፈርተው ፡ ሸሹ ።
፵፮፡ እግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ፡ መጸጀዬም ፡ ቡሩክ ፡ ነው ፡
የመድኀኒቴም ፡ አመላክ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፵፯፡ በቀሌን ፡ የሚመልስልኝ ፡ አምላክ ፡
አሕዛብንም ፡ በታቼ ፡ ያስገዛል ።
፵፰፡ ከጸላቶቼ ፡ የሚያድነኝ ፡ እርሱ ፡ ነው ፡
በኔም ፡ ከቆሙብኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርገኛለኽ ፡
ከበደለኛ ፡ ሰው ፡ አደንኽኝ ።
፵፱፡ ስለዚህ ፡ አመሰግንኻለሁ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አቤቱ ፡
ለስምኽም ፡ እዘምራለሁ ።
፶፡ የንጉሡን ፡ መድኀኒት ፡ ታላቅ ፡ የምታደርግ ፡
ምሕረትህንም ፡ ለመሢሕኽ ፡ ያደረግኽ ፡
ለደዊት ፡ ለዘሩም ፡ ለዘላለም ።

አራተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፲፰፡

፩፡ ሰማዮች ፡ የአምላክን ፡ ምስጋና ፡ ይናገራሉ ፡
የሰማይም ፡ ጠፈር ፡ የጆቹን ፡ ስራ ፡ ያወራል ።
፪፡ ቀን ፡ ለቀን ፡ ነገርን ፡ ታወፃለች ፡
ሌትም ፡ ለሌት ፡ ዕውቀትን ፡ ትናገራለች ።
፫፡ ነገር ፡ የለም ፡ መናገርም ፡ የለም ፡
ቃላቸው ፡ ያልተሰማበት ።



፬፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወፃ ፡ ገመዳቸው ፡
እስከ ፡ ዓለም ፡ ዳርቻም ፡ ነገራቸው ።
ለፀሐይም ፡ ድንኳንን ፡ አኖረባቸው ።
፭፡ እርሱም ፡ እንደ ፡ ሙሽራ ፡ ከልፍኙ ፡ ይወጣል ።
እንደ ፡ ኀያልም ፡ መንገዱን ፡ ለመሮጥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፮፡ ከሰማዮች ፡ ዳርቻ ፡ መውጣቱ ፡ ነው ፡
መግባቱም ፡ ወደ ፡ ዳርቻቸው ፡ ይላል ፡
ከሙቀቱም ፡ የሚሰወር ፡ የለም ።
፯፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ፍጹም ፡ ነው ፡
ነፍስንም ፡ ይመልሳል ።
የእግዚአብሔር ፡ ምስክር ፡ የታመነ ፡ ነው ፡
ሕፃናትንም ፡ ጠቢባን ፡ ያደርጋል ።
፰፡ የእግዚአብሔር ፡ ሥርዓት ፡ የቀና ፡ ነው ፡
ልብንም ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።
የእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝም ፡ ጽሩ ፡ ነው ፡
ዓይንንም ፡ ያበራል ።
፱፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፡
ለዘላለሙም ፡ ይኖራል ።
የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ እውነትና ፡ ጽድቅ ፡ ባንድ ፡ ነው ።
፲፡ እጅግ ፡ ከሚጸራ ፡ ከወርቅ ፡ ይልቅ ፡ ይወደደል ።
ከማር ፡ ከማርም ፡ ወለላ ፡ ነጠብጣብ ፡ ይጣፍጣል ።
፲፩፡ ባርያኽ ፡ ደግሞ ፡ በርሱ ፡ ይገሠፃል ።
እርሱንም ፡ በመጠበቅ ፡ እጅግ ፡ ጥቃሜ ፡ ይገኛል ።
፲፪፡ ስሕተቱን ፡ ማን ፡ ያስተውላታል ።
ከተሰወረው ፡ ኀጢአቴ ፡ አንጻኝ ።
፲፫፡ ከዕቡያንም ፡ ባርያኽን ፡ ጠብቅ ፡ እንዳይገዙብኝ ፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ቀንቼ ፡ እሆናለሁ ፡
ከታላቁም ፡ ኀጢአት ፡ እነጻለሁ ።
፲፬፡ ያፌ ፡ ነገር ፡ በፊትኽ ፡ ያማረ ፡ ይሁን ፡ የልቤም ፡ አሳብ ፡
አቤቱ ፡ አምባዬ ፡ መድኀኒቴም ።

## መዝሙር ፡ ፳

፩፡ በመከራ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስማኽ ፡
የያዕቆብ ፡ አምላክም ፡ ስም ፡ ያንሣኽ ።
፪፡ ከመቅደሱ ፡ ረድኤትን ፡ ይላክልኽ ፡
ከፅዮንም ፡ ያጽናኽ ።
፫፡ ቍርባንህን ፡ ሁሉ ፡ ያስብልኽ ፡
መሥዋዕትንም ፡ ያለምልምልኽ ።
፬፡ እንደ ፡ ልብኽ ፡ ይስጥኽ ፡
ምክርኽንም ፡ ሁሉ ፡ ይፈጽምልኽ ።
፭፡ በመድኃኒትኽ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡
በአምላካችነም ፡ ስም ፡ ባደረቅ ፡ እናነሣለን ።
ልመናኽን ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈጽምልኽ ።
፮፡ ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቀብቶ ፡ ያነገሠውን ፡ እንደ ፡ ደነው ፡ አወቅሁ ።
ከሰማይ ፡ መቅደሱ ፡ ይመልስለታል ፡ በቀኙ ፡ ማደን ፡ ብርታት ።
፯፡ እሌህ ፡ በሠረገላ ፡ እልያም ፡ በፈረስ ፡
እኛ ፡ ግን ፡ ባምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እናሳስባለን ።
፰፡ እርሳቸው ፡ ተምበርክከው ፡ ወደቁ ፡
እኛ ፡ ግን ፡ ቆምነ ፡ ተደግፈነም ።
፱፡ አድነነ ፡ አቤቱ ። ይስማነ ፡ ንጉሥ ፡ በጸራነው ፡ ቀን ።

## መዝሙር ፡ ፳፩

፩፡ በኃይልኽ ፡ አቤቱ ፡ ንጉሥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡
በማደንኽም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እጅግ ፡ ዕልል ያድርጋል ።
፪፡ የልቡን ፡ ፈቃድ ፡ ሰጠኸው ፡
የከንፈረንም ፡ ልመና ፡ አልከለከልኸውም ።
፫፡ በመልካም ፡ በረከት ፡ ቀድመሀዋልና ።
የጽሩ ፡ ወርቅንም ፡ ዘውድ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አስቀመጥህ ።
፬፡ ሕይወትን ፡ ለመነብኽ ፡ ሰጠኸውም ።
ረጅምንም ፡ ዘመን ፡ ለዘላለሙ ።
፭፡ በማደንኽ ፡ ክብሩ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡
ምስጋናና ፡ ጌጽም ፡ ጨመርኽለት ።



፮፡ የዘላለምን ፡ በረከት ፡ ሰጥተኸዋልና ።
በፊትኽም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ታሰኘዋለኽ ።
፯፡ ንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምነዋልና ።
በልዑልም ፡ ምሕረት ፡ አይታወክም ።
፰፡ ጸላቶችኽን ፡ ሁሉ ፡ እጅኽ ፡ ታገኛለች ።
ቀኝኽም ፡ የሚጸሉኽን ፡ ታገኛለች ።
፱፡ እንደ ፡ እሳት ፡ እቶን ፡ ታደርጋቸዋለኽ ፡ በመጕበኘትኽ ፡ ጊዜ ።
እግዚአብሔር ፡ በቍጣው ፡ ያጠፋቸዋል ፡ እሳትም ፡ ትበላቸዋለች ።
፲፡ ፍሬያቸውን ፡ ከምድር ፡ ታጠፋለኽ ፡
ዘራቸውንም ፡ ከሰው ፡ ልጆች ።
፲፩፡ ክፋትን ፡ ወደንተ ፡ አድርሰዋልና ፡
የማይቻላቸውንም ፡ ምክር ፡ አሰቡ ።
፲፪፡ ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ትመልሳቸዋለኽ ።
ፍላፃኽን ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ ታዘጋጃለኽ ።
፲፫፡ በኃይልኽ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ አቤቱ ፡
ለጽኑነትኽም ፡ እንቀኛለን ፡ ዝማሬንም ፡ እናደርጋለን ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፳፪

፩፡ አምላኬ ፡ አምላኬ ፡ ለምን ፡ ተውኸኝ ።
እኔን ፡ ከማደን ፡ ከጩኸቴም ፡ ነገር ፡ የራቅኽ ፡ ነኽ ።
፪፡ አምላኬ ፡ በቀን ፡ ወደንተ ፡ እጮኻለሁ ፡ አትመልስልኝም ።
ሌሊትም ፡ እንኳ ፡ ዕረፍት ፡ የለችኝም ።
፫፡ አንተ ፡ ግን ፡ ቅዱስ ፡ ነህ ፡ በእሥራኤል ፡ ምስጋና ፡ የምትኖር ።
፬፡ አባቶቻችን ፡ አንተን ፡ አመኑ ። አመኑ ፡ ተረዱም ።
፭፡ ወደንተ ፡ ጮኹ ፡ አመለጡም ። አንተን ፡ አመኑ ፡ አላፈሩም ።

፮፡ እኔ ፡ ግን ፡ ትል ፡ ነኝ ፡ ሰውም ፡ አይደለሁም ፡
የሰውም ፡ ነውር ፡ በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ የተናቅሁ ።
፯፡ የሚያዩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይላገጡብኛል ፡
በከንፈራቸው ፡ ይላሉ ፡ ራሳቸውንም ፡ ያንቀሳቅሳሉ ።
፰፡ በእግዚአብሔር ፡ ይመን ፡ እርሱም ፡ ያድነው ።
ቢወደውስ ፡ ያድነው ።
፱፡ አንተ ፡ ከሆድ ፡ አውፅተኸኛልና ፡
በእናቴ ፡ ጡት ፡ ሳለሁ ፡ አንተን ፡ አመንሁ ፡
፲፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ከማሕፀን ፡ ተጣልሁ ።
ከእናቴ ፡ ሆድ ፡ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ።
፲፩፡ ከኔ ፡ አትራቅ ፡ ጭንቀት ፡ ቀርባለችና ፡
የሚረዳኝም ፡ የለምና ።
፲፪፡ ብዙ ፡ በሮች ፡ ከበቡኝ ፡
የሰቡም ፡ ገቾች ፡ ከባሳን ፡ ዞሩኝ ።
፲፫፡ በላዬ ፡ አፋቸውን ፡ ከፈቱ ፡
እንደ ፡ ተርታሪ ፡ እንደሚጮኽም ፡ አንበሳ ።
፲፬፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ፈሰስሁ ፡ አፅንቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ተለያዩ ፡
ልቤ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ የሚቀልጥ ፡ ሆነ ፡ በሆዴ ፡ ማኸል ።
፲፭፡ ኃይሌ ፡ እንደ ፡ ገል ፡ ደረቀች ፡
ባንደበቴም ፡ መላሴ ፡ ተጣጋ ፡
ወደ ፡ ሞት ፡ መሬትም ፡ ታኖረኛለህ ።
፲፮፡ ብዙ ፡ ውሾች ፡ ከበቡኝና ፡ የእኩያን ፡ ጉባዔ ፡ ዞሩኝ ።
እጄንና ፡ እግሬን ፡ ቸነከሩኝ ።
፲፯፡ አፅንቶቼን ፡ ሁሉ ፡ እቈጥራለሁ ፡
እርሳቸው ፡ ግን ፡ ያያሉ ፡ ይመለከቱብኛልም ።
፲፰፡ ልብሶቼንም ፡ ለራሳቸው ፡ ይከፋፈላሉ ፡
በልብሴም ፡ ላይ ፡ ዕፃ ፡ ይጥላሉ ።
፲፱፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ከኔ ፡ አትራቅ ።
አንተ ፡ ጉልበቴ ፡ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፈጠን ።
፳፡ ነፍሴን ፡ ከሰይፍ ፡ አድናት ፡ ብቸኒቴንም ፡ ከውሻ ፡ እጅ ።
፳፩፡ ካንበሳ ፡ አፍ ፡ አድነኝ ፡
አንድ ፡ ቀንድም ፡ ካለው ፡ አርዌ ፡ ሰማሀኝ ።



፳፪፡ ለወንድሞቼ ፡ ስምኽን ፡ እነግራለሁ ፡
በጉባዔም ፡ ማኸል ፡ አመሰግንኻለሁ ።
፳፫፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ አመስግኑት ፡
የያዕቆብ ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፡ አክብሩት ፡
የእሥራኤልም ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፡ ፈሩት ።
፳፬፡ የችጋረኛን ፡ ችጋር ፡ አልናቀምና ፡ ቸልም ፡ አላለምና ፡
ፊቱንም ፡ ከርሱ ፡ አልሰወረምና ፡
ወደርሱ ፡ ግን ፡ በጮኸ ፡ ጊዜ ፡ ሰማው ።
፳፭፡ በታላቅ ፡ ጉባዔ ፡ ምስጋናዬ ፡ ካንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
እርሱንም ፡ በሚፈሩት ፡ ፊት ፡ ስለቴን ፡ እሰጣለሁ ።
፳፮፡ ችጋረኞች ፡ ይበላሉ ፡ ይጸግቡማል ፡
እግዚአብሔርንም ፡ የሚሹት ፡ ያመሰግኑታል ፡
ልባችሁ ፡ ለዘላለሙ ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ።
፳፯፡ ያስቡ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይመለሱ ፡ የምድር ፡
ዳርቻ ፡ ሁሉ ።
የአሕዛብ ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡ በፊትኽ ፡ ይሰግዳሉ ።
፳፰፡ መንግሥት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናትና ፡
እርሱም ፡ አሕዛብን ፡ ይገዛልና ።
፳፱፡ የምድር ፡ ደንደኖች ፡ ሁሉ ፡ ይበላሉ ፡ ይሰግዳሉም ፡
በፊቱ ፡ ይወድቃሉ ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ የሚወርዱ ፡ ሁሉ ፡
ለነፍሱም ፡ ሕይወት ፡ የሌለው ።
፴፡ ዘር ፡ ይገዛለታል ። ለእግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ትው
ልድ ፡ ይቈጠራል ።
፴፩፡ ይመጻሉ ፡ ጽድቁንም ፡ ይነግራሉ ፡
ለሚወለድ ፡ ሕዝብ ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ሰራው ።

## መዝሙር ፡ ፳፫፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ እረኛዬ ፡ ነው ፡ የሚያጣኝም ፡ የለም ።
፪፡ በተወደደ ፡ መስክ ፡ ያሳድረኛል ፡
በዕረፍትም ፡ ውኃ ፡ ዘንድ ፡ ያጠጣኛል ።
፫፡ ነፍሴን ፡ ይመልሳል ፡ በጽድቅም ፡ መንገድ ፡ ይመራኛል ፡
በስሙ ፡ መክንያት ።

፬፡ በሞት ፡ ጽላም ፡ ወንዝ ፡ እንኳ ፡ ብሔድ ፡ ክፉውን ፡ አልፈራም ፡፡
አንተ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነኽና ፡፡
በትርኽና ፡ ቦለታኽ ፡ እርሳቸው ፡ ያጸናኑኛል ፡፡
፭፡ በፊቴ ፡ ማዕድን ፡ ታሰናደልኛለህ ፡ መከራ ፡ በሚያመጹብኝ ፡ ፊት ፡፡
ራሴን ፡ በቅቤ ፡ ቀባኽ ፡፡ ጽዋዬም ፡ ምሉ ፡ ነው ፡፡
፮፡ ቸርነትና ፡ ምሕረት ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይከተሉኛል ፡፡
በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለረዥም ፡ ዘመን ፡ እኖራለሁ ፡፡

---

## አምስተኛ ፡ ቀን ፡፡

---

### የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

### መዝሙር ፡ ፳፬፡

፩፡ ምድር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናት ፡ ምላትዋም ፡፡
ዓለምም ፡ በርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡፡
፪፡ እርሱ ፡ በውኆች ፡ መሠርትዋታልና ፡
በፈሳሾችም ፡ አጸንትዋታልና ፡፡
፫፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ማን ፡ ይወጣል ፡፡
በቅድስናውም ፡ ስፍራ ፡ ማን ፡ ይቆማል ፡፡
፬፡ እጆቹ ፡ የነጹ ፡ ልቡም ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡፡
ለከንቱ ፡ ነፍሱን ፡ ያላነሣ ፡ በሽንግላም ፡ ያልማለ ፡፡
፭፡ እርሱ ፡ በረከትን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ይወስዳል ፡
ጽድቁንም ፡ ከመድኀኒቱ ፡ አምላክ ፡፡
፮፡ ይህች ፡ እርሱን ፡ የሚሹ ፡ ትውልድ ፡ ናት ፡
የያዕቆብ ፡ ትውልድ ፡ ፊትኽን ፡ የሚፈልጉ ፡፡
፯፡ ደጆች ፡ ራሳችሁን ፡ አንሡ ፡፡ የዓለምም ፡ ደጆች ፡ ይነሡ ፡
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይገባል ፡፡
፰፡ ማነው ፡ እርሱ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ብርቱ ፡ ኃያልም ፡፡ እግዚአብሔር ፡ በጦር ፡ የበረታ ፡፡



፱፡ ደጆች ፡ ራሳችሁን ፡ አንሡ ፡፡ የዓለምም ፡ ደጆች ፡ ይነሡ ፡
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይገባል ፡፡
፲፡ ማነው ፡ እርሱ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ የጭፍሮች ፡ አምላክ ፡፡ እርሱ ፡ ነው ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡፡

### መዝሙር ፡ ፳፭፡

፩፡ ወደንተ ፡ አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ አነሣለሁ ፡፡
፪፡ አምላኬ ፡ አንተን ፡ አመንሁ ፡ አልፈር ፡፡
ጸላቶቼ ፡ ደስ ፡ አይላቸውብኝ ፡፡
አንተን ፡ የሚቆዩ ፡ ሁሉ ፡ አያፍሩምና ፡፡
፫፡ በከንቱ ፡ የሚገብዙ ፡ ግን ፡ ሁላቸው ፡ ይፈራሉ ፡፡
፬፡ መንገድኽን ፡ አመልክተኝ ፡ አቤቱ ፡፡
ፍለጋኽንም ፡ አስተምረኝ ፡፡
፭፡ በውነትኽ ፡ ምራኝ ፡ አስተምረኝም ፡
አንተ ፡ የመድኀኒቴ ፡ አምላክ ፡ ነኽና ፡፡
ሁለግዜ ፡ አንተን ፡ ቈይቼሃለሁ ፡፡
፮፡ አቤቱ ፡ ምሕረትኽን ፡ አስብ ፡ ጸጋኽንም ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ነውና ፡፡
፯፡ የታናሽነቴን ፡ ኃጢአትና ፡ መታላለፉ ፡ አታስብብኝ ፡
አንተ ፡ እንደ ፡ ምሕረትኽ ፡ አስበኝ ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ቸርነትኽ ፡ አቤቱ ፡፡
፰፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነው ፡ የቀናም ፡ ነው ፡፡
ስለዚኽ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ በመንገዱ ፡ ያስተምራል ፡፡
፱፡ ገሮችን ፡ በፍርድ ፡ ይመራል ፡፡ ገሮችንም ፡ በመንገዱ ፡ ያስተምራቸዋል ፡፡
፲፡ የእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ጸጋና ፡ እውነት ፡ ነው ፡
ኪዳኑንና ፡ ምስክሩን ፡ ለሚጠብቁ ፡፡
፲፩፡ ስለ ፡ ስምኽ ፡ አቤቱ ፡ ኃጢአቴን ፡ ይቅር ፡ ትለኛለህ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፡፡
፲፪፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡፡

የሚመርጸውን ፡ መንገድ ፡ ያስተምረዋል ።
፲፫ ነፍሱ ፡ በመልካም ፡ ታድራለች ፡
ዘሩም ፡ ምድርን ፡ ይወርሳታል ።
፲፬ የእግዚአብሔር ፡ ምሥጢር ፡ ለሚፈሩት ፡ ነው ፡
በኪዳኑም ፡ ያስታውቃቸዋል ።
፲፭ ዓይኖቼ ፡ ሁልጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ናቸው ።
እርሱ ፡ እግሮቼን ፡ ከመርበብ ፡ ያወጣልና ።
፲፮ ፊትህን ፡ ወደኔ ፡ አድርግ ፡ ማረኝም ።
እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ችጋረኛም ፡ ነኝና ።
፲፯ የልቤ ፡ አዘን ፡ እጅግ ፡ ነው ። ከጭንቀቴ ፡ አውጣኝ ።
፲፰ ድካሜንና ፡ መከራዬን ፡ እይ ፡
ኃጢኤቴንም ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ በልልኝ ።
፲፱ ጸላቶቼንም ፡ እይ ፡ በዝተዋልና ፡
የግፍንም ፡ ጽል ፡ ጸልተውኛልና ።
፳ ነፍሴንም ፡ ጠብቀህ ፡ አድነኝ ።
አንተን ፡ አምኘለሁና ፡ አልፈር ።
፳፩ ፍጹምነትና ፡ ቅን ፡ ይጠብቁን ። አንተን ፡ ተስፋ ፡ አድርጀ
ለሁና ።
፳፪ እሥራኤልን ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ ተበዣው ፡ አቤቱ ።

መዝሙር ፡ ፳፮

፩ ፍረድልኝ ፡ አቤቱ ፡ እኔ ፡ በፍጹምነቴ ፡ ሒጀለሁና ።
በእግዚአብሔርም ፡ አምኘለሁና ፡ አልናወጥም ።
፪ ፍተነኝ ፡ አቤቱ ፡ መርምረኝም ።
ልቤን ፡ ኵላሊቴንም ፡ ንጠር ።
፫ ምሕረትኸ ፡ ባይኔ ፡ ፊት ፡ ነውና ፡
በውነትኽም ፡ ተመላለስሁ ።
፬ ከምናምን ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አልተቀመጥሁም ፡
ከሸንጋዮችም ፡ ጋራ ፡ አልገባም ።
፭ የክፎችን ፡ ጉባዔ ፡ ጸላሁ ፡
ከረሲዓንም ፡ ጋራ ፡ አልቀመጥም ።
፮ በንጽሕና ፡ እጄን ፡ አፀባለሁ ፡



መሠውያኽንም ፡ እዞራለሁ ፡ አቤቱ ፡
፯ የምስጋናን ፡ ድምፅ ፡ አሰማ ፡ ዘንድ ፡
ታምራትኽንም ፡ ሁሉ ፡ እነግር ፡ ዘንድ ።
፰ አቤቱ ፡ የቤትኽን ፡ ስፍራ ፡ ወደድሁ ፡
የክብርህንም ፡ ማደርያ ፡ ቦታ ።
፱ ከኃጥኣን ፡ ጋራ ፡ ነፍሴን ፡ አትጨምር ፡
ከደም ፡ ሰዎች ፡ ጋራም ፡ ሕይወቴን ፡
፲ በጃቸው ፡ ትንኰል ፡ ያለባቸው ፡
ቀኛቸውም ፡ መማለጃ ፡ የመላች ።
፲፩ እኔ ፡ ግን ፡ በፍጹምነቴ ፡ እሔዳለሁ ። አድነኝና ፡ ማረኝ ።
፲፪ እግሮቼ ፡ በቅን ፡ ቁመዋል ።
በጉባኤዎችም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እባርካለሁ ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፳፯

፩ እግዚአብሔር ፡ ብርሃኔና ፡ ረዳቴ ፡ ነውና ። ከማን ፡ ልፈራ ።
እግዚአብሔር ፡ የሕይወቴ ፡ ብርታት ፡ ነው ፡ ከማን ፡ ልደ
ንግጥ ።
፪ ክፎች ፡ የሚያሳዝኑኝ ፡ ጸላቶቼ ፡ ሥጋዬን ፡ ለመብላት ፡
በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡
እርሳቸው ፡ ተሰናክለው ፡ ወደቁ ።
፫ ከተማም ፡ ቢሰፈርበኝ ፡ ልቤ ፡ አይፈራም ።
ሰልፍም ፡ በላዬ ፡ ቢነሣብኝ ፡ በዚህም ፡ እምነት ፡ አለኝ ።
፬ አንዲት ፡ ነገርን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ለመንሁ ፡ እርስዋን
ም ፡ እሻለሁ ።
በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እኖር ፡
ዘንድ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ሥምረት ፡ እመለከት ፡ ዘንድ ፡
በመቅደሱም ፡ ቤት ፡ እጠይቀው ፡ ዘንድ ።
፭ በመከራ ፡ ቀን ፡ በደሱ ፡ ሰውሮኛልና ፡
በድንኳኑም ፡ መሸሸጊያ ፡ ሸሸጎኛልና ፡
ባምባም ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጎኛልና ።

፮፡ ዛሬም : በዙርያዬ : ባሉ : በጸላቶቼ : ላይ : ራሴን : ከፍ : ከፍ : ያደርጋል :
በድንኳኑም : የልልታን : መሥዋዕት : እሠዋለሁ :
ለእግዚአብሔርም : እቀኛለሁ : እዘምርለትማለሁ ::
፯፡ ቃሌን : ስማኝ : አቤቱ : ወደንተ : እጸራለሁ ::
ማረኝና : መልስልኝ ::
፰፡ ልቤ : አንተን : ይላል : አንተ : ፊቴን : እሹት : አልኸ ::
ፊትኽን : አቤቱ : እሻለሁ ::
፱፡ ፊትኽን : ከኔ : አትሰውር ::
በቍጣህ : ወደ : ባርያህ : አትድረስ :: ረዳ : ሆንኸኝ ::
አጣለኝ : አተወኝም : የመድኃኒቴ : አምላክ : ሆይ ::
፲፡ አባቴ : እናቴም : ትተውኛልና : እግዚአብሔር : ግን : ይቀበለኛል ::
፲፩፡ አቤቱ : መንገድኽን : አስተምረኝ ::
የቀናውንም  መንገድህ : ምራኝ : ስለ : ጸላቶቼ ::
፲፪፡ ለጸላቶቼ : ፈቃድ : አትስጠኝ ::
ያሰት : ምስክሮች : ተነሥተውብኛልና : ዓመፃም : ያወጣሉ::
፲፫፡ ይህም : ሳይቀር : የእግዚአብሔርን : ቸርነት :
በሕያዋን : ምድር : እንደያ : አምናለሁ ::
፲፬፡ እግዚአብሔርን : ተስፋ : አድርግ ::
ብርታ : ልብህም : ይጽና ::
እግዚአብሔርን : ተስፋ : አድርግ ::

መዝሙር : ፳፰፡

፩፡ ወደንተ : እግዚአብሔር : እጸራለሁ :: ዝም : አትበለኝ ::
ዝም : ብትለኝ : ወደ : ጕድጓድ : እንደሚወርዱ : እንደ ልሆን ::
፪፡ አቤቱ : ወደንተ : የጮኽሁትን : የልመናዬን : ቃል : ስማ::
ወደ : መቅደስህ : መናገርያ : እጄን : ባነሣሁ : ጊዜ ::
፫፡ ከኃጥአን : ጋራ : ክፋም : ከሚያደርጉ : ጋራ : አትውሰደኝ ::



ከባልንጀራቸው : ጋራ : በሰላም : የሚናገሩ : ክፋም : በልባቸው : ያለ ::
፬፡ እንደ : ስራቸው : ስጣቸው : እንደ : አካሔዳቸውም : ክፋት :
እንደ : እጃቸውም : ስራ : ክፈልላቸው :
ፍዳቸውን : ወደርሳቸው : መልሰው ::
፭፡ ወደ : እግዚአብሔር : ስራ : አላሰቡምና : ወደ : እጆቹም : አደራረግ ::
ያፈርሳቸዋል : አይሠራቸውምም ::
፮፡ እግዚአብሔር : ይመስገን : የልመናዬን : ቃል : ሰምቶኛልና ::
፯፡ እግዚአብሔር : ኃይሌና : ዋልታዬ : ነው ::
ልቤ : በርሱ : ታመነ : እርሱም : ረዳኝ ::
ልቤም : ደስ : ይለዋል : በዝማሬዬም : አመሰግነዋለሁ ::
፰፡ እግዚአብሔር : ኃይላቸው : ነው :
ለመሢሑም : የምትረዳው : መድኃኒቱ : ነው ::
፱፡ ሕዝብኽን : አድን : ርስትኽንም : ባርክ ::
ጠብቃቸውም : ለዘላለሙም : ከፍ : ከፍ : አድርጋቸው ::

መዝሙር : ፳፱።

፩፡ የኃያላን : ልጆች : ለእግዚአብሔር : አምጹ :
አምጹ : ለእግዚአብሔር : ክብርና : ችሎት ::
፪፡ ለእግዚአብሔር : የስሙን : ክብር : አምጹ :
ለእግዚአብሔር : ስገዱ : በቅድስና : ጌጽ ::
፫፡ የእግዚአብሔር : ድምፅ : በውኆች : ላይ : ነው ::
የክብር : አምላክ : ያንጐደጕደል ::
እግዚአብሔር : በብዙ : ውኆች : ላይ : ነው ::
፬፡ የእግዚአብሔር : ድምፅ : በኃይል : ነው ::
የእግዚአብሔር : ድምፅ : በምስጋና : ነው::
፭፡ የእግዚአብሔር : ድምፅ : አርዝን : ይሰብራል ::
እግዚአብሔር : የሊባኖስን : አርዝ : ይሰብራቸዋል :
፮፡ እንደ : ጥጃም : ያዘላቸዋል :
ሊባኖስን : ስርዮንንም : ቀንዱ : አንድ : እንደ : ሆነ : ልጅ ::

፯፡ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ የእሳት ፡ ነበልባል ፡ ሁሮ ፡ ይ
ቈርጣል ፡፡
፰፡ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ምድረ ፡ በደውን ፡ ያናውጻል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ የቃዴስን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ያናውጻል ፡፡
፱፡ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ብሆሮችን ፡ ያዘላል ፡
ደኖችንም ፡ ይገልጻል ፡፡
በቤት ፡ መቅደሱም ፡ ሁሉ ፡ ምስጋና ፡ ይለዋል ፡፡
፲፡ እግዚአብሔር ፡ ለጥፋት ፡ ውኃ ፡ ይቀመጣል ፡፡
ይቀመጣል ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ ሁኖ ፡፡
፲፩፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይልን ፡ ይሰጣል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ በሰላም ፡ ይባርካል ፡፡

## ስድስተኛ ፡ ቀን ፡፡

### የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

### መዝሙር ፡ ፴፡

፩፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፡ አቤቱ ፡ አውጥተኸኛልና ፡
ጸላቶቼንም ፡ ደስ ፡ አላሰኘህብኝምና ፡፡
፪፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ፈወስኸኝም ፡፡
፫፡ ነፍሴን ፡ ከሢኦል ፡ አነሣኻት ፡ አቤቱ ፡፡
ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ ከሚወርዱ ፡ አዳንኸኝ ፡፡
፬፡ ዘምሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቅዱሳኑ ፡ ሆይ ፡
ለቅድስናውም ፡ መታሰብ ፡ አመስግኑት ፡፡
፭፡ ቍጣው፡ቶሎ፡ያልፋልና፡በሞገሱም፡ሕይወት፡ኑራለችና፡፡
ማታ ፡ ልቅሶ ፡ ያድራል ፡ ጽዋትም ፡ ለደስታ ፡ ይሆናል ፡፡
፮፡ እኔ፡ግን፡በደስታዬ፡ለዘላለም፡አልታወክም፡ብዬ፡ነበርሁ፡፡
፯፡ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ በሞገስህ ፡ ለተራራዬ ፡ ኃይ
ል ፡ ታጸና ፡ ነበርህና ፡
ፊትኽን ፡ መለስኽ ፡ እኔም ፡ ደነገጽሁ ፡፡
፰፡ ወደንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮሃለሁ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ምህረት ፡ እለምናለሁ ፡፡
፱፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ብወርድ ፡ ደሜ ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ፡፡



መሬትን ፡ ያመሰግንኻል ፡ እውነትኽንም ፡ ይነግራልን ፡፡
፲፡ ስማ ፡ አቤቱ ፡ ማረኝም ፡፡
አቤቱ ፡ ረዳት ፡ ሁነኝ ፡፡
፲፩፡ ልቅሶዬን ፡ ለዘፈን ፡ ለወጥህልኝ ፡፡
ማቄን ፡ ቀደድኽ ፡ ደስታም ፡ አስታጠቅኸኝ ፡፡
፲፪፡ ክብሬ ፡ ትዘምርልኽ ፡ ዘንድ ፡ ዝምም ፡ እንዳትል ፡፡
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ለዘላለም ፡ አመሰግንሃለሁ ፡፡

### መዝሙር ፡ ፴፩፡

፩፡ አንተን ፡ አመንሁ ፡ አቤቱ ፡ ለዘላለም ፡ አልፈር ፡፡
በጽድቅኽም ፡ አድነኝ ፡፡
፪፡ ጆሮኽን ፡ ወደኔ ፡ ጣል ፡፡ ፈጥነኽም ፡ አድነኝ ፡፡
ለብርቱ ፡ አምባ ፡ ሁንልኝ ፡ ለምነት ፡ ቤትም ፡ ታድነኝ ፡
ዘንድ ፡፡
፫፡ አምባዬና ፡ መታመኛዬ ፡ አንተ ፡ ነኽና ፡፡
አድላድለኝና ፡ ስለ ፡ ስምኽ ፡ ምራኝ ፡፡
፬፡ ከዚችም ፡ ከሰወሩልኝ ፡ መርበብ ፡ አውፃኝ ፡፡
አንተ ፡ ኃይሌ ፡ ነኽና ፡፡
፭፡ በጅኽ ፡ መንፈሴን ፡ አሰጣለሁ ፡፡
ተበጀተህኛልና ፡ አቤቱ ፡ የውነት ፡ አምላክ ፡፡
፮፡ ከንቱ ፡ ግብዝነት ፡ የሚጠብቁትን ፡ ሁሉ ፡ ጸላሁ ፡፡
እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመንሁ ፡፡
፯፡ በምሕረትኽ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሐሤትም ፡ አደርጋለሁ ፡፡
መከራዬን፡አይተኻልና፡ነፍሴንም፡በመከራ፡አውቀኻልና፡፡
፰፡ በጸላትም ፡ እጅ ፡ አልዘጋኸኝም ፡፡
በሰፊ ፡ ስፍራም ፡ እግሮቼን ፡ አቆምኽ ፡፡
፱፡ እዘንልኝ ፡ አቤቱ ፡ ጨንቀኛልና ፡፡
ዓይኔም ፡ካዘን ፡ ተፈጀች ፡፡ ነፍሴም ፡ ሆዴም ፡፡
፲፡ ሕይወቴ ፡ በትካዜ ፡ አልቃለች ፡ አመታቴም ፡ በልቅሶ ፡፡
ጕልበቴ ፡ ከኃጢአቴ ፡ አለቀች ፡ አጽንቴም ፡ ሁሉ ፡ ተበላሻ ፡፡
፲፩፡ በጸላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ተነወርሁ ፡ ይልቁንም ፡ በጎረቤ
ቶቼ ፡ ዘንድ ፡

ያወቁኝም ፡ ፈሩብኝ ፡፡ በሜዳ ፡ የሚያዩኝ ፡ ከኔ ፡ ይሸሹ ፡፡
፲፪፡ ከልብ ፡ ረሱኝ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡፡
እንደ ፡ ጠፋ ፡ እቃም ፡ ሆንሁ ፡፡
፲፫፡ የብዙ ፡ ሰዎች ፡ ስድብ ፡ ሰምቻለሁና ፡፡
በዙርያ ፡ ፍርሃት ፡ ነበረ ፡
በላዬ ፡ ባንድ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ነፍሴን ፡ ለመንጠቅ ፡ ተማከሩ ፡፡
፲፬፡ እኔ ፡ ግን ፡ ባንተ ፡ አመንሁ ፡ አቤቱ ፡፡ አንተን ፡ አምላኬ ፡ አልሁኽ ፡፡
፲፭፡ ዘመኖቼ ፡ በጅኽ ፡ ናቸው ፡፡ ከጸላቶቼ ፡ ከሚያሳድዱኝም ፡ አድነኝ ፡፡
፲፮፡ ፊትኽን ፡ አብራ ፡ በባርያኽ ፡ ላይ ፡፡ ስለ ፡ ምሕረትኽም ፡ አድነኝ ፡፡
፲፯፡ አልፈር ፡ አቤቱ ፡ አንተን ፡ ጸርቻለሁና ፡፡
ሸንጋዮች ፡ ይፈሩ ፡ ወደ ፡ ሢኦልም ፡ ዝም ፡ ይበሉ ፡፡
፲፰፡ የሽንግላ ፡ ከንፈሮች ፡ ድዳች ፡ ይሁኑ ፡፡ በትዕቢት ፡ በመናቅም ፡ በጻድቅ ፡ ላይ ፡ ዋዛውን ፡ የሚናገሩ ፡፡
፲፱፡ ቸርነትኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ በዛች ፡ ለሚፈሩኽ ፡ የሰወርኻት ፡፡
ባንተ ፡ ለሚታመኑም ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ያዘጋጀኻት ፡፡
፳፡ በፊትህ ፡ መሰወርያ ፡ ከሰው ፡ ትንኰል ፡ ተሰውሬቸዋለህ ፡
በድንኳንህም ፡ ከመላስ ፡ ክርክር ፡ ታጸላቸዋለህ ፡፡
፳፩፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ በተቀጸረች ፡ ከተማ ፡ ምሕረቱን ፡ በኔ ፡ የገለጸ ፡፡
፳፪፡ እኔስ ፡ ደነገጽሁ ፡ ካይንኽም ፡ ፊት ፡ ተቈረጥሁ ፡ አልሁ ፡፡
አንተ ፡ ግን ፡ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ሰማኽኝ ፡ ወደንተ ፡ በጮኽሁ ፡ ጊዜ ፡፡
፳፫፡ እግዚአብሔርን ፡ ውደዱት ፡ ቅዱሳኑ ፡ ሁላችሁ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ እውነተኞችን ፡ ይጠብቃልና ፡
ትዕቢት ፡ የሚያደርጉትንም ፡ ፈጽሞ ፡ ይበቀላቸዋልና ፡፡
፳፬፡ ጽኑ ፡ እርሱም ፡ ልባችሁን ፡ ያጸናል ፡፡
በእግዚአብሔር ፡ የምትታመኑ ፡ ሁላችሁ ፡፡



የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፴፪፡

፩፡ ምስጉን ፡ ነው ፡ ኃጢአቱ ፡ የቀረችለት ፡ ዓመፃውም ፡ የተከደነችለት ፡፡
ምስጉን ፡ ነው ፡ እግዚአብሔር ፡ መበደሉን ፡ የማይቈጥርለት ፡ ሰው ፡፡
በመንፈሱም ፡ ሽንግላ ፡ የሌለበት ፡፡
፪፡ ዝም ፡ ሳልሁ ፡ አጽንቶቼ ፡ ተበላሽተዋልና ፡ ሁለግዜ ፡ በመጮኼ ፡፡
፫፡ በቀንና ፡ በሌት ፡ እጅኽ ፡ ከብደብኖለችና ፡፡
እርጥበቴም ፡ ለበጋ ፡ ትኩሳት ፡ ተመለሰ ፡፡
፬፡ ኃጢአቴን ፡ ላንተ ፡ አስታወቅሁ ፡
መበደሌንም ፡ አልሸፈንሁም ፡፡
ለእግዚአብሔር ፡ መተላለፌን ፡ እነግራለሁ ፡ አልሁ ፡፡
አንተም ፡ የኃጢአቴን ፡ ዓመፃ ፡ ተውኽልኝ ፡፡
፭፡ ስለዚኽ ፡ ጻድቅ ፡ ሁሉ ፡ በሚያገኝኽ ፡ ጊዜ ፡ ወደንተ ፡ ይለምናል ፡፡
በውነትም ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ለማጥፋት ፡ ወደርሱ ፡ አይደርስም ፡፡
፮፡ አንተ ፡ ለኔ ፡ መሰወርያ ፡ ነህ ፡ ከጻርም ፡ ትጠብቀኛለህ ፡፡
በደኅንነት ፡ እልልታም ፡ ትከበኛለኽ ፡፡
፯፡ አስተምርኻለሁ ፡ የምትሔድበትንም ፡ መንገድ ፡ አሳይኻለሁ ፡፡
ዐይኔን ፡ በላይህ ፡ አኖራለሁ ፡፡
፰፡ ልብ ፡ እንደ ፡ ሌላቸው ፡ እንደ ፡ ፈረስና ፡ እንደ ፡ በቅሎ ፡ አትሁኑ ፡፡
በልጓምና ፡ በልባብ ፡ጉንጫቸውን ፡ የሚለጕሙላቸው ፡
ወደንተ ፡ እንዳይቀርቡ ፡፡
፱፡ ለኃጥእ ፡ ብዙ ፡ ሥቃይ ፡ አለ ፡፡
በእግዚአብሔር ፡ የሚታመነውን ፡ ግን ፡ ምሕረት ፡ ይከበዋል ፡፡
፲፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ሕዝትም ፡ አድርጉ ፡ ጻድቃን ፡ ሆይ ፡
ልባችሁም ፡ የቀና ፡ ሁላችሁ ፡ ተመኩ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፴፪፡

፩፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ጻድቃን ፡ በእግዚአብሔር ።
ለቅኖች ፡ ምስጋና ፡ ያመሪል ።
፪፡ እግዚአብሔርን ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑ ።
አሥር ፡ አውታርም ፡ ባለው ፡ በበገና ፡ ዝማሬ ፡ አድርጉለት ።
፫፡ አዲስ ፡ ቅኔን ፡ ቀኙለት ።
ዝማሬን ፡ መልካም ፡ አድርጉ ፡ በልልታ ።
፬፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ቀንትዋልና ፡
ስሪውም ፡ ሁሉ ፡ በምነት ፡ ነውና ።
፭፡ ጽድቅንና ፡ ፍርድን ፡ ይወደል ።
የእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ በምድር ፡ መላች ።
፮፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሰማዮች ፡ ተሰሩ ፡
ባፉም ፡ እስትንፋስ ፡ ሠሪዊታቸው ፡ ሁሉ ።
፯፡ የባሕርን ፡ ውኃ ፡ እንደ ፡ መደብ ፡ የሚያከማቸው ፡
ጥልቆችንም ፡ በመዝገቦች ፡ የሚያኖሪቸው ።
፰፡ ምድር ፡ ሁልዋ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትፍሪ ።
ከርሱ ፡ ይደንግጹ ፡ በዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ።
፱፡ እርሱ ፡ ብሎ ፡ ሁንዋልና ። እርሱም ፡ አዞ ፡ ጸንትዋልና ።
፲፡ እግዚአብሔር ፡ የአሕዛብን ፡ ምክር ፡ ይሽሪል ።
ያሕዛብንም ፡ አሳብ ፡ ያጠፋል ።
፲፩፡ የእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ለዘላለሙ ፡ ይቆማል ።
የልቡም ፡ አሳብ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡ የሚሆን ፡ ሕዝብ ፡ ምስጉን ፡
ነው ።
እርሱ ፡ ለርስቱ ፡ የመረጸው ፡ ሕዝብ ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ ተመለከተ ።
የሰውንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አየ ።
፲፬፡ ከማደሪያው ፡ ቦታ ፡ ዘንድ ፡
በመድር ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ተመለከተ ።
፲፭፡ ልባቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይሰሪል ፡ ስሪቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ያስተ
ውላል ።
፲፮፡ ንጉሥ ፡ በሠሪዊቱ ፡ ብዛት ፡ አይድንም ።



ኃያልም ፡ በኃይሉ ፡ ብዛት ፡ አያመልጥም ።
፲፯፡ ፈረስም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ አያድንምም ፡
በኃይሉም ፡ ብዛት ፡ አያመልጥም ።
፲፰፡ እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወደሚፈሩት ፡ ናቸው ፡
ምህረቱንም ፡ ደጅ ፡ ወደሚጸኑ ።
፲፱፡ ነፍሳቸውን ፡ ከሞት ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡
በሪብም ፡ ጊዜ ፡ ይመግባቸው ፡ ዘንድ ።
፳፡ ነፍሳችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተስፋ ፡ ታደርጋለች ።
ረዳታችንና ፡ ጋሻችን ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፳፩፡ በርሱ ፡ ልባችን ፡ ደስ ፡ ይለዋልና ፡
በቅዱስ ፡ ስሙም ፡ ታምነናልና ።
፳፪፡ ምሕረትኽ ፡ አቤቱ ፡ በላያችን ፡ ትሁን ፡
ባንተ ፡ እንደ ፡ ታመነ ።

## መዝሙር ፡ ፴፫፡

፩፡ እግዚአብሔርን ፡ ሁለግዜ ፡ እባርካለሁ ፡
ምስጋናውም ፡ ወትሮ ፡ ባፌ ፡ ነው ።
፪፡ ነፍሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ ትላለች ፡
ገሮችም ፡ ሰምተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፫፡ እግዚአብሔርን ፡ ከኔ ፡ ጋሪ ፡ ታላቅ ፡ አድርጉ ፡
ባንድም ፡ ስሙን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እናድርግ ።
፬፡ እግዚአብሔርን ፡ እሻሁት ፡ መለሰልኝም ፡
ከፍርሃቴም ፡ ሁሉ ፡ አዳነኝ ።
፭፡ ወደርሱ ፡ ተመለከቱ ፡ አበሪላቸውም ፡
ፊታቸውም ፡ አላፈረም ።
፮፡ ደኽ ፡ ችጋረኛ ፡ ጮኸ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰማው ፡
ከመከሪውም ፡ ሁሉ ፡ አደነው ።
፯፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በሚፈሩት ፡ ዙርያ ፡ ይሰፍ
ሪል ፡ ያድናቸውማል ።
፰፡ ቅመሱ ፡ እዩም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
በርሱ ፡ የታመነ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፱፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩት ፡ ቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ።

የሚፈረት ፡ አንደችን ፡ አያጡምና ።
፲፡ ያንበሶች ፡ ግልገሎች ፡ ተቸገሩ ፡ ተራቡም ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚሹት ፡ ግን ፡ ከመልካም ፡ ነገር ፡ ሁ
ሉ ፡ አይጐደሉም ።
፲፩፡ ኑ ፡ ልጆቼ ፡ ስሙኝ ። እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ አስተ
ምራችኋለሁ ።
፲፪፡ ሕይወትን ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡ በጎንም ፡ ለማየት ፡
ዘመን ፡ የሚወድ ።
፲፫፡ መላስኽን ፡ ከክፉ ፡ ከልክል ።
ከንፈሮችኽንም ፡ ሽንግላ ፡ እንዳይናገሩ ።
፲፬፡ ከክፉ ፡ ሽሽ ፡ መልካምም ፡ አድርግ ።
ሰላምን ፡ እሻ ፡ ተከተላትም ።
፲፭፡ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወደ ፡ ጻድቃን ፡ ናቸውና ፡
ጆሮቹም ፡ ወደ ፡ ጩኸታቸው ።
፲፮፡ የእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ ነው ፡
መዘከራቸውን ፡ ከምድር ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ።
፲፯፡ ጻድቃን ፡ ጮሁ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰማቸው ፡
ከመከራቸውም ፡ ሁሉ ፡ አዳናቸው ።
፲፰፡ እግዚአብሔር ፡ ልባቸው ፡ ለተሰበረ ፡ ቅርብ ፡ ነው ፡
በመንፈሳቸው ፡ የተሰበሩትንም ፡ ያድናቸዋል ።
፲፱፡ የጻድቅ ፡ መከራው ፡ ብዙ ፡ ነው ።
እግዚአብሔርም ፡ ከሁሉ ፡ ያድነዋል ፡
፳፡ እግዚአብሔር ፡ አፅንቱን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃል ፡
ከርሳቸውም ፡ አንድ ፡ አይሰበርም ።
፳፩፡ ኃጢአተኞችን ፡ ክፋት ፡ ያጠፋቸዋል ፡
ጻድቃንንም ፡ የሚጸሉ ፡ ይኰነናሉ ።
፳፪፡ የባሮችን ፡ ነፍስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያድናል ፡
በርሱም ፡ የሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ አይኰነኑም ።



ሰባተኛ ፡ ቀን ።

---

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፴፬፡

፩፡ የሚጻሉኝን ፡ ተጻላቸው ፡ አቤቱ ፡
የሚዋጉኝንም ፡ ተዋጋቸው ።
፪፡ ጋሻንና ፡ ዋልታን ፡ ያዝ ፡ እኔንም ፡ ለመርዳት ፡ ተነሣ ።
፫፡ ጦርኽን ፡ አቅና ፡ ከሚያሳድዱኝም ፡ ጋራ ፡ ትገናኝ ፡ ዘንድ ፡
ቊልፋባቸው ፡
ነፍሴንም ፡ እኔ ፡ ረዳትሽ ፡ ነኝ ፡ በላት ፡
፬፡ ይፈሩ ፡ ይጐስቊሉም ፡ ነፍሴን ፡ የሚሹ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይበሉ ፡ ይፈሩም ፡ ለክፋቴ ፡ የሚያስቡ ።
፭፡ በንፋስ ፡ ፊት ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ ይሁኑ ፡
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ይነዳቸው ።
፮፡ መንገዳቸው ፡ ዳፅና ፡ ጨለማ ፡ ትሁን ፡
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ያሳዳቸው ።
፯፡ የጥፋትን ፡ ወጽመዳቸው ፡ በከንቱ ፡ ሰውረውብኛልና ፡
በከንቱም ፡ ለነፍሴ ፡ ጕድጓድን ፡ ቈፈረዋልና ።
፰፡ በድንገት ፡ ሞት ፡ ትምጻበት ፡
እርሱም ፡ የሰወራት ፡ መርበብ ፡ ትያዘው ።
በድንገትም ፡ ይውደቅበት ።
፱፡ ነፍሴ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላት ።
በማዳኑም ፡ እሤትን ፡ ታድርግ ።
፲፡ አፅንቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ማነው ፡ እንዳንተ ፡ አቤቱ ፡ ይሉኻል ፡
ችጋረኛን ፡ ከሚበረታበት ፡ የምታድነው ፡
ችጋረኛንም ፡ ምስኪንንም ፡ ከሚነጥቀው ፡ እጅ ።
፲፩፡ የግፍ ፡ ምስክሮች ፡ ይነሣሉ ።
የማላውቀውንም ፡ ይፈልጉብኛል ።
፲፪፡ ስለ ፡ በጎ ፡ ክፉ ፡ ይመልሱልኛል ፡ ለነፍሴ ፡ ችጋር ።
፲፫፡ እኔስ ፡ እርሳቸው ፡ በታመሙ ፡ ጊዜ ፡ ማቅ ፡ ለበስሁ ።
ነፍሴንም ፡ በጾም ፡ አደከምኋት ።
ጸሎቴም ፡ ወደ ፡ ብብቴ ፡ ተመለሳለች ።

፲፬፡ ወደጀኛ ፡ ወንድሜ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ተመላለስሁ ፡
ለናቱም ፡ እንደሚያለቅስ ፡ ራሴን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረግሁ ፡፡
፲፭፡ እኔ ፡ ግን ፡ ባነከስሁ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ ተሰበሰቡም ፡
ግፈኞችም ፡ በላዬ ፡ ተሰበሰቡ ፡ አላወቅሁምም ፡
ቀደዱኝም ፡ አልተውኝም ፡፡
፲፮፡ ከመናፍቃን ፡ ጋራ ፡ ተሣለቁብኝ ፡ ሳቁብኝም ፡
ጥርሳቸውንም ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ፈጩ ፡፡
፲፯፡ አቤቱ ፡ እንዴት ፡ ታይልኛለህ ፡፡
ነፍሴን ፡ ከጥፋታቸው ፡ አድናት ፡ ካንበሶችም ፡ ብቸነቴን ፡፡
፲፰፡ በታላቅ ፡ ጉባዔ ፡ አመሰግንኻለሁ ፡፡
በጽኑ ፡ ሕዝብም ፡ መኻከል ፡ እልል ፡ እልልኻለሁ ፡፡
፲፱፡ በግፈ ፡ የሚጸሉኝ ፡ በላዬ ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ፡፡
በከንቱ ፡ የሚጸሉኝ ፡ ባይናቸው ፡ አይጣቀሱብኝ ፡፡
፳፡ በሰላም ፡ አይናገሩምና ፡ በምድር ፡ ገሮችም ፡ ላይ ፡
የሸንግላውን ፡ ነገር ፡ ያስባሉ ፡፡
፳፩፡ አፋቸውንም ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ አሰፉ ፡
እንኳ ፡ እንኳ ፡ ባይናችን ፡ አየነው ፡ አሉም ፡፡
፳፪፡ አንተ ፡ አየኸው ፡ አቤቱ ፡ ዝም ፡ አትበል ፡
አቤቱ ፡ ከኔ ፡ አትራቅ ፡፡
፳፫፡ ተነሣ ፡ ለፍርዴም ፡ ንቃ ፡፡ አምላኬ ፡ ጌታዬ ፡ ወደ ፡ ፍርዴ ፡ ተነሣ ፡፡
፳፬፡ ፍረድልኝ ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እንደ ፡ ጽድቅኽ ፡
በላዬም ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ፡፡
፳፭፡ በልባቸው ፡ አይበሉ ፡ እንኳ ፡ እንኳ ፡
ነፍሳችን ፡ ደስ ፡ አላት ፡ ዋጥነውም ፡ አይበሉ ፡፡
፳፮፡ ይፈሩ፡ባንድም፡ይጐስቊሉ፡በመከራዬ፡ደስ፡የሚላቸው፡፡
ኀፍረትና ፡ ኀሳር ፡ ይልበሱ ፡ የታበዩብኝ ፡
፳፯፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትም ፡ ያድርጉ ፡ ጽድቄን ፡ የሚወድዋት ፡፡
ወትሮም ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ይበሉ ፡
የባርያውን ፡ ሰላም ፡ የሚወድ ፡፡
፳፰፡ መላሴም፡ጽድቅኽን፡ይናገራል፡ሁልጊዜም፡ምስጋናኽን፡፡



መዝሙር ፡ ፴፮፡

፩፡ የኃጢአተኛ ፡ ክፋት ፡ በልቤ ፡ ውሥጥ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ባይኑ ፡ ፊት ፡ የለም ፡ ይላል ፡፡
፪፡ ባይኑ ፡ መልካም ፡ ይመስለዋልና ፡
የተጸላችውን ፡ ኃጢአት ፡ ባገኘ ፡ ጊዜ ፡፡
፫፡ ያፉ ፡ ነገር ፡ ሐሰትና ፡ ሸንግላ ፡ ነው ፡፡
በጎ ፡ ማድረግን ፡ ማስተዋልንም ፡ ተወ ፡፡
፬፡ በመኝታው ፡ ሲተኛ ፡ ላሰት ፡ ያስባል ፡፡
መልካም ፡ ባልሆነች ፡ መንገድ ፡ ጸንትዋል ፡፡
ክፋትን ፡ አይታክታትም ፡፡
፭፡ ምህረትህ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፡ አቤቱ ፡፡
እውነትኽም ፡ ወደ ፡ ደመናት ፡ ትደርሳለች ፡፡
፮፡ ጽድቅኽም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራሮች ፡
ፍርድኽም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ናት ፡፡
ሰውንና ፡ እንስሳንም ፡ ታድናለኽ ፡ አቤቱ ፡፡
፯፡ ምሕረትኽ ፡ እንደምን ፡ ትከብራለች ፡ አቤቱ ፡
የሰው ፡ ልጆች ፡ በክንፎችኽ ፡ ጽላል ፡ ይታመናሉ ፡፡
፰፡ ከቤትኽ ፡ ቀቤ ፡ ይጸግባሉ ፡
ከታድላኽም ፡ ፈሳሽ ፡ ታጠጣቸዋለኽ ፡፡
፱፡ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡፡
በብርሃንኽም ፡ ብርሃኑን ፡ እናያለን ፡፡
፲፡ ምሕረትኽን ፡ ዘርጋ ፡ አቤቱ ፡ ከሚያውቁኽ ፡ ላይ ፡፡
ቸርነትኽንም ፡ ልባቸው ፡ በቀና ፡ ላይ ፡፡
፲፩፡ የትዕቢት ፡ እግር ፡ አይምጻብኝ ፡
የኃጢአተኞች ፡ እጅም ፡ አያውከኝ ፡፡
፲፪፡ ከዚያ ፡ ወደቁ ፡ ግፈ ፡ የሚሰሩ ፡፡
ወደቁ ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ፡፡

የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፴፯፡

፩፡ ስለ ፡ ክፎች ፡ አትቈጣ ፡ ግፍም ፡ በሚያደርጉ ፡ አትቅና ፡፡
፪፡ እንደ ፡ ሣዕር ፡ ፈጥነው ፡ ይቈረጣሉና ፡

እንደ : ለመለመ : ቅጠልም : ይረግፋሉና ::
፫ በእግዚአብሔር : እመን : በጎንም : አድርግ ::
በምድር : ተቀመጥ : ታምነኽም : ትመገባለኽ ::
፬ በእግዚአብሔር : ደስ : ይበልኽ : የልብኽንም : መሻት : ይሰጥኻል ::
፭ መንገድኽን : ለእግዚአብሔር : አደራ : ስጥ : በርሱም : ታመን :
እርሱም : ያደርግልኻል ::
፮ ጽድቅኽንም : እንደ : ብርሃን : ያወጻል : ፍርድኽንም : እንደ : ቀትር ::
፯ ለእግዚአብሔር : ዝም : በል : ደጅ : ጽናለትም ::
መንገዱም : በቀናችለትና : ሸንግላን : በሚያደርግ : ሰው : አትቅና ::
፰ ቍጣህ : ይቅር : መዓትህንም : ተው :
አንተ : ደግመህ : ክፉ : እንደታደርግ : አትቍጣ ::
፱ ክፎች : ይቍረጣሉና ::
እግዚአብሔርን : የሚ[illegible] : ግን : እርሳቸው : ምድርን : ይወርሳሉ ::
፲ ገና : ጥቂት : ኃጢአተኛም : አይኖርም :
ቦታውን : ትሻላኽ : አታገኘውምም ::
፲፩ ገሮች : ግን : ምድርን : ይወርሳሉ :
በብዙም : ሰላም : ደስ : ይላቸዋል ::
፲፪ ኃጢአተኛ : ጻድቅን : ይመለከታል :
ጥርሱንም : በርሱ : ያፋጫል ::
፲፫ እግዚአብሔር : ይስቅበታል ::
ቀኑ : እንዲደርስ : አይቶዋልና ::
፲፬ ኃጢአተኞች : ሰይፋቸውን : መዘዙ :
ቀስታቸውንም : ገተሩ ::
ደካማውንና : ችጋረኛውን : ያወድቁ : ዘንድ :
መንገዳቸውም : የቀናውን : ያርዱ : ዘንድ ::
፲፭ ሰይፋቸው : ወደ : ልባቸው : ይገባል :
ቀስታቸውም : ይሰበራል ::



፲፮ ለጻድቅ : የሆነ : ጥቂት : ከብዙ : ከኃጥኣን : ብዛት : ይሻላል ::
፲፯ የኃጥኣን : ክንድ : ትሰበራለችና :
እግዚአብሔር : ግን : ጻድቃንን : ይደግፋል ::
፲፰ የንጹሓንን : ዘመን : እግዚአብሔር : ያውቃል :
ርስታቸውም : ለዘላለም : ነው ::
፲፱ በክፉ : ዘመን : አያፍሩም ::
በራብ : ዘመንም : ይጸግባሉ ::
፳ ኃጥኣን : ግን : ይጠፋሉ :
የእግዚአብሔርም : ጸላቶች : እንደ : ደንግሎች : ስብ : ያልቃሉ ::
እንደ : ጢስም : ይጠፋሉ ::
፳፩ ኃጢአተኛ : ይበደራል : አይከፍልም ::
ጻድቅ : ግን : ይራራልና : ይሰጣል ::
፳፪ እግዚአብሔር : የሚባርካቸው : ምድርን : ይወርስዋታልና :
የሚያቃላቸው : ግን : ይቍረጣሉ ::
፳፫ ከእግዚአብሔር : ዘንድ : የጻድቅ : አካሔድ : ይጸናል :
በመንገዱም : ደስ : ይለዋል ::
፳፬ ቢወድቅም : አይጣልም ::
እግዚአብሔር : እጁን : ይደግፋልና ::
፳፭ ጐለመስሁ : አረጀሁም :: የተጣለውን : ጻድቅ : ግን : አላየሁም :
ዘሩንም : እኽል : የሚለምነውን ::
፳፮ ሁለጊዜ : ይራራል : ያበድርማል :
ዘሩም : በበረከት : ይኖራል ::
፳፯ ከክፉ : ሽሽ : በጎንም : አድርግ : ለዘላለሙም : ትኖራለኽ ::
፳፰ እግዚአብሔር : ፍርድን : ይወደልና : ቅዱሳኑንም : አይጥላቸውምና ::
ለዘላለም : ይጠበቃሉ : እንጅ :
የኃጥኣን : ዘር : ግን : ይጠፋል ::
፳፱ ጻድቃን : ምድርን : ይወርሳሉ :
በርስዋም : ለዘላለም : ይኖራሉ ::

፴፡ የጻድቅ ፡ አፉ ፡ ጥበብ ፡ ያወጣል ፡
መላሱም ፡ ፍርድን ፡ ይናገራል ።
፴፩፡ ያምላኩ ፡ ሕግ ፡ በልቡ ፡ ነው ፡ ሰኩናውም ፡ አይሰናከልም ።
፴፪፡ ኃጢአተኛ ፡ ጻድቅን ፡ ይጠብቃል ፡
ሊገድለውም ፡ ይፈልጋል ።
፴፫፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በጁ ፡ አይጥለውም ፡
በተከራከረውም ፡ ጊዜ ፡ አያሸንፈውም ።
፴፬፡ እግዚአብሔርን ፡ ቍይ ፡ መንገዱንም ፡ ጠብቅ ፡
ከፍም ፡ ያደርግኻል ፡ ምድርን ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ።
ኃጥኣንም ፡ እንዲ ጠፉ ፡ ታያለኽ ።
፴፭፡ ኃጥእን ፡ አየሁት ፡ ብርቱ ፡ ሁኖ ፡
እንደ ፡ ለመለመም ፡ እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዛፍ ፡ ተዘረጋ ።
፴፮፡ ብመለስ ፡ ግን ፡ አጣሁት ።
አኻሁም ፡ አላገኘሁትምም ።
፴፯፡ ፈጹሙን ፡ ሰው ፡ ጠብቅ ፡ ጻድቁንም ፡ እይ ።
ለርሱ ፡ ስላም ፡ ቀርትዋልና ።
፴፰፡ በደለኞች ፡ ግን ፡ ባንድ ፡ ይጠፋሉ ።
የኃጥኣን ፡ ቅሬታ ፡ ይጠፋል ።
፴፱፡ የጻድቃንም ፡ መድኃኒት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ መሸሸግያቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ፡
፵፡ እግዚአብሔርም ፡ ይረደቸዋል ፡ ያድናቸውማል ፡
ከኃጥኣን ፡ እጅ ፡ ያስጥላቸዋል ፡
በርሱም ፡ አምነዋልና ፡ ያድናቸዋል ።

ስምንተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፴፰፡

፩፡ አቤቱ ፡ በቍጣኽ ፡ አትቅሠፈኝ ፡
በመዓትኽም ፡ አትገሥፀኝ ።
፪፡ ፍላፃችኽ ፡ ወግተውኛልና ፡ እጅኽንም ፡ አከብደህብኛልና ።



፫፡ ከቍጣኽም ፡ የተነሣ ፡ ለሥጋዬ ፡ ጤና ፡ የለውም ።
ላፅንቶቼም ፡ ደህንነት ፡ የላቸውም ፡ ከኃጢአቴ ፡ ፊት ።
፬፡ ኃጢአቴ ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ አልፏልና ።
እንደ ፡ ከቢድ ፡ ሸክም ፡ ከበደብኝ ።
፭፡ ሰለቸ ፡ ቍስሌ ፡ በሰበሰም ፡ ከስንፍናዬ ፡ ፊት ።
፮፡ ጐሰቈልሁ ። እጅግም ፡ ጐበጥሁ ፡
ሁለግዜ ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁና ።
፯፡ ወገቤ ፡ በስድብ ፡ መልቷልችና ፡ ለሥጋዬም ፡ ጤና ፡ የ
ለችምና ።
፰፡ ደከምሁ ፡ እጅግም ፡ ተሰበርሁ ።
ከልቤም ፡ አዘን ፡ የተነሣ ፡ ጮኽሁ ።
፱፡ አቤቱ ፡ ፈቃዴ ፡ ሁሉ ፡ በፊትኽ ፡ ነው ፡
ጻሬዬም ፡ ካንተ ፡ አይሰወርም ።
፲፡ ልቤ ፡ ደነገጠብኝ ፡ ኃይሌም ፡ ተወኝ ።
ያይኔም ፡ ብርሃን ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ የለብኝም ።
፲፩፡ ወዳጆቼ ፡ ባልንጀሮቼም ፡ በቍስሌ ፡ ፊት ፡ ቆሙ ።
ዘመዶቼም ፡ ርቀው ፡ ቆሙ ።
፲፪፡ ነፍሴንም ፡ የሚሹዋት ፡ ተሸመቁብኝ ፡
መከራዬንም ፡ የሚፈልጉ ፡ ከንቱ ፡ ተናገሩ ።
ሁለግዜም ፡ ሽንግላውን ፡ ያወጡብኛል ።
፲፫፡ እኔ ፡ ግን ፡ እንደማይሰማ ፡ደንቆሮ ፡ ነኝ ።
አፉንም ፡ እንደማይከፍት ፡ ድዳ ።
፲፬፡ እንደማይሰማም ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ፡
ባፉም ፡ ተግሣጽ ፡ እንደሌለው ።
፲፭፡ አንተን ፡ ቍይቻለሁና ፡ አቤቱ ።
አንተ ፡ ስማኝ ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ።
፲፮፡ ደስ ፡ እንዳይላቸውብኝ ፡ ብያለሁና ።
እግሬ ፡ ቢናወጥ ፡ ራሳቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጉብኛልና ።
፲፯፡ እኔስ ፡ ለማንከስ ፡ የቀረብሁ ፡ ነኝና ፡
ቍስሌም ፡ ወትሮ ፡ በፊቴ ፡ ነው ።
፲፰፡ በደሌን ፡ እናገራለሁና ፡ ስለ ፡ ኃጢአቴም ፡ አዝናለሁ ።
፲፱፡ ጸላቶቼ ፡ ግን ፡ ሕያዋን ፡ ሁነው ፡ ይበረታሉ ።

በከንቱም : የሚጸሉኝ : በዙ ።
፳፡ ስለ : በጎም : ክፉ : የሚመልሱብኝ :
በጎ : ነገርንም : ስለ : ተከተልሁ : ያጸሉኛል ።
፳፩፡ አንተ : አጣለኝ : አቤቱ ። አምላኪ : ከኔ : አትራቅ ።
፳፪፡ እኔን : ወደ : መርደት : ፈጠን : አቤቱ : መድኃኒቴ ።

## መዝሙር : ፴፱፡

፩፡ በመላሴ : እንዳልስት : መንገዴን : እጠብቃለሁ : አልሁ ።
አፌን : በልጓም : እጠብቃለሁ : ኃጢአተኛ : በፊቴ : ሳለ ።
፪፡ ዝም : አልሁ : ለበጎም : እንኳ : ዝም : አልሁ ።
ሕማሜም : ታደሰብኝ ።
፫፡ ልቤ : በውሥጤ : ሞቀብኝ ። ከማሰቤም : የተነሣ :
እሳት : ነደደ : በመላሴም : ተናገርሁ ።
፬፡ አቤቱ : ፍጻሜን : አስታውቀኝ : የዘመኔም : ቍጥር : ምን : ያህል : ነው :
እኔ : እንደ : ምን : ደካማ : የሆንሁ : አውቅ : ዘንድ ።
፭፡ እነሆ : ዘመኖቼን : እንደ : ስንዝር : ርዝመት : አደረግኻቸው :
አካሌም : በፊትኽ : እንደቅን : አይመስልም ።
በውነት : የሰው : መኖር : ሁሉ : ከንቱ : ነው ።
፮፡ በውነት : ሰው : ሁሉ : በጽላ : ይመላለሳል :
በውነት : በከንቱ : ይታወካል :
ያከማቻል : የሚሰበስበውም : ማን : ይሆናል : አያውቅም ።
፯፡ አሁንስ : ተስፋዬ : ምንድር : ነው : አቤቱ ።
ተስፋዬን : አንተን : አደረግሁ ።
፰፡ ከኃጢአቴ : ሁሉ : አድነኝ ።
የሰነፎችን : ስድብ : አታድርገኝ ።
፱፡ ዝም : አልሁ : አፌንም : አልከፈትም : አንተ : አድርገኸዋልና ።
፲፡ መቅሠፍትኽን : ከኔ : አርቅ :
ከጅኽ : አመታት : የተነሣ : እኔ : አልቂያለሁና ።
፲፩፡ በተግሣፅኽ : ስለ : ኃጢአቱ : ሰውን : ዘለፍኸው :
መልካምነቱም : እንደ : ትንኝ : ትፈጀለች ።



በውነት : ሰው : ሁሉ : ከንቱ : ነው ።
፲፪፡ ጸሎቴን : ስማ : አቤቱ : ጬኸቴንም : አድምፅ :
ለልቅሶዬም : ዝም : አትበል ።
እኔ : ባንተ : ዘንድ : መጻተኛ : ነኝና :
እንደባቶቼም : ሁሉ : ተቀምጫለሁና ።
፲፫፡ ተወኝ : አርፈ : ዘንድ : ሳልሔድ : መሆኔም : ሳትጠፋ ።

## መዝሙር : ፵፡

፩፡ ቍዩቼ : እግዚአብሔርን : ደጅ : ጸናሁት :
እርሱም : ዘነበለልኝ : ጬኸቴንም : ሰማኝ ።
፪፡ ከጥፋትም : ጕድጓድ : ከረግረግም : ጭቃ : አወፃኝ :
እግሮቼንም : በደንጊያ : ላይ : አቆመ : አረጋገጤንም : አጸና ።
፫፡ አዲስ : ቅኔንም : ባፌ : ሰጠ : የአምላካችንን : ምስጋና :
ብዙ : ሰዎችም : አይተው : ይፈራሉ :
በእግዚአብሔርም : ያምናሉ ።
፬፡ እግዚአብሔርን : ተስፋውን : ያደረገ : ሰው : ምስጉን : ነው ።
ወደ : ትቢተኞችም : ያላየ : ወደ : አሰትም : ወደሚሉ ።
፭፡ ታምራትኽን : ብዙ : አደረግኽ : አቤቱ : አምላኬ :
አሳብኽም : ስለኛ : ልክ : የለውም ።
ባወራት : ብናገራትም : ከቍጥር : ሁሉ : በዛቸ ።
፮፡ መሥዋዕትና : ቍርባን : አልወደድኽም ።
ጆሮቼን : በሳህልኝ ።
ማቃጠያ : ስለ : ኃጢአትም : የሚቀርበውን : መሥዋዕት : አልሻኽም ።
፯፡ የዚያን : ጊዜ : አልሁ : እነሆ : መጣሁ ።
በመጻፉ : መጠቅለያ : ስለኔ : ተጽፏዋል ።
፰፡ ፈቃድኽን : ለማድረግ : ወደድሁ : አምላኬ : ሆይ :
ሕግኽም : በሆዴ : ውሥጥ : ነው ።
፱፡ በታላቅ : ጉባዔ : ጽድቅን : ነገርሁ ።
ከንፈሮቼን : እነሆ : አልከለከልሁም ።
አቤቱ : አንተ : ታውቃለኽ ።
፲፡ ጽድቅህን : በልቤ : ውሥጥ : አልሸፈንሁም :

እውነትክንና ፡ ማደንክን ፡ ነገርሁ ።
ምሕረትክንና ፡ እውነተኝነትክን ፡ ከታላቅ ፡ ጉባዔ ፡ አልሰወርሁም ።
፲፩፡ አንተ ፡ አቤቱ ፡ ምሕረትክን ፡ ከኔ ፡ አትከልክል ።
ቸርነትክና ፡ እውነትክ ፡ ወትሮ ፡ ያድኑኝ ።
፲፪፡ ቍጥር ፡ የሌላት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አግኝታኛለችና ።
ኃጢአቶቼ ፡ ያዙኝ ፡ ማየትም ፡ ተስኖኛል ።
ከራሴም ፡ ጸጕርም ፡ በዙ ፡ ልቤም ፡ ተወኝ ።
፲፫፡ ውደድ ፡ አቤቱ ፡ ታድነኝ ፡ ዘንድ ።
አቤቱ ፡ እኔን ፡ ወደ ፡ ማደን ፡ ፍጠን ።
፲፬፡ ይፈሩ ፡ ባንድም ፡ ይነወሩ ፡ ነፍሴን ፡ ለማጥፋት ፡ የሚወዱ ።
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ይጐስቍሉም ፡ ክፉ ፡ ሊያደርጉብኝ ፡ የሚወዱ ።
፲፭፡ ይደንግጡ ፡ በጣምም ፡ ይፈሩ ፡ እንኳ ፡ እንኳ ፡ የሚሉኝ ።
፲፮፡ ባንተ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትም ፡ ያድርጉ ፡ የሚሹክ ፡ ሁሉ ።
ወትሮም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታላቅ ፡ ያድርጉ ፡ ማደንክን ፡ የሚወዱ ።
፲፯፡ እኔ ፡ ችጋረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝ ። ጌታዬ ፡ ግን ፡ ያስብልኛል ።
አንተ ፡ ረዳ ፡ መድኃኒቴም ፡ ነክ ። አምላኬ ፡ አትዘግይ ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፵፩፡

፩፡ ለችጋረኛ ፡ ለምስኪንም ፡ የሚያስብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ በክፉ ፡ ቀን ፡ ያስመልጠዋል ።
፪፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቀዋል ፡ ሕያውንም ፡ ያደርገዋል ።
በምድር ፡ ላይም ፡ የተመሰገነ ፡ ይሆናል ።
በጸላቶቹም ፡ ነፍስ ፡ አሳልፈህ ፡ አትጣለው ።
፫፡ እግዚአብሔር ፡ በደዌው ፡ አልጋ ፡ ሳለ ፡ ይረደዋል ።
ምኝታውን ፡ ሁሉ ፡ በደዌው ፡ ታነጽፍለታለክ ።
፬፡ እኔስ ፡ አቤቱ ፡ ማረኝ ፡ አልሁ ።



ነፍሴን ፡ ፈውሳት ፡ አንተን ፡ በድያለሁና ።
፭፡ ጸላቶቼም ፡ በላዬ ፡ ክፉ ፡ ይናገራሉ ።
መቸ ፡ ይሞታል ፡ ስሙስ ፡ ይሻራል ፡ ይላሉ ።
፮፡ ያየኝ ፡ ዘንድ ፡ የሚገባ ፡ በከንቱ ፡ ይናገራል ።
ልቡ ፡ ኃጢአት ፡ ሰበሰበለት ።
ሜዳ ፡ ይወጣል ፡ ይናገረውማል ።
፯፡ ጸላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ ይመካከሩብኛል ።
በኔ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ያስባሉ ።
፰፡ የብልያል ፡ ነገርም ፡ በላዩ ፡ ነው ፡ አሉ ።
ወደቀ ፡ ከቶ ፡ አይነሣምም ።
፱፡ ደግሞም ፡ የሰላሜ ፡ ሰው ፡ የታመንሁበት ፡
እንጀራዬን ፡ የበላ ፡ ሰኰናውን ፡ በኔ ፡ አነሣ ።
፲፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ማረኝ ፡ አስነሣኝም ፡ እከፍላቸውማለሁ ።
፲፩፡ ስለዚክ ፡ እንደ ፡ ወደድክኝ ፡ አወቅሁ ።
ጸላቴ ፡ እልል ፡ አይልብኝምና ።
፲፪፡ እኔን ፡ ግን ፡ በቅንነቴ ፡ ደገፍህኝ ፡
በፊትክም ፡ ለዘላለም ፡ ታኖረኛለክ ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ ይባረክ ፡
ከዘላለም ፡ ለዘላለም ። አሜን ። አሜን ።

## መዝሙር ፡ ፵፪፡

፩፡ ብሆር ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ እንደሚናፍቅ ፡
እንዲሁም ፡ ነፍሴ ፡ ወደንተ ፡ ትናፍቃለች ፡ አቤቱ ።
፪፡ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ሕያው ፡ አምላክ ፡ ተጸማች ።
መቸ ፡ እገባለሁ ፡ ያምላኬንም ፡ ፊት ፡ አያለሁ ።
፫፡ እንቤ ፡ በቀንና ፡ በሌት ፡ ምግብ ፡ ሆነኝ ።
ሁለግዜ ፡ አምላክክ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ሲሉኝ ።
፬፡ ይህንን ፡ አስቤ ፡ ፈሰሰችብኝ ፡ ነፍሴ ፡ በውሥጤ ።
ወደ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋራ ፡ ልገባ ፡ ነበርሁና ፡ በእልልታ ፡ ቃል ፡

በደስታም ፡ በዓል ፡ ከሚያደርጉ ፡ ሕዝብ ፡ ጋራ ።
፭፡ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ ለምንስ ፡ ታውከሽብኛል ።
ለእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ጽኝ ፡ ደግሞ ፡ አመስግኘዋለሁና ፡
በፊቱ ፡ መድኃኒት ።
፮፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ነፍሴ ፡ ታዝንብኛለች ።
ስለ ፡ ዚኽም ፡ አስብኻለሁ ፡ ከዮርዳኖስ ፡ ምድር ፡
ካርሞንዔም ፡ ከታናሹ ፡ ተራራ ።
፯፡ ቀላይና ፡ ቃላይ ፡ ተጻረ ፡ በፏፏቴኽ ፡ ድምጽ ።
መውጀኽም ፡ ሞገድኽም ፡ ሁሉ ፡ በላዬ ፡ አለፈ ።
፰፡ እግዚአብሔር ፡ በቀን ፡ ምሕረቱን ፡ ያዛል ፡
በሌትም ፡ ዝማሬው ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ ይሆናል ።
ጸሎቴ ፡ ለሕይወቴ ፡ አምላክ ፡ ነው ።
፱፡ እግዚአብሔርን ፡ አምባዬን ፡ ለምን ፡ ረሳኸኝ ፡ እለዋለሁ ።
ለምንስ ፡ አዚኜ ፡ እመላለሳለሁ ፡ ጸላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ።
፲፡ አፀንቶቼን ፡ እንደ ፡ ጠመዘዙኝ ፡ ጸላቶቼ ፡ ሰደቡኝ ።
ሁለግዜ ፡ አምላክኽ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ይሉኛልና ።
፲፩፡ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ ለምንስ ፡ ታወኪብኛለሽ ።
ለእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ጽኝ ። ደግሞ ፡ አመስገኘዋለሁና ።
እርሱን ፡ የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬንም ።

መዝሙር ፡ ፵፪፡

፩፡ ፈረድልኝ ፡ አቤቱ ፡ ክርክሬንም ፡ ተከራከር ፡ ከቅድስና ፡
ከራቀች ፡ ሕዝብ ፡
ከሸንጋይና ፡ ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ አድነኝ ።
፪፡ አንተ ፡ የኀይሌ ፡ አምላክ ፡ ነኽና ። ለምን ፡ ትጥለኛለኽ ፡
ለምንስ ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁ ፡ ጸላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ።
፫፡ ብርሃንኽንና ፡ እውነትኽን ፡ ላክ ።
እርሳቸው ፡ ይምረኝ ፡ ወደ ፡ ቅድስናኽም ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ መ
ኖርያኽም ፡ ይውሰዱኝ ።
፬፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መሠውያ ፡ እገባለሁ ።
ወደ ፡ ደስታዬና ፡ ወደልልታዬ ፡ አምላክ ፡
በበገናም ፡ አመሰግንኻለሁ ፡ አምላክ ፡ አምላኬ ።



፭፡ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ ለምንስ ፡ ታወኪብኛለሽ ።
ለእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ጽኝ ፡ ደግሞ ፡ አመስግኘዋለሁና ።
እርሱ ፡ የፊቴ ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬም ፡ ነውና ።

ዘጠነኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፵፫፡

፩፡ በጆሮቻችን ፡ ሰማነ ፡ አቤቱ ፡ አባቶቻችነም ፡ ነገሩነ ።
በዘመናቸውና ፡ በቀደማቸው ፡ ዘመን ፡ የሰራኸውን ፡ ስራ ።
፪፡ አንተ ፡ በጅኽ ፡ አሕዛብን ፡ አወጣኽ ፡ እርሳቸውንም ፡ ተ
ከልኽ ።
አሕዛብን ፡ ሣቀይኻቸው ፡ አሳደድኻቸውም ።
፫፡ በሰይፋቸው ፡ ምድርን ፡ አልወረሱምና ፡ ክንዳቸውም ፡
አላደነቻቸውምና ።
ቀኝህና ፡ ክንድህ ፡ እንጅ ፡ የፊትህም ፡ ብርሃን ፡ ስለ ፡ ወደ
ድሃቸውም ።
፬፡ አንተ ፡ አምላክ ፡ ንጉሢ ፡ ነኽ ። የያዕቆብን ፡ መድኃኒት ፡
እዘዝ ።
፭፡ ባንተ ፡ ጸላቶቻችነን ፡ እንመታለን ።
በስምኽም ፡ በላያችን ፡ የቆሙትን ፡ እንረግጣለን ።
፮፡ በቀስቴ ፡ የምታመን ፡ አይደለሁምና ፡ ሰይፌም ፡ አያድ
ነኝምና ።
፯፡ አንተ ፡ ግን ፡ ከጸላቶቻችን ፡ አደንኽነ ፡ የሚጸሉነንም ፡ አ
ሳፈርኻቸው ።
፰፡ በእግዚአብሔር ፡ ሁለግዜ ፡ እልል ፡ እንላለን ፡
ስምኽንም ፡ ለዘላለም ፡ እናመሰግናለን ።
፱፡ አሁን ፡ ግን ፡ ጣልኸነ ፡ አሳፈርኸነም ፡
ከሠራዊታችንም ፡ ጋራ ፡ አትወጣም ።
፲፡ ከጸላቶቻችን ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ኋላችን ፡ መለስኸነ ፡
የሚጸሉነም ፡ ቀሙነ ።
፲፩፡ እንደ ፡ በጎች ፡ ሊበሉነ ፡ አሳልፈኽ ፡ ሰጠኸነ ፡

ወደ : አሕዛብም : በተንኸነ ::
፲፪ ሕዝብኽን : ያለ : ዋጋ : ትሸጣለኽ : አንደኛችም : በርሳቸ
ው : ለውጥ : አትወስድም ::
፲፫ ለጎረቤታችን : ስድብ : ታደርገናለህ :
ሳቅም : ሥላቅም : በዙርያችን : ላሉ ::
፲፬ ባሕዛብ : ዘንድ : ምሳሌ : ታደርገናለህ :
በሕዝብም : ዘንድ : ለራስ : መንቀሳቀሻ ::
፲፭ ጕስቍልናዬ : ሁለግዜ : በፊቴ : ነው :
የፊቴ : ኃፍረትም : ሸፈነኝ :
፲፮ ከሚሳደብ : ከሚላገድም : ቃል : የተነሣ :
ከጸላት : ከሚበቀልም : ፊት : የተነሣ ::
፲፯ ደህ : ሁሉ : በኛ : ደረሰ : አልረሳነኽም :
ኪደንኽንም : አልወነጀልነም ::
፲፰ ልባችን : ወደ : ኋላው : አላለም :
ፍላጋችንም : ከመንገድኽ : ፈቀቅ : አላለም ::
፲፱ በባቦች : ስፍራ : ሰብረኸናልና :
በሞትም : ጽላ : ሰውረኸናልና ::
፳ ያምላካችነንስ : ስም : በረሳነ :
እጃቸነንም : ወደ : ሌላ : አምላክ : ባነሣነ ::
፳፩ እግዚአብሔር : ደህነን : በደመራመርብንን : ነበር ::
እርሱ : ልብ : የሰወረውን : ያውቃልና ::
፳፪ ስላንተ : ዕለት : ዕለት : ተገድለናልና ::
እንደሚታረዱ : በጎችም : ሁናልና ::
፳፫ ንቃ : ለምን : ትተኛለኽ : አቤቱ ::
ተነሣ : ለወትሮም : አትጣለነ ::
፳፬ ለምንስ : ፊትኽን : ትሰውራለኽ ::
መከራችነንና : ችጋራችነንስ : ለምን : ትረሳላኽ ::
፳፭ ነፍሳችን : ለመሬት : ትጐብጣለችና ::
ሆዳችንም : በምድር : ተጣጋች ::
፳፮ ተነሣ : አቤቱ : ረጃችን : ስለ : ምሕረትኽም : ተበጀነ ::



መዝሙር : ፵፭

፩ ልቤ : መልካም : ነገርን : አፈላ ::
እኔ : ስዬራን : ለንጉሥ : እነግራለሁ ::
መላሴ : እንደ : ብልሃተኛ : ጻፊ : እንደ : ብርዕ : ነው ::
፪ ከሰው : ልጆች : አንተዋብኽ :: ሞገስ : በከንፈሮችኽ : ፈሰሰ ::
ስለዚኽ : እግዚአብሔር : ለዘላለም : ባረከኽ ::
፫ ሰይፍኽን : በወገብኽ : ታጠቅ : ኃያል : ሆይ ::
ክብርህንም : ሽልምህንም ::
፬ በሽልምህ : ተከናወን : ለውነት : ቃል : ውጣ : ለገርነት
ም : ለጽድቅም ::
ቀኝኽም : የሚያስፈራውን : ነገር : ታስተምረኻለች ::
፭ ፍላፃችኽ : የሾሉ : ናቸው :: አሕዛብም : በታችኽ : ይወድቃሉ ::
በንጉሥ : ጸላቶች : በልባቸው : ይገባሉ ::
፮ ዙፋንኽ : አምላክ : ሆይ : ለዘላለም : ነው ::
የመንግሥትኽም : በትር : የቀና : በትር : ነው ::
፯ እውነትን : ወደድኽ : ዐመጸኝነትንም : ጸላኽ ::
ስለዚኽ : እግዚአብሔር : አምላክኽ : በደስታ : ዘይት : ቀባ
ኽ : ከባልንጀሮችኽ : ይልቅ ::
፰ ከርቤ : ሽቱ : ምስክም : በልብሶችኽ : ሁሉ ::
ከዝሆን : ጥርስ : ቤቶችም : ዘንድ : ደስ : ይላቸውብሃል ::
፱ የነገሥት : ልጆች : ለክብርኽ : ናቸው ::
ንግሥትም : በቀኝኽ : ትቆማለች : ያአውፈርን : ወርቅ : ለብሳ ::
፲ ስሚ : ልጄ : ሆይ : እዩም : በጆሮሽም : አድምጪ ::
ሕዝብሽንም : ርሺ : ያባትሽንም : ቤት ::
፲፩ ንጉሥም : ውበትሽን : ይወደል ::
እርሱ : ጌታሽ : ነውና : ለርሱም : ስገጂ ::
፲፪ የጢሮስም : ልጅ : በመማለጃ : ትመጣለች ::
ለፊትሽ : ይማለላሉ : የአሕዛብ : ባለጠጎች ::
፲፫ የንጉሥ : ልጅ : ውሥጥዋ : ሁሉ : ክብር : ነው ::
ልብስዋ : የወርቅ : መጐናጸፊያ : ነው ::
፲፬ በወርቅ : ዘርፍ : ተጐናጽፋ : ወደ : ንጉሥ : ይወስድዋታል ::
በኋላዋ : ቈነጃጅት : ባልንጀሮችዋ : ወደንተ : ይቀርባሉ ::

፲፭፡ በደስታ ፡ በሐሤትም ፡ ይወስድዋቸዋል ፡፡
ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ እንጉሥ ፡ ይገባሉ ፡፡
፲፮፡ ባባቶችኽ ፡ ፈንታ ፡ ልጆች ፡ ይሆኑልኻል ፡፡
በምድርም ፡ ሁሉ ፡ ገዦች ፡ አድርገኽ ፡ ትሾማቸዋለኽ ፡፡
፲፯፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ስምኽን ፡ አሳስባለሁ ፡፡
ስለዚኽ ፡ አሕዛብ ፡ ለዘላላም ፡ ያመሰግኑኻል ፡፡

መዝሙር ፡ ፵፮፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ መታመኛችንና ፡ ኃይላችን ፡ ነው ፡፡
ባገኘንም ፡ በታላቅ ፡ መከራ ፡ ረዲታችን ፡፡
፪፡ ስለዚኽ ፡ አንፈራም ፡ ምድር ፡ ብትለዋወጥ ፡
ተራሮችም ፡ በውኆች ፡ ልብ ፡ ቢናወጡ ፡፡
፫፡ ውኆቹ ፡ ይጮኻሉ ፡ ይደፈርሳሉም ፡፡
ተራሮችም ፡ በኀይታው ፡ ይናወጣሉ ፡፡
፬፡ የፈሳሽ፡መስኖች፡የእግዚአብሔርን፡አገር፡ደስ፡ያሰኛሉ፡፡
የተቀደሱንም ፡ የልዑልን ፡ ማደርያዎች ፡፡
፭፡ እግዚአብሔር ፡ በማኽልዋ ፡ ነው ፡ እንዳትታወክ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ሳይጠባ ፡ ይረዳታል ፡፡
፮፡ አሕዛብ ፡ ጮኹ ፡ መንግሥታትም ፡ ተናወጡ ፡፡
ቃሉን ፡ ሰጠ ፡ ምድርም ፡ ትቀልጣለች ፡፡
፯፡ የሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡፡
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ አምባችን ፡ ነው ፡፡
፰፡ ኑ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታአምራት ፡ ታዩ ፡ ዘንድ ፡
በምድር ፡ ላይም ፡ ያደረገውን ፡ ጥፋት ፡
፱፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ዘምቻውን ፡ የሚሽር ፡፡
ቀስትን ፡ ይሰብራል ፡ ሰላጢንም ፡ ይቈርጣል ፡፡
ሠረገላውን ፡ በሳት ፡ ያቃጥላል ፡፡
፲፡ ዝም ፡ በሉ ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እወቁ ፡፡
በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላለሁ ፡ በምድር ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ እላለሁ ፡፡
፲፩፡ የሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡፡
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ አምባችን ፡ ነው ፡፡



የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፵፯፡

፩፡ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፡ እጃችሁን ፡ አጨብጭቡ ፡፡
ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ፡ በደስታ ፡ ቃል ፡፡
፪፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ ግሩም ፡ ነውና ፡
ታላቅ ፡ ንጉሥም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡፡
፫፡ አሕዛብን ፡ ከኛ ፡ በታች ፡ ያስገዛል ፡
ሰዎችንም ፡ ከግሮቻችን ፡ በታች ፡፡
፬፡ ርስታችንን፡ይመርጽልናል፡፡የያዕቆብን፡ግርማ፡የወደደውን፡፡
፭፡ አምላክ ፡ በልልታ ፡ ወጣ ፡፡ እግዚአብሔር ፡ በመለከት ፡
ድምጽ ፡፡
፮፡ ዘምሩ ፡ ለአምላክ ፡ አዝምሩ ፡
ዘምሩ ፡ ለንጉሣችን ፡ አዝምሩ ፡፡
፯፡ እግዚአብሔር ፡ የምድር ፡ ሁሉ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ፡፡
ዝምሬን ፡ አቅርቡ ፡ አስተውላችሁ ፡፡
፰፡ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ በቅድስናወ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ይቀመጣል ፡፡
፱፡ የሕዝብ ፡ አሽተኞች ፡ ተከማቹ ፡ የአብርሃም ፡ ያምላኩ ፡
ሕዝብ ፡፡
የምድር ፡ ጋሾች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናቸውና ፡
እርሱም ፡ እጅግ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፡፡

መዝሙር ፡ ፵፰፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ እጅግም ፡ እልልታ ፡ ይገባዋል ፡
ባምላካችን ፡ አገር ፡ በተቀደሰም ፡ ተራራው ፡፡
፪፡ የምድር ፡ ሁሉ ፡ ደስታ ፡ የፅዮን ፡ ተራራ ፡ ነው ፡ በመልካ
ም ፡ ስፍራ ፡ ቁሞ ፡፡
በግራ ፡ አጸገብ ፡ የታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ አገር ፡ ናት ፡፡
፫፡ እግዚአብሔር ፡ በታላቆች ፡ ቤቶችዋ ፡ አምባ ፡ ሁኖ ፡ ይታ
ወቃል ፡፡
፬፡ እነሆ ፡ ነገሥት ፡ ተከማችተው ፡ ባንድ ፡ አልፈዋልና ፡፡
፭፡ እርሳቸውስ ፡ አይተው ፡ እንዲህ ፡ አደነቁ ፡

ደነገጹም ፡ ፈርተውም ፡ ሸሹ ።
፭፡ መንቀጥቀጥ ፡ ከዚያ ፡ ያዛቸው ። ምጽም ፡ እንደ ፡ ወላጂቱ ።
፮፡ በምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ የተርሴስን ፡ መርከቦች ፡ ትሰብራለኽ ።
፯፡ እንደ ፡ ሰማነ ፡ እንደሁም ፡ አየነው ።
በሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ፡ አገር ፡ ባምላካችንም ፡ አገር ።
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያጸናታል ።
፰፡ ምህረትህን ፡ አቤቱ ፡ በመቅደስህ ፡ ውሥጥ ፡ ደጅ ፡ እንጸ
ናለን ።
፲፡ እንደ ፡ ስምኽ ፡ አቤቱ ፡ እንደሁም ፡ ምስጋናኽ ፡ ነው ፡
እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ።
በቀኝኽ ፡ ጽድቅ ፡ ትመላለች ።
፲፩፡ የፅዮን ፡ ተራራ ፡ ደስ ፡ ይበለው ፡
የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ሐሤት ፡ ያድርጉ ፡ ስለ ፡ ፍርድኽ ።
፲፪፡ ፅዮንን ፡ ክበቡ ፡ በዙርያዋም ፡ ተመላለሱ ። ግምቦችዋ
ን ፡ ቍጠሩ ።
፲፫፡ በብርታትዋ ፡ ልባችሁን ፡ አኑሩ ።
ታላቆችንም ፡ ቤቶችዋን ፡ አስቡ ፡ ለሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ ት
ነግሩ ፡ ዘንድ ።
፲፬፡ ይኽ ፡ አምላክ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ፡ ለዘላለም ።
እርሱ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ ይመራናል ።

መዝሙር ፡ ፵፰፡

፩፡ ይህነን ፡ ስሙ ፡ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ።
አድምፁ ፡ ሁላችሁ ፡ በዘመን ፡ የምትኖሩ ፡ ሁሉ ።
፪፡ የአደም ፡ ልጆችም ፡ የሰውም ፡ ልጆች ፡ ባለጠጎችም ፡ ች
ጋረኞችም ፡ አብራችሁ ።
፫፡ አፌ ፡ ጥበብ ፡ ይናገራል ፡ ልቤም ፡ ማስተዋልን ፡ ያወጣል ።
፬፡ ጆሮዬን ፡ ወደ ፡ ምሳሌ ፡ አደርጋለሁ ፡ በበገናም ፡ ምሥጢ
ሬን ፡ እከፍታለሁ ።
፭፡ ለምን ፡ እፈራለሁ ፡ በክፉ ፡ ቀን ።
የሚረገጡኝ ፡ ኃጢአት ፡ ሲከበኝ ፡ ጊዜ ።
፮፡ በኃይላቸው ፡ የሚታመኑ ፡



በባለጠግነታቸውም ፡ ብዛት ፡ የሚጓደዱ ።
፯፡ ወንድም ፡ ወንድሙን ፡ አያበጅምና ።
ካሳውንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አይሰጥምና ።
፰፡ የነፍሳቸው ፡ ካሳ ፡ ከብርዋልና ፡ ለዘላለምም ፡ ቀርትዋልና ።
፱፡ ለዘላለም ፡ እንዲኖር ፡ ጥፋትንም ፡ እንዳያይ ።
፲፡ ብልሀተኞች ፡ እንዲሞቱ ፡ አይትዋልና ፡
ከሰነፎችና ፡ ከደንቆሮች ፡ ጋራ ፡ ይጠፋሉ ፡ ገንዘባቸውን
ም ፡ ለሌሎች ፡ ይተዋሉ ።
፲፩፡ በልባቸውም ፡ ቤታቸው ፡ ለዘላለም ፡ እንዲኖር ፡
ማደርያቸውም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ይመስላቸዋል ።
በያገራቸውም ፡ ስማቸው ፡ ይጸራል ።
፲፪፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ታላቅ ፡ ቢሆን ፡ አይኖርም ።
እንደሚጠፉም ፡ እንደ ፡ እንስሶች ፡ ሆነ ።
፲፫፡ ይህች ፡ መንገዳቸው ፡ ስንፍናቸው ፡ ናት ።
ልጆቻቸውም ፡ ነገራቸውን ፡ ይወዳሉ ።
፲፬፡ እንደ ፡ በጎች ፡ በሢኦል ፡ ይኖራሉ ። ሞት ፡ ይሰማራቸዋል ።
ቅኖችም ፡ በማለዳ ፡ ይገዟቸዋል ።
መልካቸውም ፡ በሢኦል ፡ ታረጃለች ፡ ከማደርያቸው ፡ ተ
ለይታ ።
፲፭፡ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ነፍሴን ፡ ከሢኦል ፡ እጅ ፡
ይበጃል ፡ ይቀበለኛልና ።
፲፮፡ ሰውን ፡ አትፍራ ፡ ባለጠጋ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የቤቱ ፡ ክብ
ርም ፡ በበዛ ፡ ጊዜ ።
፲፯፡ በሞት ፡ ጊዜ ፡ ምንም ፡ በርሱ ፡ ጋራ ፡ አይወስድምና ።
ክብሩም ፡ ከርሱ ፡ በኋላ ፡ አይወርድምና ።
፲፰፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ ነፍሱን ፡ አመስግንዋልና ።
ሰዎችም ፡ ያመሰግኑኻል ፡ ለሰውነትኽ ፡ በጎ ፡ ብታደርግ ።
፲፱፡ ወደባቶቹ ፡ ትውልድ ፡ ይገባል ። ለዘላለሙም ፡ ብርሃ
ን ፡ አያዩም ።
፳፡ ሰውስ ፡ ታላቅ ፡ ቢሆን ፡ አእምሮም ፡ ባይኖረው ፡
እንደሚጠፉ ፡ እንደ ፡ እንስሶች ፡ ሆነ ።

## አሥረኛ ፡ ቀን ፡

---

### የጽዋት ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፵፱፡

፩፡ ያምላኮች ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረ ፡ ምድር
ንም ፡ ጸራት ፡
በጸሐይ ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያዋ ፡ ድረስ ።
፪፡ ከፅዮን ፡ ጌጽ ፡ ፍጻሜ ፡ እግዚአብሔር ፡ አበራ ።
፫፡ አምላካችን ፡ ይመጻል ፡ ዝምም ፡ አይልም ።
በፊቱ ፡ እሳት ፡ ይቃጠላል ። በዙርያውም ፡ ዓውሎ ፡ ይበ
ርታል ።
፬፡ በላይ ፡ ሁኖ ፡ ሰማይን ፡ ይጸራታል ፡ ምድርንም ፡ ሕዝ
ቡን ፡ ለመፍረድ ።
፭፡ ቅዱሳኔን ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ኪዳን ፡ በመሥዋዕት ፡ ያቆሙ
ትን ፡ ሰብስቡልኝ ።
፮፡ ሰማዮችም ፡ ጽድቁን ፡ ይናገራሉ ። እግዚአብሔር ፡ ፈ
ራጅ ፡ ነውና ።
፯፡ ስማኝ ፡ ሕዝቤ ፡ ልንገርኽ ። እሥራኤልም ፡ ልመሰክርብህ ።
እኔ ፡ አምላክ ፡ አምላክኽ ፡ ነኝ ።
፰፡ ስለ ፡ መሥዋዕትኽ ፡ የምወቅሠኽ ፡ አይደለሁም ።
የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትኽ ፡ ሁለግዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ።
፱፡ ከቤትኽ ፡ በሬን ፡ አልወስድም ። አውራ ፡ ፍየልንም ፡
ከበረትኽ ።
፲፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡ ናቸውና ።
በሸኽ ፡ ተራሮችም ፡ ያሉ ፡ እንስሶች ።
፲፩፡ የተራሮችን ፡ ወፍ ፡ ሁሉ ፡ አውቃለሁ ።
የምድረ ፡ በዳም ፡ ከብት ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፲፪፡ ብራብም ፡ ባልነግረኽ ። ዓለምና ፡ ያለበት ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡
ነውና ።
፲፫፡ በውኑ ፡ የፍሪዳውን ፡ ሥጋ ፡ እበላለሁን ፡ የፍየልንስ ፡
ደም ፡ እጠጣለሁን ።



፲፬፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋናን ፡ ሥዋ ።
ለልዑልም ፡ ስለትኽን ፡ ስጥ ።
፲፭፡ በመከራም ፡ ቀን ፡ ጽራብኝ ።
አድንኽማለሁ ፡ አንተም ፡ ልታከብረኝ ።
፲፮፡ ኃጢአተኛን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ አለው ።
ለምን ፡ አንተ ፡ ሕጌን ፡ ትነግራለኽ ። ኪዳኔንም ፡ ባፍኽ ፡
ትወስዳለኽ ።
፲፯፡ አንተስ ፡ ተግሣጽን ፡ ጸላኽ ፡ ቃላቴንም ፡ ወደ ፡ ኋላኽ ፡
ትጥላለኽ ።
፲፰፡ ሌባንም ፡ ብታይ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ትሮጣለኽ ፡
ፈንታኽም ፡ ካመንዝሮች ፡ ጋራ ፡ አለኽ ።
፲፱፡ አፍኽን ፡ በክፉ ፡ ለቀቅኽ ፡ መላስኽም ፡ ሸንግላን ፡ ተበተበ ።
፳፡ ተቀምጠኽ ፡ በወንድምኽ ፡ ላይ ፡ ትናገራለኽ ፡
የናትኽንም ፡ ልጅ ፡ በመላስኽ ፡ ትመታለኽ ።
፳፩፡ ይህነን ፡ አድርገኽ ፡ ዝም ፡ አልሁልኽ ። እንደንተ ፡ እን
ድሆን ፡ ጠረጠርኽ ።
አዋቀሥኻለሁ ፡ ኃጢአትኽንም ፡ በፊትኽ ፡ አቆማለሁ ።
፳፪፡ ይህነን ፡ አስተውሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትረሱ ።
እንዳልነጥቃችሁ ፡ የሚያድን ፡ ሳይኖር ።
፳፫፡ ምስጋናውን ፡ የሚሠዋ ፡ ያከብረኛል ።
መንገደንም ፡ ለሚያቀና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መድኃኒት ፡
አሳየዋለሁ ።

### መዝሙር ፡ ፶፡

፩፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ምህረትኽ ፡ መጠን ፡ ማረኝ ።
እንደ ፡ ርኅራኄኽም ፡ ብዛት ፡ ዐመፄን ፡ ደምስስ ።
፪፡ ከመበደሌ ፡ ፈጽመኽ ፡ እፀበኝ ፡ ከኃጢአቴም ፡ አንጻኝ ።
፫፡ እኔ ፡ ዓመፄን ፡ አውቃለሁና ፡
ኃጢአቴም ፡ ሁለግዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ።
፬፡ አንተን ፡ ብቻ ፡ በደልሁ ፡ በፊትኽም ፡ ክፉ ፡ አደረግሁ ።
በነገርኽ ፡ ትጸድቅ ፡ ዘንድ ፡ በፍርድኽም ፡ ንጹሕ ፡ ትሆን ፡
ዘንድ ።

፮፡ ባመፃ ፡ እነሆ ፡ ተሰርቻለሁና ፡ እናቴም ፡ በኃጢአት ፡
አረገዘችኝ ፡፡
፯፡ እነሆ ፡ እውነትን ፡ በውስጥ ፡ ወደኻል ፡
በስውርም ፡ ጥበብን ፡ ታስታውቀኛለኽ ፡፡
፰፡ በሁሶጵ ፡ ርጨኝ ፡ እነጻማለሁ ፡
አጽበኝ ፡ ከበረዶም ፡ ነጭ ፡ እሆናለሁ ፡፡
፱፡ ሐሤትንና ፡ ደስታውን ፡ አስማኝ ፡፡
የሰበርኻቸውም ፡ አፅንቶች ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡፡
፲፡ ከኃጢአቴ ፡ ፊትኽን ፡ መልስ ፡ በደሌንም ፡ ሁሉ ፡ ደምስስ ፡፡
፲፩፡ ንጹሕ ፡ ልብ ፡ ፍጠርልኝ ፡ አቤቱ ፡፡ የቀናውንም ፡ መንፈስ ፡
በውስጤ ፡ አድስ ፡፡
፲፪፡ ከፊትኽ ፡ አጣለኝ ፡ ቅዱስ ፡ መንፈስኽንም ፡ አትውሰድብኝ ፡፡
፲፫፡ የማደንኽን ፡ ደስታ ፡ መልስልኝ ፡ በእሽታ ፡ መንፈስም ፡
ደግፈኝ ፡፡
፲፬፡ ዐመፀኞችንም ፡ በመንገድህ ፡ አስተምራለሁ ፡
ኃጢአተኞችም ፡ ወደንተ ፡ ይመለሳሉ ፡፡
፲፭፡ ከደምም ፡ አድነኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡፡
መላሴም ፡ በጽድቅኽ ፡ ሐሤትን ፡ ታደርጋለች ፡፡
፲፮፡ ከንፈሮቼን ፡ ክፈት ፡ አቤቱ ፡ አፌም ፡ ምስጋናኽን ፡ ይነግራል ፡፡
፲፯፡ ብትወድስ ፡ መሥዋዕትም ፡ በሰጠሁ ፡፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ አትወድም ፡፡
፲፰፡ የእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ የተሰበረ ፡ መንፈስ ፡ ነው ፡
የተሰበረውን ፡ የተደቀቀውንም ፡ ልብ ፡ አትንቅም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ሆይ ፡፡
፲፱፡ በሞገስኽ ፡ ፅዮንን ፡ አብጀት ፡ አቤቱ ፡፡
የየሩሳሌምንም ፡ መከበብዮች ፡ ሥራ ፡፡
፳፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የጽድቅን ፡ መሥዋዕት ፡ ትወዳለኽ ፡
የመቃጠል ፡ መሥዋዕትም ፡ ፍጹም ፡ መሥዋዕትም ፡፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በመሠዊያኽ ፡ ላይ ፡ ፍሪዶችን ፡ ይሠዋሉ ፡፡



መዝሙር ፡ ፶፪፡

፩፡ ለምን ፡ በክፋት ፡ ትጓደደለኽ ፡ ኃያል ፡ ሆይ ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ሁለግዜ ፡ ይኖራል ፡፡
፪፡ መላስኽ ፡ መጉደትን ፡ ታስባለች ፡
እንደ ፡ ተሳለ ፡ መላጭ ፡ ሽንግላውን ፡ አድርጋ ፡፡
፫፡ ከበጎ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡ ወደድኽ ፡
አሰትንም ፡ ጽድቅን ፡ ከመናገር ፡ ይልቅ ፡፡
፬፡ የሚውጥን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ወደድኽ ፡ የሽንግላ ፡ መላስ ፡ ሆይ ፡
፭፡ እግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡ ለዘላለም ፡ ያፈርስኻል ፡፡
ይነቅልኻል ፡ ከቤትኽም ፡ ያፈልስኻል ፡፡
ስርኽንም ፡ ከሕያዋን ፡ ምድር ፡፡
፮፡ ጻድቃንም ፡ አይተው ፡ ይፈራሉ ፡ በርሱም ፡ ይስቃሉ ፡፡
፯፡ እነሆ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቻዩን ፡ ያላደረገው ፡ ሰው ፡
በባለጠግነቱም ፡ ብዛት ፡ የታመነ ፡ በመጉደቱም ፡ የበረታ ፡፡
፰፡ እኔ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ለመለመ ፡ እንደ ፡ ወይራ ፡ ዛፍ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እሆናለሁ ፡፡
በእግዚአብሔርም ፡ ምሕረት ፡ ተወከልሁ ፡ ለዘላለም ፡፡
፱፡ ለዘላለም ፡ አመሰግንኻለሁ ፡ አድርገኽልኛልና ፡
ስምኽንም ፡ ደጅ ፡ እጸናለሁ ፡ በቅዱሳንኽ ፡ ዘንድ ፡ መልካ
ም ፡ ነውና ፡፡

መዝሙር ፡ ፶፫፡

፩፡ ሰነፍ ፡ በልቡ ፡ አምላክ ፡ የለም ፡ አለ ፡፡
ስራውን ፡ አጠፋ ፡ በግፍም ፡ ረከሱ ፡፡ በጎ ፡ የሚያደርግ ፡ የለም ፡፡
፪፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ተመለከተ ፡
የሚያስተውል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የሚሻ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡
ያይ ፡ ዘንድ ፡፡
፫፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ሔዱ ፡ አብረውም ፡ ገበዙ ፡፡
በጎ ፡ የሚያደርግ ፡ የለም ፡ የለም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡፡
፬፡ አያውቁምን ፡ ግፍን ፡ አድራጎች ፡ ሁሉ ፡፡
ሕዝቤን ፡ የሚበሉ ፡ እንጀራ ፡ እንደሚበላ ፡፡
እግዚአብሔርን ፡ ግን ፡ አልጸረትም ፡፡

፭፡ በዚያ ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነገር ፡ ሳይኖር ፡፡
እግዚአብሔር ፡ የጸላቶችኽን ፡ አፅንት ፡ በትንዋልና ፡፡
አሳፈርኻቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ይንቃቸዋልና ፡፡
፮፡ ማን ፡ ይሰጣል ፡ መድኀኒት ፡ ከፅዮን ፡ ለእሥራኤል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ የሕዝቡን ፡ ምርኮ ፡ ሲመልስ ፡ ጊዜ ፡
ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ እሥራኤልም ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ፡፡

## መዝሙር ፡ ፶፫፡

፩፡ በስምኽ ፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ፡ በኀይልኽም ፡ ፍረድልኝ ፡፡
፪፡ ጸሎቴን ፡ ስማኝ ፡ አቤቱ ፡፡ ያፌንም ፡ ነገር ፡ አድምፅ ፡፡
፫፡ እንግዶች ፡ ቈመውብኛልና ፡ ኃያላንም ፡ ነፍሴን ፡ ሽተዋልና ፡፡
እግዚአብሔርንም ፡ በፊታቸው ፡ አላደረጉም ፡፡
፬፡ እነሆ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይረዳኛል ፡፡
ጌታዬም ፡ ነፍሴን ፡ ደጋፊ ፡ ነው ፡፡
፭፡ ክፋን ፡ ወደ ፡ ጸላቶቼ ፡ ይመልሳል ፡፡
በውነትኽ ፡ አጥፋቸው ፡፡
፮፡ ወድጄ ፡ እሠዋልኻለሁ ፡፡
ስምኽንም ፡ አመሰግናለሁ ፡ አቤቱ ፡ መልካም ፡ ነውና ፡፡
፯፡ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ አድኖኛልና ፡
ዓይኔም ፡ በጸላቶቼ ፡ አየቸው ፡፡

## መዝሙር ፡ ፶፬፡

፩፡ ጸሎቴን ፡ አድምፅ ፡ አቤቱ ፡፡ ከልመናዬም ፡ አትሸሽግ ፡፡
፪፡ አድምጸኝና ፡ መልስልኝ ፡፡
ባዘኔ ፡ ተቅበዝብዣለሁና ፡ ተናውጬማለሁና ፡፡
፫፡ ከጸላት ፡ ቃል ፡ ካማፂም ፡ ግፍ ፡፡
ሸንግላውን ፡ በላዬ ፡ ይጥላሉና ፡ በቍጣም ፡ ይጸሉኛል ፡፡
፬፡ ልቤ ፡ በውሥጤ ፡ ያመኛል ፡፡
የሞትም ፡ ድንጋጤ ፡ ወደቀችብኝ ፡፡
፭፡ ፍርሃት ፡ ረዓድም ፡ መጹብኝ ፡ መንቀጣቀጥም ፡ ሸፈነኝ ፡፡
፮፡ አልሁም ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ክንፍ ፡ ይሰጠኛል ፡ በርሬ ፡
አርፍ ፡ ዘንድ ፡፡



፯፡ እነሆ ፡ ኰብልዬ ፡ በራቅሁ ፡፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ በተቀ
መጥሁ ፡፡
፰፡ ከዓውሎ ፡ ንፋስ ፡ ሸሽቼ ፡ በፈጠንሁ ፡፡
፱፡ መላሳቸውን ፡ አቤቱ ፡ ፍጀውና ፡ ለየው ፡
ግፍንና ፡ ጽብን ፡ ባገር ፡ አይቻለሁና ፡፡
፲፡ በሌትና ፡ በቀን ፡ በቅጽርዋ ፡ ዙረዋልና ፡፡
ሸንግላና ፡ ድካምም ፡ በውሥጥዋ ፡ አለ ፡፡
፲፩፡ መጉደት ፡ በውሥጥዋ ፡ ነው ፡
ትንኰልና ፡ ሸንግላም ፡ ካደባባይዋ ፡ አይርቁም ፡፡
፲፪፡ ጸላትስ ፡ ቢሰድበኝ ፡ በታገሥሁ ፡፡
የሚጸላኝም ፡ ራሱን ፡ በላዬ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ቢያደርግ ፡
ከርሱ ፡ በተሸሸግሁ ፡፡
፲፫፡ አንተ ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ የኔ ፡ እኩል ፡፡
ባልንጀራዬም ፡ የታወቅህልኝም ፡፡
፲፬፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ባንድ ፡ ምክር ፡ ያጻፈጥኽልኝ ፡፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ባንድ ፡ እንሒድ ፡ የነበርን ፡፡
፲፭፡ ሞት ፡ ሳይጠብቁት ፡ ይምጻባቸው ፡
በሕይወትም ፡ ሳሉ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ይውረዱ ፡
በማደርያቸውና ፡ በውሥጣቸው ፡ ክፋት ፡ ተገኝታለችና ፡፡
፲፮፡ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አምላኬ ፡ እጮኻለሁ ፡ እግዚአብሔር
ም ፡ ያድነኛል ፡፡
፲፯፡ በማታ ፡ በጽዋትም ፡ በቀትርም ፡ እናገራለሁ ፡
እጮኽማለሁ ፡ ቃሌንም ፡ ይሰማል ፡፡
፲፰፡ ነፍሴን ፡ ከሚቀርቡኝ ፡ በሰላም ፡ አደናት ፡፡
ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ ነበሩና ፡፡
፲፱፡ እግዚአብሔር ፡ ሰምቶ ፡ ያጕሰቍላቸዋል ፡፡
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ኑርዋልና ፡
አይለወጡምና ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አልፈሩም ፡፡
፳፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፡ በወዳጆቹ ፡ ላይ ፡፡ ኪዳኑንም ፡ አፈረሰ ፡፡
፳፩፡ አፉ ፡ ከቅቤ ፡ ሲለዝብ ፡ በልቡ ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፡፡
ነገሩም ፡ ከቅቤ ፡ ይልቅ ፡ ለዘበች ፡
እርስዋም ፡ እንደ ፡ ተመዘዘ ፡ ሰይፍ ፡ ናት ፡፡

፳፪፡ ትካዜኽን : በእግዚአብሔር : ላይ : ጣል : እርሱም : ይመግብኻል :
ለጻድቅም : ለዘላለም : ሁከት : አይሰጠውም ::
፳፫፡ አንተ : አቤቱ : ወደ : ሞት : ጕድጓድ : ታወርዳቸዋለኽ ::
የደምና : የሽንግላም : ሰዎች : ዘመናቸውን : አይከፍሉም ::
እኔ : ግን : አንተን : ታመንሁ ::

---

አሥራ : አንደኛ : ቀን ::

---

የ ጽ ዋ ት : ጸ ሎ ት ::

መዝሙር : ፶፮፡

፩፡ ማረኝ : አቤቱ : ሰው : ውጦኛልና :
ሁልግዜም : በሰልፍ : አሳዘኖኛልና ::
፪፡ ጸላቶቼ : ቀኑን : ሁሉን : ሊውጡኝ : ይወዳሉ :
የሚዋጉኝ : በዝተዋልና : ልዑል : ሆይ ::
፫፡ እኔ : ግን : በፈራሁ : ጊዜ : ባንተ : ታመንሁ ::
፬፡ በእግዚአብሔር : ነገሬን : አመሰግናለሁ ::
በእግዚአብሔር : አመንሁ : አልፈራም ::
ሥጋውስ : ምን : ያደርግብኛል :
፭፡ ሁልግዜ : ነገሬን : ይከራከራሉ ::
በላዬም : የሚያስቡት : ሁሉ : ለክፉ : ነው ::
፮፡ ይሰበሰባሉም : ይሸሸጋሉም ::
እርሳቸውም : ሰኰናዬን : ይጠብቃሉ : ነፍሴን : እንደሚቆዩ ::
፯፡ ስለ : አመፃቸው : ጣላቸው ::
አሕዛብን : በቍጣ : አውርዳቸው : አቤቱ ::
፰፡ መዘዋወሬን : ትቈጥራለኽ :: አንተ : እንባን : በስልቻኽ : አስቀምጥ ::
በመጽሐፍኽ : የተጻፈ : አይደለምን ::
፱፡ ጸላቶቼ : ወደ : ኋላቸው : ይመለሳሉ : ስጸራ : ጊዜ ::
ይህነን : አወቅሁ : አምላክ : ለኔ : እንደ ለ ::
፲፡ በአምላክ : ነገሬን : አመሰግናለሁ :



በእግዚአብሔር : ነገሬን : አመሰግናለሁ ::
፲፩፡ በእግዚአብሔር : አመንሁ : አልፈራም ::
ሰውስ : ምን : ያደርግብኛል ::
፲፪፡ የተሳልሁልኽ : ስለት : አቤቱ : በላዬ : ነው ::
ላንተ : ምስጋና : እሰጣለሁ ::
፲፫፡ ነፍሴን : ከሞት : አድንኻልና ::
እግሮቼንም : ከመነደት : አታድንምን ::
በእግዚአብሔር : ፊት : እሔድ : ዘንድ : በሕያዋን : ብርሃን ::

መዝሙር : ፶፯፡

፩፡ ማረኝ : አቤቱ : ማረኝ :: አንተን : ነፍሴ : ታምናለችና ::
በክንፎችኽም : ጽላ : እታመናለሁ : መጉደት : እስክታልፍ : ድረስ ::
፪፡ ወደ : ልዑል : አምላክ : እጮኻለሁ ::
ወደ : ሚያበጅልኝ : እግዚአብሔር ::
፫፡ ከሰማይ : ይልካል : ያድነኝማል :
ይውጠኝ : ዘንድ : የሚሻ : ቢሰድበኝ ::
እግዚአብሔር : ቸርነቱንና : እውነቱን : ይልካል ::
፬፡ ነፍሴ : ባንበሶች : ማኸል : አለች :: በሳትም : ተኛሁ ::
የሰው : ልጆች : ጥርሳቸው : ጾርና : ፍላፃ : ነው :
መላሳቸውም : የተሳለ : ሾተል : ነው ::
፭፡ ከፍ : ከፍ : በል : አቤቱ : በሰማዮች : ላይ ::
በምድር : ሁሉ : ላይ : ምስጋናኽ : ትሁን ::
፮፡ ላረጋገጤ : መርበብን : አዘጋጁ : ነፍሴም : ጐበጠች ::
ጕድጓድ : በፊቴ : ቈፈሩ : በርሱም : ወደቁ ::
፯፡ ልቤ : ተዘጋጅቷል : አቤቱ : ልቤ : ተዘጋጅቷል ::
እቀኝልኻለሁ : አዘምርልህማለሁ ::
፰፡ ተነሺ : ክብሬ : ሆይ :: ተነሺ : በገና : መሰንቆም ::
ማልጄ : እነሣለሁ ::
፱፡ በአሕዛብ : ዘንድ : አመሰግንኻለሁ : አቤቱ ::
በሰዎችም : ዘንድ : አዘምርልኻለሁ ::
፲፡ ምሕረትኽ : ወደ : ሰማይ : ደርሳ : ታላቅ : ናትና :

እውነትኽም ፡ ወደ ፡ ደመናት ።
፲፩፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ በሰማዮች ፡ ላይ ።
ምስጋናኽም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ።

መዝሙር ፡ ፶፰፤

፩፡ በውነት ፡ ጸጥታን ፡ አለ ፡ ጽድቅንም ፡ ትናገሩላችሁን ፡
ቅንም ፡ ትፈርዱላችሁን ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ።
፪፡ በልባችሁ ፡ እንኳ ፡ መጉደትን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ትሰ
ራላችሁ ፡
እጆቻችሁም ፡ ሽንግላ ፡ ያደርጋሉና ።
፫፡ ኃጥኣን ፡ ከማሕፀን ፡ጀምረው ፡ ተለዩ ።
ከሆድም ፡ ጀምረው ፡ ሳቱ ፡ አሰትም ፡ ተናገሩ ።
፬፡ የባብን ፡ መርዝ ፡ የሚመስል ፡ መርዝ ፡ አላቸው ፡
እንደ ፡ ምድር ፡ አርዌም ፡ ጆሮዋን ፡ እንደምትደፍን ።
፭፡ ያስማተኛውን ፡ ቃል ፡ እንዳትሰማ ፡ አዋቂ ፡ ሲደግምባት ።
፮፡ ጥርሳቸውን ፡ ባፋቸው ፡ ስበር ፡ አቤቱ ።
ንጋጋ ፡ ያደቃል ፡ እግዚአብሔር ።
፯፡ እንደሚፈስ ፡ ውኃ ፡ ይጐሰቍላሉ ።
ፍላፆቹን ፡ ይገትራል ፡ እስኪቈረጡ ፡ ድረስ ።
፰፡ እንደሚሰባ ፡ ትል ፡ አልቀው ፡ ይሔዳሉ ።
እንደ ፡ ሴት ፡ ጭንጋፍ ፡ ፀሐይን ፡ አያዩም ።
፱፡ ምንቸታችሁ ፡ በሾኽ ፡ ሳይተኰስ ፡
እንደ ፡ ሕያው ፡ እንደ ፡ ተቃጣይም ፡ እንደሁ ፡ በቍጣው ፡
ይነጥቃቸዋል ።
፲፡ ጻድቅ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ በቀል ፡ አይቶዋልና ።
በኃጢአተኛ ፡ ደም ፡ አረጋገጡን ፡ ይታፀባል ።
፲፩፡ ሰውም ፡ በውነት ፡ ለጻድቅ ፡ ፍሬ ፡ አለው ፡ ይላል ።
በውነት ፡ በመድር ፡ ላይ ፡ የሚፈርድ ፡ አምላክ ፡ አለ ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፶፱፤

፩፡ ከጸላቶቼ ፡ አድነኝ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ።
በላዬም ፡ ከቆሙት ፡ ጠብቀኝ ።



፪፡ ግፍን ፡ ከሚያደርጉ ፡ ታደገኝ ፡ ከደም ፡ ሰዎችም ፡ አድነኝ ።
፫፡ ለነፍሴ ፡ እነሆ ፡ ሸምቀዋልና ። ብርቶችም ፡ በላዬ ፡ ተሰበሰቡ ።
በመበደሌም ፡ በኃጢአቴም ፡ አይደለም ፡ አቤቱ ።
፬፡ ያለ ፡ መበደሌ ፡ ሮጡ ፡ ተዘጋጁም ። ተነሣ ፡ ተቀበለኝ ፡ እይም ።
፭፡ አንተም ፡ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ የእሥራኤል ፡
አምላክ ፡
አሕዛብንም ፡ ሁሉ ፡ ትጐበኛቸው ፡ ዘንድ ፡ ተነሣ ።
ግፍ ፡ የሚለብሱትን ፡ አትማራቸው ።
፮፡ ማታ ፡ ይመለሱ ፡ እንደ ፡ ውሾችም ፡ ያንጐርጕሩ ፡ ባገ
ርም ፡ ይዙሩ ።
፯፡ እነሆ ፡ ባፋቸው ፡ ይናገራሉ ፡ ሰይፍም ፡ በከንፈራቸው ፡ አለ ።
ማን ፡ ይሰማልም ፡ ይላሉ ።
፰፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ትስቅባቸዋለኽ ።
አሕዛብንም ፡ ሁሉ ፡ ትላገዷለኽ ።
፱፡ ስለ ፡ ኃይሉ ፡ አንተን ፡ አምናለሁ ። እግዚአብሔር ፡ መጸ
ጊዬ ፡ ነውና ።
፲፡ የምህረቴ ፡ አምላክ ፡ ይቀድመኛል ። አምላኬ ፡ በጸላ
ቶቼ ፡ አሳየኝ ።
፲፩፡ አትግደላቸው ፡ ሕዝቤ ፡ እንዳይረሱ ።
በኃይልኽ ፡ በትናቸው ፡ አውርዳቸውም ፡ አቤቱ ፡ ጋሻችን ።
፲፪፡ ያፋቸው ፡ ኃጢአት ፡ የከንፈራቸው ፡ ነገር ፡ ነው ።
በትዕቢታቸውም ፡ ይጸመዱ ፡ ከመርገምና ፡ ካሰት ፡ ይና
ገራሉ ።
፲፫፡ በቍጣ ፡ አጥፋቸው ። አጥፋቸው ፡ እንዳይሆኑ ።
እግዚአብሔርም ፡ በያዕቆብ ፡ እንዲገዛ ፡ ይወቁ ፡ እስከ ፡
ምድርም ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ።
፲፬፡ ማታም ፡ ይመለሱ ፡ እንደ ፡ ውሾችም ፡ ያንጐርጕሩ ፡ ባገ
ርም ፡ ይዙሩ ።
፲፭፡ እርሳቸው ፡ ለመብላት ፡ ይበተኑ ፡
ምናልባት ፡ ባይጸግቡ ፡ ባያድሩም ።
፲፮፡ እኔ ፡ ግን ፡ ለጕልበትኽ ፡ እቀኛለሁ ፡ ማልደም ፡ በምሕረ
ትኽ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡

መጸጊዬ ፡ አምባዬም ፡ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ሁነኸኛልና ።
፲፯፤ አንተ ፡ ጕልበቴ ፡ ላንተ ፡ ዝማሬን ፡ አቀርባለሁ ።
እግዚአብሔር ፡ መጸጊዬ ፡ ነውና ፡ የምህረቴ ፡ አምላክ ።

መዝሙር ፡ ፷፤

፩፤ አቤቱ ፡ ጣልኸን ፡ አፈረስኸንም ።
ተቈጣኸ ፡ ወደኛ ፡ ተመለስ ።
፪፤ ምድርን ፡ አናወጽኸና ፡ ሰበርኻት ።
ቍስልዋን ፡ ፈውስ ፡ ተናውጻለችና ።
፫፤ ለሕዝብኸ ፡ ጭንቅ ፡ አሳይተኻልና ።
የሚያስደነግፀውን ፡ ወይን ፡ አጠጣኸን ።
፬፤ ለሚፈሩኸ ፡ ባይረቅ ፡ ሰጠኻቸው ፡
ስለ ፡ እውነት ፡ ያነሡዋት ፡ ዘንድ ።
፭፤ ወዳጆችኸ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ። በቀኝኸ ፡ አድነኝ ፡ መልስልነም ።
፮፤ እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ተናገረ ። ደስ ፡ ይለኛል ።
ሴኬምን ፡ እካፈላለሁ ፡ የሳኩትንም ፡ ወንዝ ፡ እሰፍራለሁ ።
፯፤ የኔ ፡ ነው ፡ ገለዓድ ፡ ምናሴም ፡ የኔ ፡ ነው ።
ኤፍሬም ፡ የራሴ ፡ ኃይል ፡ ነው ። ይሁዳ ፡ አዛዤ ፡ ነው ።
፰፤ ሞአብ ፡ መታጠቢያዬ ፡ ነው ፡
በኤዶምያስ ፡ ላይም ፡ ጫማዬን ፡ አረግፈለሁ ።
የፍልስጥኤምን ፡ አገር ፡ ሆይ ፡ እልል ፡ ብይልኝ ።
፱፤ ወደ ፡ ጽኑ ፡ አገር ፡ ማን ፡ ይወስደኛል ።
ማንስ ፡ ወደ ፡ ኤዶምያስ ፡ ይመራኛል ።
፲፤ አንተ ፡ አይደለኸምን ፡ አቤቱ ፡ የጣልኸን ።
ከሠራዊታችንም ፡ ጋራ ፡ የማትወፃ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ።
፲፩፤ ከመከራችን ፡ ረድኤት ፡ ስጠን ፡
የሰው ፡ ማዳን ፡ ከንቱ ፡ ነውና ።
፲፪፤ በእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ እናደርጋለን ።
እርሱ ፡ ጸላቶቻችንን ፡ ይረግጣልና ።

መዝሙር ፡ ፷፩፤

፩፤ ጩኸቴን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ስማ ። ጸሎቴንም ፡ አድምፅ ።
፪፤ ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ወደንተ ፡ እጮኻለሁ ፡ ልቤ ፡ ከብዶብኛልና ።



ከኔ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ወደለው ፡ አምባ ፡ ምራኝ ።
፫፤ ተስፋዬ ፡ ሁነኸኛልና ። የጸና ፡ ግምብ ፡ ከጸላት ፡ ፊት ።
፬፤ በድንኳንኸ ፡ ለዘላለም ፡ እኖራለሁ ።
በክንፎችኸ ፡ ጽላ ፡ እታመናለሁ ።
፭፤ አንተ ፡ አቤቱ ፡ ስለቴን ፡ ሰምተኻልና ።
ስምኽን ፡ ለሚፈሩ ፡ ርስትን ፡ ሰጠኻቸው ።
፮፤ ለንጉሥ ፡ በቀኑ ፡ ላይ ፡ ቀን ፡ ትጨምራለኸ ።
አመታቱም ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ትውልዶች ፡ ናቸው ።
፯፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለዘላለም ፡ ይቀመጣል ፡
ምሕረትና ፡ እውነት ፡ ይጠብቁት ፡ ዘንድ ፡ አዘጋጅለት ።
፰፤ እንዲሁ ፡ ለስምኸ ፡ ለዘላለም ፡ እዘምራለሁ ፡
ስለቴንም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እከፍላለሁ ።

አሥራ ፡ ሁለተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፷፪፤

፩፤ ነፍሴ ፡ በውነት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዝም ፡ትላለች ፡
መድኃኒቴ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ናትና ።
፪፤ እርሱ ፡ አምባዬ ፡ መድኃኒቴም ፡ ነው ።
እርሱ ፡ መጸጊዬ ፡ ነው ፡ እጅግ ፡ አልታወክም ።
፫፤ እስከ ፡ መቼ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ታስባላችሁ ።
ሁላችሁስ ፡ ትገደላላችሁ ። እንደ ፡ ዘነበለ ፡ ግድግዳ ፡
እንደ ፡ ተደፋ ፡ ቅጥርም ፡ ትሆናላችሁ ።
፬፤ ከከፍታው ፡ ይጥሉት ፡ ዘንድ ፡ ይማከራሉ ፡ አሰትንም ፡
ይወዳሉ ።
ባፋቸው ፡ ይባርካሉ ፡ በልባቸውም ፡ ያቃላሉ ።
፭፤ ነገር ፡ ግን ፡ ዝም ፡ በይ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንቺ ፡ ነፍሴ ፡
ሆይ ።
አለኝታዬ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ።
፮፤ አዎን ፡ እርሱ ፡ አምባዬና ፡ መድኃኒቴ ፡ ነው ።
እርሱም ፡ መጸጊዬ ፡ ነው ፡ አልታወክምም ።

፯፡ መድኀኒቴና ፡ ክብሬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ነው ።
የኀይሌ ፡ አምባ ፡ መታመኛዬም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ነው ።
፰፡ በርሱ ፡ እመኑ ፡ ሁለግዜ ፡ እላንተ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ።
ልባችሁን፡በፊቱ፡አፍሱ።እግዚአብሔር፡መታመኛችን፡ነው።
፱፡ ነገር ፡ ግን ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ናቸው ፡
የሰው ፡ ልጆችም ፡ አሰት ፡ ናቸው ።
እርሳቸውስ ፡ ሁላቸው ፡ በሚዛን ፡ ከምናምን ፡ የቀለሉ ፡ ናቸው ።
፲፡ በግፍ ፡ በመቀማትም ፡ አትመኑ ፡ ከንቱ ፡ ነገርንም ፡ አትውደዱ ።
ባለጠግነታችሁ ፡ ቢበዛ ፡ ልባችሁን ፡ አጣሉበት ።
፲፩፡ አንደግዜ ፡ ተናገረ ፡ እግዚአብሔር ። ሁለተግዜም ፡ ይህነን ፡ ሰማሁ ።
ኀይል ፡ የእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፲፪፡ ምሕረትም ፡ ያንተ ፡ ነው ፡ አቤቱ ።
አንተ ፡ ፍዳውን ፡ ትሰጣለኽና ፡ ለኢያንዳንዱ ፡ ኢየስራው ።

## መዝሙር ፡ ፷፫፡

፩፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ፡ ወዳንተ ፡ እማልዳለሁ ።
ነፍሴ ፡ ወዳንተ ፡ ትጸማለች ። ሥጋዬም ፡ ወዳንተ ፡ ይናፍቃል ፡
በመካን ፡ ውኃም ፡ በሌለባት ፡ ምድር ።
፪፡ ኀይልኽን ፡ ምስጋናኽንም ፡ እመለከት ፡ ዘንድ ፡ በመቅደስ ፡ እንደየሁኽ ።
፫፡ ምሕረትኽ ፡ ከሕይወት ፡ ትሻላለችና ።
ከንፈሮቼም ፡ ያመሰግኑኻል ።
፬፡ እንዲህ ፡ በሕይወቴ ፡ አመሰግንኻለሁ ። በስምኽ ፡ እጆቼን ፡ አነሣለሁ ።
፭፡ ነፍሴ ፡ እንደ ፡ በቅቤና ፡ በስብ ፡ ትጸግባለች ።
ከንፈሮቼም ፡ ደስ ፡ ብለው ፡ አፌ ፡ እልል ፡ ይልብሃል ።
፮፡ በምኝታዬም፡አስብኻለሁ።በትጋቶችም፡እናገርብኻለሁ።
፯፡ ረዳቴ ፡ ሁነኻልና ፡ በክንፎችኽም ፡ ጽላ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፰፡ ነፍሴ ፡ በኋላኽ ፡ ጥብቃለች ፡ እኔንም ፡ ቀኝኽ ፡ ደገፈችኝ ።



፱፡ እልያ ፡ ግን ፡ ሊያጠፏኝ ፡ ነፍሴን ፡ የሚሽዋት ፡
ወደ ፡ ምድር ፡ ታችኛ ፡ ስፍራ ፡ ይገባሉ ።
፲፡ ወደ ፡ ሰይፍ ፡ እጅ ፡ ይወድቃሉ ።
የቀበሮም ፡ ፈንታ ፡ ይሆናሉ ።
፲፩፡ ንጉሥ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
የሚምሉበትም ፡ ሁሉ ፡ እልል ፡ ይላሉ ።
አሰት ፡ የሚናገሩ ፡ አፋቸው ፡ ይዘጋልና ።

## መዝሙር ፡ ፷፬፡

፩፡ ቃሌን ፡ ስማኝ ፡ አቤቱ ፡ ወዳንተ ፡ ስናገር ፡ ጊዜ ።
ከጸላት ፡ ፍርሃት ፡ ሕይወቴን ፡ ጠብቅ ።
፪፡ ከክፎች ፡ ሸንጎ ፡ ሰውረኝ ። ከግፍ ፡ አድራጎችም ፡ ሁከት ።
፫፡ እንደ ፡ ሰይፍ ፡ መላሳቸውን ፡ ያሳሉ ፡
ቀስታቸውንም ፡ ገትረው ፡ ፍላጻቻቸውን ፡ መራራ ፡ ነገር ፡ ያደረጉ ።
፬፡ ንጹሕን ፡ በስውር ፡ ሊዋሉት ።
ድንገት ፡ ይነድፉታል ፡ አይፈሩምም ።
፭፡ ነፍሳቸውን ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ ያጸናሉ ።
ወጽመድ ፡ ሊሰውሩ ፡ ይማከራሉ ፡
ማን ፡ ያይላቸዋልም ፡ አሉ ።
፮፡ ግፍን ፡ መረመሩ ። በጣም ፡ መረመሩት ፡
የተመረመረውንም ፡ ምክር ፡ ፈጸሙ ።
በሰው ፡ ሁሉ ፡ ውሥጥ ፡ የጠለቀ ፡ ልብ ፡ ነው ።
፯፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ፍላፃውን ፡ ይወረውርባቸዋል ።
ቍስላቸው ፡ ድንገት ፡ ይሆንባቸዋል ።
፰፡ መላሳቸው ፡ ያሰናክላቸዋል ፡
የሚያይዋቸውም ፡ ሁሉ ፡ራሳቸውን ፡ ይነቀንቃሉ ።
፱፡ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ይፈራል ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ስራ ፡ ይነግራል ።
ስራውንም ፡ ያስተውላሉ ።
፲፡ ጻድቅ፡በእግዚአብሔር፡ደስ፡ይለዋል፡በርሱም፡ያምናል።
ልባቸውም ፡ የቀና ፡ ሁሉ ፡ እልል ፡ ይላሉ ።

የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

## መዝሙር ፡ ፷፭፤

፩፤ ላንተ ፡ ይገባል ፡ ምስጋና ፡ በቀስታ ፡ በፅዮን ፡ አቤቱ ፡፡
ላንተም ፡ ስለት ፡ ይሰጣል ፡፡
፪፤ አንተ ፡ ጸሎትን ፡ የምትሰማ ፡ ወደንተ ፡ ይመጻል ፡ ሥጋ ፡
ሁሉ ፡፡
፫፤ መታላለፊ ፡ በረታብኝ ፡፡ ዓምፃችንንስ ፡ አንተ ፡ ይቅር ፡
ትለናለኸ ፡፡
፬፤ ምስጉን ፡ ነው ፡ አንተ ፡ የመረጽኸው ፡
በቦታኽም ፡ ለማደር ፡ የተቀበልኸው ፡፡
ከቤትኽ፡በረከት፡ከቅዱስም፡ቤተመቅደስኽ፡እንጸግባለን፡፡
፭፤ ታምራትን ፡ በጽድቅኽ ፡ ትመልስልናለኽ ፡ የመድኃኒታ
ችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡
ተስፋቸው ፡ ለምድር ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ በሩቅ ፡ ባሕርም ፡ ላሉ ፡፡
፮፤ በጉልበቱ ፡ ተራሮችን ፡ የሚያጸና ፡፡ በርታትም ፡ የታጠቀ ፡፡
፯፤ የባሕርን ፡ ጩኸት ፡ የሚያስረጋ ፡ የሞገዱንም ፡ ጩኸት ፡
የአሕዛብንም ፡ ሁከት ፡፡
፰፤ በምድር ፡ ዳርቻም ፡ የሚኖሩ ፡ ከተአምራትኽ ፡ ይፈራሉ ፡፡
የጽዋትንና ፡ የማታን ፡ መውጫ ፡ ደስ ፡ ታሰኛቸዋለኽ ፡፡
፱፤ ምድርን ፡ ጐበኘኻት ፡ አጠጣኻትም ፡፡ ባለጠግነትዋንም ፡
እጅግ ፡ አበዛኽ ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ የመላ ፡ ነው ፡፡
እኽላቸውን ፡ አዘጋጀኽ ፡ እንደሁ ፡ ትሰራታለኽና ፡፡
፲፤ ትልምዋን ፡ አርካ ፡ ቦያዋንም ፡ አስተካክል ፡፡
በነጠብጣብ፡ ታቀልጣታለኽ ፡ ብቋያዋንም ፡ ትባርካለኽ ፡፡
፲፩፤ አመቱን ፡ በቸርነትኽ ፡ ከለልኻት ፡፡ ከፍለጋኽም ፡ ቅቤ ፡
ይንጠበጠባል ፡፡
፲፪፤ በምድረ ፡ በዳ ፡ መሰማርያ ፡ ይንጠበጠባል ፡ ኮረፍቶች
ም ፡ በደስታ ፡ ይታጠቃሉ ፡፡
፲፫፤ በጎች ፡ መሰማርያቸውን ፡ ለበሱ ፡ ቊሎችም ፡ በስንዴ ፡
ተሸፈኑ ፡፡
እልል ፡ ይላሉ ፡ ይቀኛሉ ፡ እንኳ ፡፡



## መዝሙር ፡ ፷፮፤

፩፤ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡፡
፪፤ የስሙን ፡ ክብር ፡ ዝመሩ ፡፡ ለምስጋናውም ፡ ክብር ፡ ስጡ፡፡
፫፤ እግዚአብሔርን ፡ ስራኽ ፡ እንዴት ፡ ይገርማል ፡ በሉት ፡፡
በኃይልኽ ፡ ብዛት ፡ ጸላቶችኽ ፡ ያልቃሉ ፡፡
፬፤ ምድር ፡ ተካታ ፡ ላንተ ፡ ትሰግዳለች ፡ ላንተም ፡ ዝመሬ ፡
ታቀርባለች ፡፡
ለስምኽ ፡ ዝማሬን ፡ ታቀርባለች ፡፡
፭፤ ኑ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ አደራረግ ፡ እዩ ፡፡
ለሰው ፡ ልጆች ፡ የሚያደርገው ፡ ነገር ፡ ግሩም ፡ ነው ፡፡
፮፤ ባሕርን ፡ ለውጦ ፡ ደረቅ ፡ አደረጋት ፡ ፈሳሹንም ፡ በግር ፡
ተሻገሩ ፡፡
በዚያ ፡ በርሱ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡፡
፯፤ በጉልበቱ ፡ ዓለሙን ፡ ይገዛል ፡፡ ዓይኖቹ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡
ያያሉ ፡፡
ምቀኞች ፡ በነፍሳቸው ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አይበሉ ፡፡
፰፤ አሕዛብ ፡ ሆይ ፡ አምላካችንን ፡ ባርኩ ፡ የምስጋናውንም ፡
ድምፅ ፡ አስሙ ፡፡
፱፤ ነፍሳችንን ፡ በሕይወት ፡ የሚያኖር ፡፡
እግራችንንም ፡ ለመናወጥ ፡ አልሰጣትም ፡፡
፲፤ ፈትነኸናልና ፡ አቤቱ ፡፡ ብርን ፡ እንደ ፡ ያነጥሩ ፡ አነጥረኸናል ፡፡
፲፩፤ ወደ ፡ መርበብ ፡ አገባኸነ ፡፡ በወገባችንም ፡ ላይ ፡ የከበደ
ውን ፡ ጭነት ፡ ጫንኽ ፡
፲፪፤ ሰውን ፡ በራሳችን ፡ ላይ ፡ አስቀመጥኽ ፡፡
በሳትና ፡ በውኃ ፡ አሻገርኽነ ፡፡ ወደ ፡ ጽጋብም ፡ አወፃኽነ፡፡
፲፫፤ የሚቃጠልን ፡ መሥዋዕት ፡ ይዤ ፡ ወደ ፡ ቤትኽ ፡ እገባለሁ፡፡
ላንተ ፡ ስለቴን ፡ እፈጽማለሁ ፡፡
፲፬፤ ከንፈሮቼ ፡ ያወጡትን ፡ ባፌም ፡ የነገርሁትን ፡ በመከራዬ ፡፡
፲፭፤ ከቅልጥ ፡ መሥዋዕት ፡ እሠዋልኻለሁ ፡ ዕጣንም ፡ ከጥ
ቦት ፡ ጋራ ፡፡
ላሞች ፡ ከፍየሎች ፡ ጋራ ፡ እሠዋልኻለሁ ፡፡
፲፮፤ ኑ ፡ ስሙኝ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሁላችሁ ፡፡

ለነፍሴ ፡ ያደረገውን ፡ ልንገራችሁ ።
፲፯፤ ባፌ ፡ ወደርሱ ፡ ጸራሁ ። በመላሴም ፡ አመሰገንሁት ።
፲፰፤ በልቤስ ፡ ዓመፃ ፡ ብመለከት ፡ ጌታዬ ፡ በደሰማኝ ፡ ነበር ።
፲፱፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በውነት ፡ ሰማኝ ።
የልመናዬን ፡ ድምፅ ፡ አደመፀ ።
፳፤ ይመስገን ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸሎቴን ፡ ያልከለከለ ፡
ምሀረቱንም ፡ ከኔ ፡ ያላራቀ ።

መዝሙር ፡ ፷፯፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ይማረን ፡ ይባርከነም ። ፊቱንም ፡ ያበራልን ።
፪፤ መንገድኽ ፡ በምድር ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ።
በአሕዛብ ፡ ሁሉም ፡ መኻከል ፡ መድኃኒትኽ ።
፫፤ አሕዛብ ፡ ይገዙልኽ ፡ አቤቱ ። አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይገዙልኽ ።
፬፤ አሕዛብ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሕሤትም ፡ ያድርጉ ።
በአሕዛብ ፡ በቅን ፡ ትፈርደለኽና ፡
አሕዛብንም ፡ በምድር ፡ ትመራለኽና ።
፭፤ አሕዛብ ፡ ይገዙልኽ ፡ አቤቱ ። አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይገዙልኽ ።
፮፤ ምድር ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ። እግዚአብሔርም ፡ አምላካችን ፡ ይባርከናል ።
፯፤ ይባርከናል ፡ እግዚአብሔር ፡ የመድርም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩታል ።

አሥራ ፡ ሶስተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፷፰።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ይንሣ ፡ ጸላቶቹም ፡ ይበተኑ ።
የሚጸሉትም ፡ ከፊቱ ፡ ይሽሹ ።
፪፤ ጢስ ፡ እንደ ፡ በተን ፡ እንዲሁ ፡ ትበትናቸዋለኽ ።
ሰምም ፡ ከእሳት ፡ ፊት ፡ እንደሚቀልጥ ፡
እንዲሁ ፡ ይቀልጣሉ ፡ ኃጥኣን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ።
፫፤ ጻድቃን ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡



በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ሕሤት ፡ ያደርጋሉ ፡
በደስታም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፬፤ ለእግዚአብሔር ፡ ቅኙ ። ለስሙም ፡ ዝመሩ ፡
መንገድ ፡ አድርጉ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ለወፃ ፡
እግዚአብሔር ፡ ስሙ ፡ በፊቱም ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።
፭፤ አባትና ፡ እናት ፡ የሌላቸው ፡ አባት ፡ የባልቴቶችም ፡ ዳኛ ፡
እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ በቅዱስ ፡ ቤቱ ።
፮፤ እግዚአብሔር ፡ ባሕታውያንን ፡ በቤት ፡ ያሳድራል ።
እስሮችንም ፡ ወደ ፡ ባለጠግነት ፡ ያወጣቸዋል ።
ምቀኞች ፡ ግን ፡ በበረኻ ፡ ይኖራሉ ።
፯፤ አቤቱ ፡ በሕዝብኽ ፡ ፊት ፡ በወፃኽ ፡ ጊዜ ።
በምድረ ፡ በዳ ፡ ባለፍኽ ፡ ጊዜ ፡
፰፤ ምድር ፡ ተናወጸች ፡ ሰማይም ፡ አንኳ ፡ አንጠበጠበ ።
ሲናም ፡ ከአምላክ ፡ ፊት ፡ ተናወጸ ።
ከእግዚአብሔር ፡ ከእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ ፊት ።
፱፤ የሞገስን ፡ ዝናም ፡ ለርስትኽ ፡ አዘነምኽ ፡ አቤቱ ።
በደከመም ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ አጸናኸው ።
፲፤ ሕያዋንኽም ፡ በርሱ ፡ አደሩ ። በምሕረትኽ ፡ ለድኆች ፡ አዘጋጀኽ ፡ አቤቱ ።
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ።
የምስራች ፡ የሚነግሩት ፡ ጉባዔ ፡ ታላቅ ፡ ናት ።
፲፪፤ የሠራዊት ፡ ነገሥታት ፡ ሸሹ ፡ ሸሹ ።
በቤትም ፡ የምትኖር ፡ ምርኮውን ፡ ተካፈለች ።
፲፫፤ ብተኙም ፡ በምንቸቶች ፡ ማኸል ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ክንፎች ፡ ትሆናላችሁ ፡
በብር ፡ የተለበጡ ፡ ላባቹዋም ፡ ብልጭልጭ ፡ በሚል ፡ ወርቅ ።
፲፬፤ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ ነገሥታትን ፡ በበተነባት ፡ ጊዜ ፡
በሰልሞን ፡ እንደ ፡ በረደ ፡ ሆነ ።
፲፭፤ የባሣን ፡ ተራራ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ነው ።
የባሣን ፡ ተራራ ፡ ሰፊ ፡ ተራራ ፡ ነው ።
፲፮፤ ለምን ፡ ትዘሉ ፡ የምትሰፉ ፡ ተራሮች ።
እግዚአብሔር ፡ ይሆነን ፡ ተራራ ፡ ያድርበት ፡ ዘንድ ፡ ፈቀደው ፡

አዎን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያድርበታል ።
፲፯፡ የእግዚአብሔር ፡ መንኰራኵር ፡ ሁለት ፡ እልፍ ፡ ናቸው ፡
እርሳቸውም ፡ የደስተኞች ፡ ሺሖች ።
እግዚአብሔር ፡ በመካከላቸው ፡ ነው ፡ በሲና ፡ በመቅደሱ ።
፲፰፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ወጣኽ ፡ ምርኮንም ፡ ማረክኽ ።
ለሰዎችም ፡ ስጦታ ፡ ተቀበልኽ ።
ደግሞም ፡ ላመፀኞች ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ያድርባ
ቸው ፡ ዘንድ ።
፲፱፡ እግዚአብሔር ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይመስገን ።
የመድኀኒታችን ፡ አምላክ ፡ ያሸክመናል ።
፳፡ አምላካችንስ ፡ የድኅነት ፡ አምላክ ፡ ነው ።
የሞት ፡ መውጫ ፡ ለጌታችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነው ።
፳፩፡ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ የጸላቶቹን ፡ ራስ ፡ ይቀጠቅጣል ።
በኀጢአቱ ፡ የሚሔድንም ፡ የጸጕሩን ፡ አናት ።
፳፪፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡ ከባሳን ፡ እመልሳቸዋለሁ ።
ከባሕር ፡ ጥልቅ ፡ እመልሳቸዋለሁ ።
፳፫፡ እግሮችኽ ፡ በደም ፡ ይረግጡ ፡ ዘንድ ።
የውሾችኽም ፡ መላስ ፡ የጸላቶችኽን ፡ ደም ፡ ይልስ ፡ ዘንድ ።
፳፬፡ መንገድኽ ፡ ተገለጸች ፡ አቤቱ ።
የንጉሤ ፡ የአምላኬ ፡ መንገድ ፡ በመቅደስ ።
፳፭፡ የሚቀኙ ፡ ቀደሙ ፡ አዝማሮችም ፡ በኋላ ፡ ተከተሉ ፡
ከበሮንም ፡ የሚመቱ ፡ ቈነጃጅት ፡ በመካከል ፡ ነበሩ ።
፳፮፡ በጉባኤዎች ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ። ጌታችንንም ፡
ከእሥራኤል ፡ ምንጭ ።
፳፯፡ ከዚያ ፡ ታናሽ ፡ ብንያም ፡ አለቃቸው ።
የይሁዳ ፡ አለቆችና ፡ ዓላማቸው ።
የዛብሎን ፡ አለቆች ፡ የንፍታሌምም ፡ አለቆች ።
፳፰፡ አምላክኽ ፡ ኀይልኽን ፡ አዘዘው ።
ይህነን ፡ ለኛ ፡ የሠራኸውን ፡ አጽናልን ፡ አቤቱ ።
፳፱፡ ስለ ፡ የሩሳሌም ፡ ቤተ ፡ መቅደስኽ ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ መ
ንሻ ፡ ያመጹልኻል ።
፴፡ የሸምበቆን ፡ አርዌ ፡ ገሥፅ ፡ የበሮችን ፡ጉባዔ ፡



የሕዝብንም ፡ ወይፈኖች ፡ ስለ ፡ ብር ፡ የሚረግጡትን ፡
ሰልፍ ፡ የሚወዱትን ፡ አሕዛብ ፡ በትን ።
፴፩፡ ባለጠጎች ፡ ከምስር ፡ ይመጻሉ ።
ኢትዮጵያም ፡ እጅዋን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትዘረጋለች ።
፴፪፡ የምድር ፡ መንግሥታት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቅኙ ።
ለጌታችንም ፡ ዝማሬን ፡ አቅርቡ ።
፴፫፡ በሰማዮች ፡ ላይ ፡ ለሚሔድ ። ከድሮ ፡ ዘመን ፡ በነበሩ ፡
ሰማዮች ፡ ላይ ።
እነሆ ፡ ቃሉን ፡ ይሰጣል ፡ የኀይልን ፡ ቃል ።
፴፬፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኀይልን ፡ ስጡ ።
በእሥራኤል ፡ ላይ ፡ ምስጋናው ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ኀይሉም ፡
በደመናት ።
፴፭፡ ከመቅደስኽ ፡ ዘንድ ፡ የተፈራኽ ፡ ነኽ ፡ አቤቱ ።
የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ እርሱ ፡ ኀይል ፡ ይሰጣል ፡ ብርታ
ትም ፡ ለወገኑ ።
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።

---

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፷፱፡

፩፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ነፍሴ ፡ ደርስዋልና ።
፪፡ በጥልቅ ፡ ጭቃ ፡ ጠለቅሁ ፡ መቆምያም ፡ የለኝም ።
ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ባሕር ፡ ደረስሁ ፡ሞገዲም ፡ አሰጠመኝ ።
፫፡ በጩኸት ፡ ደከምሁ ። ጉሮሮዬ ፡ ሰለለ ፡
ዓይኖቼም ፡ ፈዘዙ ፡ አምላኬን ፡ ስቈይ ።
፬፡ በከንቱ ፡ የሚጸሉኝ ፡ ከራስ ፡ ጸጕሬ ፡ በዙ ፡
ባሰት ፡ ጥፈቴን ፡ የሚሹ ፡ ጸላቶቼ ፡ በረቱ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ያልቀማሁትን ፡ መለስሁ ።
፭፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡ ስንፍናዬን ፡ታውቃለኽ ።
ኀጢአቴም ፡ ካንተ ፡ አልተሰወረም ።
፮፡ በኔ ፡ አደፈሩ ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉኽ ፡ አቤቱ ፡ የሠራዊ
ት ፡ እግዚአብሔር ።

በኔ ፡ አይነወሩ ፡ የሚሹኽ ፡ የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡፡
፯፡ ስላንተ፡ስድብን፡ታግሼአለሁና፡፡ኀፍረትም፡ፊቴን፡ሸፈነች፡፡
፰፡ ከወንድሞቼ፡ተለየሁ፡ለናቴ፡ልጆችም፡እንግዳ፡ሆንሁ፡፡
፱፡ የቤትኽ ፡ ቅንዓት ፡ በልታኛለችና ፡፡
የሚለገዱኽም ፡ መለገድ ፡ በላዬ ፡ ወደቀ ፡፡
፲፡ አለቀስሁ ፡ ነፍሴንም ፡ በጾም ፡ አሳዘንሁ ፡፡ እርሱም ፡ ለ
ስድብ ፡ ሆነብኝ ፡፡
፲፩፡ ማቅ ፡ ለበስሁ ፡ ምሳሌም ፡ ሆንኋቸው ፡፡
፲፪፡ በደጅ ፡ የሚቀመጡ ፡ በኔ ፡ ይጫወታሉ ፡፡
በኔም ፡ ይዘፍናሉ ፡ ሰካሮች ፡፡
፲፫፡ የኔ ፡ ጸሎት ፡ ግን ፡ ወዳንተ ፡ ነው ፡ አቤቱ ፡፡
የተወደደ ፡ ዘመን ፡ ይሁን ፡ አቤቱ ፡ በምሕረትኽ ፡ ብዛት ፡፡
በማዳንኽ ፡ እውነት ፡ መልስልኝ ፡፡
፲፬፡ ከረግረግ ፡ አውጣኝ ፡ እንዳይውጠኝ ፡፡
ከሚጸሉኝ ፡ አስጥለኝ ፡ ከውኃ ፡ ጥልቅም ፡፡
፲፭፡ የውኃ ፡ሞገድ ፡ አያስጥመኝ ፡ ጥልቅም ፡ አይዋጠኝ ፡፡
ጕድጓድም ፡ አፉዋን ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ አትዝጋ ፡፡
፲፮፡ ስማኝ ፡ አቤቱ ፡ ምሕረትኽ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡፡
እንደ ፡ ርኅራኄኽ ፡ ብዛትም ፡ ወደኔ ፡ ተመልከት ፡፡
፲፯፡ ከባርያኽም ፡ ፊትኽን ፡ አትሰውር ፡ ተጨንቄያለሁና ፡፡ ፈ
ጥነኽ ፡ መልስልኝ ፡፡
፲፰፡ ለነፍሴ ፡ ቅረብ ፡ ተበዣትም ፡፡ ስለ ፡ ጸላቶቼ ፡ አድነኝ ፡፡
፲፱፡ አንተ ፡ ስድቤን ፡ ታውቃለኽ ፡ ኃፍረቴንም ፡ነውሬንም ፡፡
መከራ ፡ የሚያመጹብኝ ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ ፊት ፡ ናቸው ፡፡
፳፡ ኀፍረት ፡ ልቤን ፡ ሰበረች ፡፡ አዝኜ ፡ ተቀመጥሁ ፡
አይዞኽ ፡ የሚለኝም ፡የለም ፡ የሚያዝኑልኝንም ፡ አጣሁ ፡፡
፳፩፡ በመብሌም ፡ ከርቤ ፡ ጨመሩ ፡ ለጽማቴም ፡ መጣጣ ፡ አ
ጠጡኝ ፡፡
፳፪፡ ማዕዳቸው ፡ ወጥመድ ፡ ትሁንላቸው ፡ በፊታቸው ፡፡
ለብድራትም ፡ ለንቅፋትም ፡፡
፳፫፡ ዓይኖቻቸው ፡ ይጨልሙ ፡ እንዳያዩ ፡ ወገባቸውም ፡ ደና
ወጥ ፡ ሁለግዜ ፡፡



፳፬፡ በላያቸው ፡ መዓትኽን ፡ አፍስስ ፡ የቍጣኽም ፡ ትኵሳት ፡
ያዛቸው ፡፡
፳፭፡ ማደርያቸው፡ደፍረስ፡በድንኳናቸውም፡የሚኖር፡አይኑር፡፡
፳፮፡ አንተ ፡ የመታኸውን ፡ እርሳቸው ፡ አሳደዋልና ፡፡
ያቈሰልኻቸውም ፡ ያሳዝኑ ፡ ዘንድ ፡ ተጫወቱ ፡፡
፳፯፡ በኃጢአታቸው ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ጨምርባቸው ፡ በጽድቅ
ኽም ፡ አይግቡ ፡፡
፳፰፡ ከሕያዋን ፡ መጽሐፍ ፡ ይጥፉ ፡ ከጻድቃን ፡ ጋራም ፡ አይጻፉ ፡፡
፳፱፡ እኔ ፡ ግን ፡ ችጋረኛ ፡የቈሰልሁም ፡ ነኝ ፡፡
መድኃኒትኽ ፡ ትጠብቀኝ ፡ አቤቱ ፡፡
፴፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በዝማሬ ፡ አመሰግናለሁ ፡
በምስጋናም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርገዋለሁ ፡፡
፴፩፡ ይኽም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ፡ ከወይፈን ፡
ይልቅ ፡ ቀንድና ፡ ጽፍር ፡ ካበቀለ ፡፡
፴፪፡ ችጋረኞች ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡፡
እግዚአብሔርንም ፡ የምትሹት ፡ ልባችሁ ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ፡፡
፴፫፡ እግዚአብሔር ፡ ችጋረኞችን ፡ ሰምቶዋልና ፡
እሥሮቹንም ፡ አልናቀምና ፡፡
፴፬፡ ሰማይና ፡ ምድር ፡ ያመሰግኑታል ፡፡
ባሕርም ፡ በርስዋም ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ ሁሉ ፡፡
፴፭፡ እግዚአብሔር ፡ ፅዮንን ፡ አድንዋታልና ፡ የይሁዳንም ፡
አገሮች ፡ ይሠራልና ፡፡
ከዚያም ፡ ይቀመጣሉ ፡ ይወርስዋትማል ፡፡
፴፮፡ የባሮቹም ፡ ዘር ፡ ይወርስዋታል ፡
ስሙንም ፡ የሚወዱ ፡ በርስዋ ፡ ያድራሉ ፡፡

መዝሙር ፡ ፷፱፡

፩፡ አቤቱ ፡ እኔን ፡ ለማዳን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ እኔን ፡ ለ
መርዳት ፡ ፍጠን ፡፡
፪፡ ይፈሩ ፡ ይነወሩም ፡ ነፍሴን ፡ የሚሿት ፡፡
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ይፈሩም ፡ ክፉ ፡ የሚሹብኝ ፡፡
፫፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ድንገት ፡ አፍረው ፡ እንኳ ፡ እ
ንኳ ፡ የሚሉኝ ፡፡

፬፡ ባንተ፡ሐሤት፡ያድርጉ፡ደስም፡ይበላቸው፡የሚሹኽ፡ሁሉ።
ሁለግዜም ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ይበሉ ፡ ማደን
ኽን ፡ የሚወዱ ።
፭፡ እኔስ ፡ ችጋረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝ ።
አቤቱ ፡ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፈጠን ።
ረጂ ፡ ታዳጊዬም ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ አቤቱ ፡ አትዘግይ ።

---

## አሥረ ፡ አራተኛ ፡ ቀን ።

## የጽዋት ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፸፩፡

፩፡ አንተን ፡ አመንሁ ፡ አቤቱ ። ለዘላለም ፡ አልፈር ።
፪፡ በጽድቅኽ ፡ አስጥለኝ ፡ ታደገኝም ።
ጆሮኽን ፡ ወደኔ ፡ ጣል ፡ አድነኝም ።
፫፡ አንተ ፡ ላምባና ፡ ለመሸሸግያ ፡ ሁንልኝ ፡ ሁለግዜ ፡ አገባበ
ት ፡ ዘንድ ።
እኔን ፡ ለማደን ፡ አዘዝኽ ። አንተ ፡ መጸጊዬና ፡ አምባዬ ፡
ነኽና ።
፬፡ አምላኬ ፡ ካመፀኛ ፡ እጅ ፡ አድነኝ ። ከግፈኛና ፡ ከሁከተ
ኛም ፡ ጽፌ ።
፭፡ አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነኽና ፡ አቤቱ ።
ከታናሽነቴም ፡ ጀምረኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ መታመኛ
ዬ ፡ ነኽ ።
፮፡ ከማሕፀን ፡ ባንተ ፡ ተደገፍሁ ። ከናቴ ፡ ሆድ ፡ አንተ ፡ አ
ወፃኸኝ ።
ሁለግዜም ፡ ላንተ ፡ ምስጋናዬ ፡ ነው ።
፯፡ ለብዙ ፡ እንደ ፡ ታምራት ፡ ሆንሁ ። አንተ ፡ ግን ፡ ብርቱ ፡
መታመኛዬ ፡ ነኽ ።
፰፡ አፌን ፡ ምስጋናኽን ፡ ምላ ። ክብርኽንም ፡ ሁለግዜ ።
፱፡ በርጅና ፡ ዘመን ፡ አጣለኝ ።
ኃይሌ ፡ ስታልቅብኝ ፡ ጊዜ ፡ አተወኝ ።
፲፡ ጸላቶቼ ፡ በላዬ ፡ ተናገረዋልና ።



ነፍሴንም ፡ የሚጠብቁ ፡ ባንድ ፡ ተማከሩ ።
፲፩፡ አሉም ፡ እግዚአብሔር ፡ ተወው ። ተከተሉት ፡ ያዙትም ፡
የሚያድነው ፡ የለምና ።
፲፪፡ አምላኬ ፡ ከኔ ፡ አትራቅ ። አምላኬ ፡ እኔን ፡ ለመርደት ፡
ፈጠን ።
፲፫፡ ይፈሩ ፡ ይጥፉም ፡ ነፍሴን ፡ የሚቃወሙ ።
ኅፍረትና ፡ ኃሳር ፡ ይልበሱ ፡ መጐዳቴን ፡ የሚፈልጉ ።
፲፬፡ እኔ ፡ ግን ፡ ወትሮ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ።
በምስጋናኽም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጨምራለሁ ።
፲፭፡ አፌ ፡ ጽድቅኽን ፡ ይነግራል ፡ ሁለግዜም ፡ መድኃኒትኽን ።
ቍጥሩን ፡ አላውቅምና ።
፲፮፡ በጌታዬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ እገባለሁ ።
ጽድቅኽን ፡ ብቻ ፡ አሳስባለሁ ።
፲፯፡ አስተማርኸኝ ፡ አምላኬ ፡ ከታናሽነቴ ፡ ጀምረኽ ።
እስከ ፡ ዛሬም ፡ ታምራትኽን ፡ እናገራለሁ ።
፲፰፡ እስካረጅም ፡ ደግሞ ፡ እስክሸመግልም ፡ ድረስ ፡ አተወኝ ፡
አምላኬ ።
ክንድኽን ፡ ለዚች ፡ ትውልድ ፡ እስክነግር ፡ ድረስ ፡
ኃይልኽንም ፡ ለሚመጻ ፡ ሁሉ ።
፲፱፡ ጽድቅኽም ፡ አቤቱ ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፡
የሰራኸውም ፡ ስራ ፡ ታላቅ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ ማነው ፡ እንደንተ ፡ ያለ ።
፳፡ ብዙና ፡ ክፉ ፡ ጭንቀት ፡ አሳየኸኛልና ።
መልሰህም ፡ ታድነኛለኽ ፡
ከምድርም ፡ ጥልቅ ፡ መልሰኽ ፡ ታወጻኛለኽ ።
፳፩፡ ታላቅነቴን ፡ ታበዛለኽ ፡ በመጸናናትም ፡ ትከበኛለኽ ።
፳፪፡ እኔም ፡ በበገና ፡ እቃ ፡ አመሰግንኻለሁ ፡
ለውነትኽም ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ በመሰንቆ ፡ ዝማሬ ፡ አቀ
ርብልኻለሁ ፡
የእሥራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ሆይ ።
፳፫፡ ከንፈሮቼ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ዝማሬን ፡ አቅርብልኻለሁና ።
የተበዣኻትም ፡ ነፍሴ ።

፳፬፡ መላሴም ፡ ደግሞ ፡ ጽድቅኽን ፡ ሁለግዜ ፡ ይናገራል ።
መጕዳቴን ፡ የሚሹ ፡ ነውረዋልና ፡ አፈረውማልና ።

## መዝሙር ፡ ፸፪፡

፩፡ አቤቱ ፡ ፍርድኽን ፡ ለንጉሠ ፡ ስጥ ። ጽድቅኽንም ፡ ለን ጉሠ ፡ ልጅ ።
፪፡ ሕዝብኽን ፡ በጽድቅ ፡ ይደኝ ፡ ዘንድ ። ችጋረኞችኽንም ፡ በፍርድ ።
፫፡ ተራሮች ፡ ለሕዝቡ ፡ ሰላምን ፡ ያመጻሉ ፡ ኮረፍቶችም ፡ በጽድቅ ።
፬፡ ለሕዝብ ፡ ነዳያን ፡ ይፈርዳል ።
የድኆችንም ፡ ልጆች ፡ ያድናል ፡
ዐቡይንም ፡ ያደቃል ።
፭፡ ፀሐይ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይፈሯኻል ፡
በጨረቃም ፡ ፊት ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ።
፮፡ እንደ ፡ ዝናም ፡ በታጨደ ፡ መስክ ፡ ላይ ፡ ይወርዳል ፡
በምድር ፡ ላይም ፡ እንደሚረጨ ፡ እንደ ፡ ነጠብጣብ ።
፯፡ በዘመኑም ፡ ጻድቅ ፡ ያብባል ።
ጨረቃም ፡ እስኪያልቅ ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ሰላም ።
፰፡ ከባሕርም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ይገዛል ፡
ከፈሳሽም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ።
፱፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚቀመጡ ፡ በፊቱ ፡ ይምበረከካሉ ።
ጸላቶቹም ፡ አፈርን ፡ ይልሳሉ ።
፲፡ የተርሴስና ፡ የደሴቶች ፡ ነገሥታት ፡ ስጥወታውን ፡ ያገባሉ ።
የሸባና ፡ የሰባም ፡ ነገሥት ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ያቀርባሉ ።
፲፩፡ ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፡ ይሰግዱለታል ።
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ይገዙለታል ።
፲፪፡ የሚጮኸውን ፡ ችጋረኛን ፡ ያድናልና ።
ምስኪንንም ፡ ረጅ ፡ የሌለውን ።
፲፫፡ ለነዳይ ፡ ለምስኪንም ፡ ይራራል ።
የችጋረኞችንም ፡ ነፍስ ፡ ያድናል ።
፲፬፡ ከግፍና ፡ ከጭንቀትም ፡ ነፍሳቸውን ፡ ያድናል ።



ደማቸውም ፡ በፊቱ ፡ ክቡር ፡ ይሆናል ።
፲፭፡ ሕያውም ፡ ይሆናል ፡ ከሸባም ፡ ወርቅ ፡ ይሰጡታል ።
ሁለግዜም ፡ ወደርሱ ፡ ይጸልያሉ ፡ ዘወትርም ፡ ይባርኩታል ።
፲፮፡ ስንዴ ፡ በምድር ፡ መልቶ ፡ ይሆናል ፡ በተራሮች ፡ ራስ ፡
ፍሬውም ፡ እንደ ፡ ልባኖስ ፡ ዛፍ ፡ ይወዘውዛል ።
ያገርም ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ እሳር ፡ ይለመልማሉ ።
፲፯፡ ስሙ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
ስሙ ፡ በጸሐይ ፡ ፊት ፡ ይዘወትራል ።
በርሱ ፡ ይባረከሉ ፡ የምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑታል ።
፲፰፡ እግዚአብሔር፡አምላክ፡የእሥራኤል፡አምላክ፡ይባረክ፡
ብቻውን ፡ ታላቅ ፡ ድንቅ ፡ የሚያደርግ ።
፲፱፡ የምስጋናው ፡ ስምም ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ።
ምስጋናውም ፡ ይምላ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ።
፳፡ አሜን ። አሜን ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፸፫፡

፩፡ በውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእሥራኤል ፡ ቸር ፡ ነው ፡ ልባ ቸው ፡ ለንጻ ።
፪፡ እኔ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ቀረ ፡ እግሮቼ ፡ ፍግምግ ፡ እንዳይሉ ።
ጥቂት ፡ አረጋገጤም ፡ ዳጽ ፡ ባለ ።
፫፡ በዐቡያን ፡ ላይ ፡ ቀንቼ ፡ ነበርሁና ።
የዓማፅያንን ፡ ሰላም ፡ አይቼ ።
፬፡ ለሞታቸው ፡ መጣጣር ፡ የለውምና ።
መግዛታቸውም ፡ በጅ ፡ ይላቸዋልና ።
፭፡ በሰው ፡ ድካም ፡ አልተገኙም ። ከሰውም ፡ ጋራ ፡ አልተ ገረፉም ።
፮፡ ስለዚኽ ፡ ትዕቢት ፡ ያሽልማቸዋል ።
ግፍ ፡ ማድረጋቸውን ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ተጐናጸፈዋት ።
፯፡ ዓይኖቸው ፡ ከስብ ፡ ትወፃለች ። የልባቸውንም ፡ መሻት ፡ አለፉ ።

፰፤ ተላገዱ ፡ በክፋትና ፡ በግፍም ፡ ተናገሩ ። ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብለ
ውም ፡ ተናገሩ ።
፱፤ በሰማይ ፡ አፋቸውን ፡ አኖሩ ። በምድርም ፡ መላሳቸው ፡
ተመላለሰ ።
፲፤ ስለዚኽ ፡ ሕዝቡም ፡ ወደዚያ ፡ ይመለሳሉ ።
ብዙም ፡ ውኃ ፡ ለርሳቸው ፡ ይገኛል ።
፲፩፤ አሉም ፡ እንዴት ፡ ያውቃል ፡ እግዚአብሔር ።
ለልዑልስ ፡ እውቀትን ፡ አለው ።
፲፪፤ እነሆ ፡ እሌኽ ፡ ኃጢአተኞች ።
በምድር ፡ ላይም ፡ ደስ ፡ ብልዋቸዋል ፡ ባለጠግነታቸውንም ፡
ያበዛሉ ።
፲፫፤ አልሁም ፡ በከንቱ ፡ እንጀ ፡ ልቤን ፡ አነጻሁ ።
እጀንስ ፡ በንጽሕና ፡ አፀብሁ ።
፲፬፤ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ የተገረፍሁ ፡ ሆንሁ ፡
ተግሣጼም ፡ ማልደ ፡ ማልደ ፡ ይመለሳል ።
፲፭፤ ብልም ፡ እንዲሁም ፡ እናገራለሁ ። እነሆ ፡ የልጆችኽን ፡ ዘ
ር ፡ እበድላለሁ ።
፲፮፤ ይኽነንም ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ አሰብሁ ።
ደሮ ፡ በፊቴ ፡ ይቸግረኝ ፡ ነበር ።
፲፯፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ እስክገባ ፡ ድረስ ፡
ፍጻሜያቸውንም ፡ እስተዋልሁ ።
፲፰፤ አንተ ፡ በደፅ ፡ ስፍራ ፡ አቆምኻቸው ። ለጥፋትም ፡ ጣል
ኻቸው ።
፲፱፤ እንዴት ፡ ድንገት ፡ ለጥፋት ፡ ሆኑ ። አለቁ ፡ በግርማም ፡
ተፈጁ ።
፳፤ እንደ ፡ ሕልም ፡ ከንቅልፍ ፡ ለሚነቃ ፡
እንዲሁም ፡ ባገርኽ ፡ መልካቸውን ፡ ታስነውራለኽ ፡ አቤቱ ።
፳፩፤ ልቤ ፡ ነድዋልና ፡ ኵላሊቴም ፡ ተወገቶብኛልና ።
፳፪፤ እኔስ ፡ ደንቆሮ ፡ ነኝ ፡ አላወቅሁምም ።
ባንተ ፡ ዘንድም ፡ እንደ ፡ እንስሳ ፡ ሆንሁ ።
፳፫፤ እኔ ፡ ግን ፡ ወትሮ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ነኝ ። ቀኝ ፡ እጀንም ፡ ያዝ
ኸኝ ።



፳፬፤ በምክርኽ ፡ ታደላድለኛለኽ ፡
በኋላም ፡ ለምስጋና ፡ ትቀበለኛለኽ ።
፳፭፤ ምንድር ፡ ነው ፡ በሰማይ ፡ ያለኝ ፡
ካንተም ፡ በቀር ፡ ምን ፡ እሻለሁ ፡ በምድር ።
፳፮፤ ልቤና ፡ ሥጋዬ ፡ አለቀ ።
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የልቤ ፡ አምባ ፡ ነው ፡
ፈንታዬም ፡ ነው ፡ ለዘላለም ።
፳፯፤ እነሆ ፡ ካንተ ፡ የሚርቁ ፡ ይጠፋሉና ፡
ካንተ ፡ የሚያመነዝሩትን ፡ ሁሉ ፡ አጠፋኻቸው ።
፳፰፤ ለኔ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ መቅረብ ፡ ይሻለኛል ።
መታመኔም ፡ በእግዚአብሔር ፡ በጌታዬ ፡ ነው ፡
ስራኽን ፡ ሁሉ ፡ እነግር ፡ ዘንድ ።

መዝሙር ፡ ፸፬፤

፩፤ ለምን ፡ ፈጽመኽ ፡ ጣልኽነ ፡ አቤቱ ።
ቍጣኽ ፡ በመሰማርያኽ ፡ በጎች ፡ ላይ ፡ ይጤሳል ።
፪፤ ጉባዔኽን ፡ አስብ ፡ የገዛኻትን ፡
የርስትኽንም ፡ በትር ፡ አስቀድመኽ ፡ የተበዣኻትን ፡
የፅዮንን ፡ ተራራ ፡ በርስዋ ፡ ያደርኽባትን ።
፫፤ እግርኽን ፡ አንሣ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ መፈታት ።
ምን ፡ ያህል ፡ በመቅደስኽ ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፡ ጸላት ።
፬፤ ጸላቶችኽ ፡ በጉባኤዎችኽ ፡ ማኽል ፡ ጮኹ ፡
ምልክታቸውን ፡ ምልክት ፡ አደረጉ ።
፭፤ እንጨት ፡ በሚበዛበት ፡ ድን ፡ ላይ ፡ ምሳርን ፡ አንሥቶ ፡
እንደሚያገባው ፡ ይታወቃል ፡
፮፤ አሁንም ፡ መግቢዎችዋን ፡ ሁሉ ፡ በምሳርና ፡ በመዶቻ ፡
ደወቃሉ ።
፯፤ መቅደስኽን ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ፡
የስምኽንም ፡ ማደርያ ፡ በምድር ፡ ጥለው ፡ አረከሱ ።
፰፤ በልባቸው ፡ አንድ ፡ ሁነን ፡ ኑ ፡ እናጥፋቸው ፡ አሉ ።
በምድር ፡ ያለውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የበዓሉን ፡ ስፍ
ራ ፡ ሁሉ ፡ አቃጠሉ ።

፱፡ ምልክታችንን ፡ አላየነም ፡ ነቢይም ፡ የለም ፡፡
በኛም ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ እንዲኖር ፡ የሚያው
ቅ ፡ የለም ፡፡
፲፡ ጸላት ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይሰድባል ፡ አቤቱ ፡፡
ጸላት ፡ ሁለግዜ ፡ ስምኽን ፡ ሊያቃልለውን ፡፡
፲፩፡ ለምን ፡ እጅኽን ፡ ትመልሳለኽ ፡፡
ቀኝኽን ፡ ከብብትኽ ፡ ማኽል ፡ አውጣ ፡፡
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከድሮ ፡ ዘመን ፡ ንጉሣ ፡ ነው ፡፡
በምድር ፡ መኻከል ፡ መድኃኒት ፡ አደረገ ፡፡
፲፫፡ አንተ ፡ በኃይልኽ ፡ ባሕርን ፡ ሰነጠቅኽ ፡፡
አንተ ፡ የባብን ፡ ራሶች ፡ በውኃ ፡ ሰበርኽ ፡፡
፲፬፡ አንተ ፡ የሌዋታንን ፡ ራሶች ፡ ቀጠቀጥኽ ፡፡
ለምድረ ፡ በዳ ፡ ወገንም ፡ ምግብ ፡ አድርገኽ ፡ ሰጠኸው ፡፡
፲፭፡ አንተ ፡ ምንጭንና ፡ ፈሳሽን ፡ ከፈትኽ ፡
አንተ ፡ ታላቆች ፡ ወንዞችን ፡ አደረቅኽ ፡፡
፲፮፡ መዐልትም ፡ ሌትም ፡ ያንተ ፡ ነው ፡፡
አንተ ፡ ብርሃኑን ፡ ጸሐይንም ፡ ፈጠርኽ ፡፡
፲፯፡ አንተ ፡ የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ሰራኽ ፡፡
በጋንም ፡ ክረምትን ፡ አንተ ፡ ፈጠርኽ ፡፡
፲፰፡ ይህነን ፡ አስብ ፡፡ ጸላት ፡ ተላገደ ፡ አቤቱ ፡
ሰነፍ ፡ ሕዝብም ፡ ስምኽን ፡ ናቀው ፡፡
፲፱፡ የዋልያኽን ፡ ነፍስ ፡ ለአራዊት ፡ አሳልፈኽ ፡ አትስጣት ፡፡
የችጋረኞችኽን ፡ ሕይወት ፡ ለዘላለም ፡ አትርሳ ፡፡
፳፡ ወደ ፡ ኪዳንኽ ፡ ተመልከት ፡፡
የጨለሙ ፡ የምድር ፡ ቤቶች ፡ ግፍን ፡ በመውደድ ፡ መል
ተዋልና ፡፡
፳፩፡ ችጋረኛ ፡ አፍሮ ፡ አይመለስ ፡፡
ችጋረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ስምኽን ፡ ያመስግኑ ፡፡
፳፪፡ ተነሣ ፡ አቤቱ ፡ በቀልኽን ፡ ተበቀል ፡፡
ሁለግዜ ፡ የተላገደኽን ፡ የሰነፎችን ፡ ስድብ ፡ አስብ ፡፡
፳፫፡ የጸላቶችኽን ፡ ቃል ፡ አትርሳ ፡፡
የጸላቶችኽ ፡ ኵራት ፡ ሁለግዜ ፡ ይወጣልና ፡፡



## መዝሙር ፡ ፸፭፡

፩፡ እናመሰግንኻለን ፡ አቤቱ ፡ እናመሰግንኻለን ፡፡
ስምኽ ፡ ቅርብ ፡ ነውና ፡ ታምራቶችኽ ፡ እንዲገልጹት ፡፡
፪፡ ጉባኤውን ፡ ስቀበል ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ በቅን ፡ እፈርዳለሁ ፡፡
፫፡ ምድር ፡ ቀለጠች ፡ በርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡፡
እኔ ፡ ዓምዶችዋን ፡ አጸናሁ ፡፡
፬፡ የኰሩትን ፡ አትኰሩ ፡ አልኋቸው ፡፡
ዐመፀኞችንም ፡ ቀንዳችሁን ፡ አታንሡ ፡፡
፭፡ ቀንዳችሁን ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ አታንሡት ፡፡
በደነደነም ፡ አንገት ፡ አትናገሩ ፡፡
፮፡ ክብር ፡ ከምሥራቅ ፡ የለምና ፡ ከምራዕብም ፡ የለም ፡
ከምድረ ፡ በዳም ፡ የለም ፡፡
፯፡ እግዚአብሔር ፡ ፈራጅ ፡ ነውና ፡
ይህነን ፡ ያወርዳል ፡ ይህነንም ፡ ያነሣል ፡፡
፰፡ ጽዋዕ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ነውና ፡
በዘፈዘፈ ፡ ፀጅ ፡ የመላ ፡ የተቀላቀለ ፡ ከርሱም ፡ ያፈሳል ፡፡
ነገር ፡ ግን ፡ አተላውን ፡ የምድር ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ ያገ
ኙሉና ፡ ይጠጣሉ ፡፡
፱፡ እኔ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ እነግራለሁ ፡፡
ለያዕቆብ ፡ አምላክም ፡ ዝማሬን ፡ አቀርባለሁ ፡፡
፲፡ የኃጥአንንም ፡ ቀንዶች ፡ ሁሉ ፡ እቈርጣለሁ ፡፡
የጻድቅ ፡ ቀንዶች ፡ ግን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፸፮፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ በይሁዳ ፡ የታወቀ ፡ ነው ፡፡
በእሥራኤልም ፡ ስሙ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡፡
፪፡ ደሱም ፡ በሳሌም ፡ ነው ፡ ማደርያውም ፡ በፅዮን ፡፡
፫፡ በዚያ ፡ የቀስትን ፡ ፍላጾች ፡ ሰበረ ፡፡
ጋሻንም ፡ ሰይፍንም ፡ ዘምቻንም ፡፡
፬፡ አንተ ፡ በክብር ፡ ታበራለኽ ፡ ከነጣቅያን ፡ ተራሮች ፡ ይልቅ፡፡
፭፡ ልበ ፡ ብርቶች ፡ ተቀሙ ፡፡ እንቅልፋቸውንም ፡ አንቀላፉ ፡
ኃያላንም ፡ ሁሉ ፡ እጃቸውን ፡ አላገኙም ፡፡

፮ ፡ ከዘለፋኽ ፡ የተኛ ፡ የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡
ሠረገሎችና ፡ ፈረሶች ፡ አንቀላፉ ።
፯ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አንተ ፡ የተፈራኽ ፡ ነኽ ።
ማንስ ፡ በፊትኽ ፡ ይቆማል ፡ ቍጣህ ፡ ሲጀመር ፡ ጊዜ ።
፰ ፡ ከሰማይ ፡ ፍርድን ፡ አሰማኽ ። ምድርም ፡ ፈራች ፡ ዝም ፡ አለች ፡
፱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለፍርድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡
የምድርን ፡ ገሮች ፡ ሁሉ ፡ ለማደን ።
፲ ፡ የሰው ፡ ቍጣ ፡ ያመሰግንኻልና ። የቍጣውንም ፡ ትርፍ ፡ ትከለክለዋለኽ ።
፲፩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ተሳሉ ፡ ስጡም ።
በዙርያው ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ለተፈራ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ያግቡ ።
፲፪ ፡ ያለቆችን ፡ ነፍስ ፡ የቈረጠ ፡ ለምድርም ፡ ነገሥት ፡ ግሩም ፡ ያለ ።

## መዝሙር ፡ ፸፮

፩ ፡ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ።
በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመንሁ ፡ እርሱም ፡ አደመጠኝ ።
፪ ፡ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እሻሁት ።
እጄን ፡ በሌት ፡ በፊቱ ፡ ዘረጋሁ ፡ አላረፍሁምም ።
ነፍሴም ፡ ለመጽናናት ፡ እምቢ ፡ አለች ።
፫ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አሰብሁት ፡ አዘኜ ። አሰብሁም ፡ ነፍሴም ፡ ተቅበዘበዘች ።
፬ ፡ ዓይኖቼን ፡ እንዲተጉ ፡ ያዝኻቸው ፡
ደነገፅሁም ፡ አልናገርምም ።
፭ ፡ የድሮውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ፡ የዓለሙን ፡ ዓመታት ።
፮ ፡ በሌት ፡ የተናገርሁትን ፡ ዝማሬን ፡ አሰብሁ ።
ከልቤም ፡ ጋራ ፡ ተጫወትሁ ፡
መንፈሴም ፡ ተግቶ ፡ ይመረምራል ።
፯ ፡ በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለምን ፡ ይጥላል ።
ጸጋውንም ፡ እንጊዴኽ ፡ አይደግምምን ።
፰ ፡ በውንስ ፡ ፈጽሞ ፡ ምሕረቱ ፡ አለቀች ።
የተናገረውም ፡ ነገር ፡ ለልጅ ፡ ልጅን ፡ ቀረች ።



፱ ፡ በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርኅራኄውን ፡ ረሳ ።
ምሕረቱንስ ፡ በመዓቱን ፡ ከለከለ ።
፲ ፡ አልሁም ፡ ደኽ ፡ ድካሜ ፡ ነው ። የልዑልም ፡ የቀኙ ፡ መለዋወጥ ።
፲፩ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አደራረግ ፡ አስባለሁ ።
የቀደመውን ፡ ታምራትኽን ፡ አስባለሁና ።
፲፪ ፡ በስራኽም ፡ ሁሉ ፡ ተናገርሁ ።
በስራውም ፡ ሁሉ ፡ እጫወታለሁ ።
፲፫ ፡ መንገድኽ ፡ አቤቱ ፡ በመቅደስ ፡ ነው ።
ማነው ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፬ ፡ አንተ ፡ ታምራት ፡ የምታደርግ ፡ አምላክ ፡ ነኽ ።
ኃይልኽን ፡ በአሕዛብ ፡ አሳየኽ ።
፲፭ ፡ ሕዝብኽን ፡ በክንድኽ ፡ አደንኻቸው ።
የያዕቆብንና ፡ የዮሴፍን ፡ ልጆች ።
፲፮ ፡ ውኆች ፡ አዩኽ ፡ አቤቱ ። አዩኽ ፡ ውኆች ፡ ተጨነቁም ።
ቀላዮችም ፡ ተንቀጠቀጡ ።
፲፯ ፡ ደመኖች ፡ ውኃውን ፡ አፈሰሱ ። ደመናትም ፡ ድምፅን ፡ ሰጡ ።
ፍላፆችኽ ፡ እንኳ ፡ ተመላለሱ ።
፲፰ ፡ የነጐድጓድኽ ፡ ድምፅ ፡ በኩርፌት ፡ ነበር ።
መብረቆችም ፡ ዓለምን ፡ አበሩ ።
ምድርም ፡ ተናወጸች ፡ ተንቀጠቀጠችም ።
፲፱ ፡ መንገድኽ ፡ በባሕር ፡ ነው ፡ ፍለጋኽም ፡ በብዙ ፡ ውኆች ፡ ነው ።
አረጋገጥኽም ፡ አይታወቅም ።
፳ ፡ ሕዝብኽን ፡ መራኻቸው ፡ እንደ ፡ በጎች ።
በሙሴና ፡ በሐሮን ፡ እጅ ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፸፯

፩ ፡ ሕዝቤ ፡ ሕጌን ፡ አድምጡ ።
ጆሮዋችሁን ፡ ወደፊ ፡ ነገር ፡ ጣሉ ።
፪ ፡ አፌን ፡ በምሳሌ ፡ እከፍታለሁ ።

ከድሮ ፡ ምሳሌን ፡ አውጥቻለሁና ::
፫ የሰማነውን ፡ ያወቅነውንም ፡ አባቶቻችንም ፡ የነገሩነውን ::
፬ ከልጆቻቸው ፡ እንደንሰውረው ፡
ለሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ እንድ
ንነግር ፡ እንጂ ::
ኃይሉንም ፡ ያደረገውንም ፡ ታምራት ::
፭ ምስክርንም ፡ በያዕቆብ ፡ አቆመ ፡
በእሥራኤልም ፡ ሕጉን ፡ ሰራ ::
ላባቶቻችን ፡ ያዘዘውን ፡ ልጆቻቸውን ፡ ያስታውቁባት ፡
ዘንድ ፡
፮ የሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ ያውቀው ፡ ዘንድ ፡ የሚወለዱ ፡ ል
ጆቻቸው ፡
እርሳቸው ፡ ተነሥተው ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ::
፯ መታመናቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንዲያደርጉ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ስራ ፡ እንደይደረሱ ::
ትእዛዙንም ፡ እንዲጠብቁ ::
፰ እንደባቶቻቸውም ፡ እንደይሆኑ ፡
ጠማማ ፡ ትውልድ ፡ የምታስመርርም ፡
ልብዋን ፡ ያላቀናች ፡ ትውልድ ፡ ነፍስዋም ፡ በእግዚአብሐ
ር ፡ ያልታመነች ::
፱ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ስለት ፡ የታጠቁ ፡ በቀስትም ፡ የ
ወረወሩ ፡
በሰልፊ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመለሱ ::
፲ የእግዚአብሔርን ፡ ኪዳን ፡ አልጠበቁም ::
በሕጉም ፡ ለመመላለስ ፡ እንቢ ፡ አሉ ::
፲፩ ስራውንም ፡ ሁሉ ፡ ረሱ ፡ ያሳያቸውንም ፡ ታምራት ፡
፲፪ ባባቶቻቸው ፡ ፊት ፡ የሰራውን ፡ ታምራት ::
በግብጽ ፡ አገር ፡ በጣኔዎስም ፡ ገደም ::
፲፫ ባሕርን ፡ ከፍሎ ፡ አሳለፋቸው ፡
ውኃውንም ፡ እንደ ፡ መደብ ፡ አቆመ ::
፲፬ በቀንም ፡ በደመና ፡ መራቸው ፡
ሌቱንም ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ብርሃን ::



፲፭ አምቦችን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሰነጠቀ ፡
አጠጣቸውም ፡ እንደ ፡ ከብዙ ፡ ቀላይ ፡
፲፮ ፈሳሾችንም ፡ ከደንጊያ ፡ አወፃ ፡
ውኃውንም ፡ እንደ ፡ ፈሳሾች ፡ አፈሰሰ ::
፲፯ ደግሞም ፡ ሊበድሉት ፡ደገሙ ፡
ልዑልንም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አስመረሩት ::
፲፰ እግዚአብሔርንም ፡ በልባቸው ፡ ፈተኑት ፡
ለነፍሳቸው ፡ መብል ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ::
፲፱ በእግዚአብሔር ፡ ላይም ፡ ተናገሩ ፡ አሉም ፡
በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ማዕድን ፡ ያሰናዳ ፡
ዘንድ ፡ ይችላልን ::
፳ አምባውን ፡ እነሆ ፡ መታ ፡ ውኃም ፡ ወጣ ፡ ፈሳሾችም ፡
ፈሰሱ ::
እንጀራ ፡ ደግሞ ፡ መስጠትስ ፡ ይችላልን ፡
ለሕዝቡስ ፡ ሥጋውን ፡ መስራት ::
፳፩ ስለዚኽም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማ ፡ ተቈጣም ፡
እሳትም ፡ በያዕቆብ ፡ ተቃጠለች ፡
መዓትም ፡ ወጣ ፡ በእሥራኤል ::
፳፪ በእግዚአብሔር ፡ አላመኑምና ፡ በማዳኑም ፡ አልተወከ
ሉምና ::
፳፫ ደመናውንም ፡ ከላይ ፡ አዘዘ ፡
የሰማይንም ፡ ደጆች ፡ ከፈተ ::
፳፬ መናም ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ አዘነበላቸው ፡
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ ሰጣቸው ::
፳፭ የክቡራንን ፡ እንጀራ ፡ ሰው ፡ በላ ፡
ስንቅንም ፡ ለጽጋብ ፡ ላከላቸው ::
፳፮ ከሰማይ ፡ የምሥራቅን ፡ ነፋስ ፡ አስነሣ ፡
በኃይሉም ፡ ዓዜቡን ፡ አስመጸ ::
፳፯ ሥጋም ፡ እንደ ፡ መሬት ፡ አዘነበላቸው ፡
እንደ ፡ በሕርም ፡ አሸዋ ፡ የሚበሩ ፡ አዕዋፍ ::
፳፰ በሰፈረም ፡ ማኽል ፡ ወደቁ ፡
በማደርያቸውም ፡ ዙርያ ::

፳፱፡ በሉም ፡ እጅግም ፡ ጸገቡ ፡
የሚያምራቸውንም ፡ ሰጣቸው ፡፡
፴፡ ፈቃዳቸውን ፡ አላሳጣቸውም ፡
መብላቸውም ፡ ገና ፡ ባፋቸው ፡ ሳለ ፡
፴፩፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ወጣባቸው ፡፡
በርሳቸውም ፡ የለመለሙትን ፡ ገደለ ፡
በእሥራኤልም ፡ የተመረጹትን ፡ አስወደቀ ፡፡
፴፪፡ ከዚኽም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ደግሞ ፡ በደሉ ፡
በታምራቱም ፡ አላመኑም ፡፡
፴፫፡ ቀናቸውም ፡ በከንቱ ፡ አለቀ ፡
አመታታቸውም ፡ በድንጋጤ ፡፡
፴፬፡ ሲገላቸው ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አሹት ፡
ተመለሱም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ማለዱ ፡፡
፴፭፡ እግዚአብሔርም ፡ አምባቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አሰቡ ፡
ልዑል ፡ አምላክም ፡ መድኃኒታቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡፡
፴፮፡ ባፋቸውም ፡ ወደዱት ፡ በመላሳቸውም ፡ አሰት ፡ ተናገሩ
በት ፡፡
፴፯፡ ልባቸውም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ አልቀናችም ፡
በኪዳኑም ፡ አላመኑም ፡፡
፴፰፡ እርሱ ፡ ግን ፡ መሐሪ ፡ ነው ፡ ኃጢአትንም ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡
አላጠፋቸውምም ፡ ቍጣውንም ፡ መመለስ ፡ አበዛ ፡
መዓቱንም ፡ ሁሉ ፡ አላስነሣም ፡፡
፴፱፡ ሥጋም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አሰበ ፡
እስትንፋስ ፡ የሚወፃ ፡ የማይመለስም ፡፡
፵፡ ምን ፡ ያህል ፡ አስቈጡት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
በውድማም ፡ አሳዘኑት ፡፡
፵፩፡ ተመለሱም ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ፈተኑ ፡
የእሥራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ ወሰኑ ፡፡
፵፪፡ እጁንም ፡ አላሰቡም ፡ ከጸላታቸውም ፡ እጅ ፡ ያዳናቸው
በትን ፡ ቀን ፡
፵፫፡ በምስር ፡ ታምራቱን ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፡
ድንቁንም ፡ በጣኔዎስ ፡ ገደም ፡፡



፵፬፡ ወንዛቸውን ፡ ለደም ፡ ለወጠ ፡፡
መስኖቻቸውንም ፡ እንዳይጠጥዋቸው ፡፡
፵፭፡ የውሻ ፡ ዝንብን ፡ ሰደደባቸው ፡ በላቸውም ፡
እንቁራቸርም ፡ አጠፋቸውም ፡፡
፵፮፡ ፍሬያቸውንም ፡ ለኩብኩባ ፡ ሰጠ ፡
የጻፉበትንም ፡ ላንበጣ ፡፡
፵፯፡ ወይናቸውንም፡በበረደ፡አጠፋ፡፡ወርካቸውንም፡በውርጭ ፡
፵፰፡ እንስሳቸውንም ፡ ለበረደ ፡ ሰጠ ፡፡
ከብታቸውንም ፡ ለመብረቅ ፡ እሳት ፡፡
፵፱፡ የቍጣውን ፡ መቅሠፍት ፡ ሰደደባቸው ፡
መቅሠፍትን ፡ መዓትንም ፡ አዘንንም ፡
ከክፉ ፡ መላእክት ፡ ጋራ ፡ ሰደደ ፡፡
፶፡ ለቍጣው ፡ መንገድ ፡ ጸረገ ፡፡
ለነፍሳቸው ፡ ከሞት ፡ አልራራላትም ፡
እንስሳቸውንም ፡ ለመርዝ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፡፡
፶፩፡ በኵሩንም ፡ ሁሉ ፡ በምስር ፡ ገደለ ፡
የጕልበታቸውን ፡ መጀመርያ ፡ በካም ፡ ቤቶች ፡፡
፶፪፡ ሕዝቡን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ በግ ፡ አወጣቸው ፡
እንደ ፡ መንጋም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አሳመራቸው ፡፡
፶፫፡ ለምነትም ፡ መራቸው ፡ አልፈሩምም ፡
ጸላቶቻቸውንም ፡ ባሕር ፡ ሸፈናቸው ፡፡
፶፬፡ ወደ ፡ መቅደሱም ፡ ደርቻ ፡ አገባቸው ፡
ወደዚህ ፡ ተራራ ፡ ቀኝ ፡ እጁ ፡ የገዛት ፡፡
፶፭፡ አሕዛብንም ፡ ከበፊታቸው ፡ አወጣላቸው ፡
ርስትም ፡ በገመድ ፡ ሰፍሮ ፡ አወረሳቸው ፡
የእሥራኤልንም ፡ ነገዶች ፡ በቤታቸው ፡ አስቀመጠ ፡፡
፶፮፡ ነገር ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈተኑት ፡ አሳዘኑትም ፡
ምስክሩንም ፡ አልጠበቁም ፡
፶፯፡ ተመለሱም ፡ እንደባቶቻቸውም ፡ ገበዙ ፡
ተገለበጡ ፡ እንደ ፡ ላላ ፡ ቀስት ፡፡
፶፰፡ በኮረፍታቸውም ፡ አሳዘኑት ፡
በጣዖታታቸውም ፡ አስቀኑት ፡፡

፶፱፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰምቶ ፡ ተቈጣ ፡
እሥራኤልንም ፡ እጅግ ፡ ናቀ ፡፡
፷፡ የሴሎንም ፡ መኖርያ ፡ ጣለ ፡፡
ድንኳኑን ፡ ከሰው ፡ ጋራ ፡ ያደረበትን ፡፡
፷፩፡ ኃይሉንም ፡ ለምርኮ ፡ ሰጠ ፡፡
ሸልሙንም ፡ በጸላቱ ፡ እጅ ፡፡
፷፪፡ ሕዝቡንም ፡ ለሰይፍ ፡ ሰጠ ፡፡
ርስቱንም ፡ ተቈጣው ፡፡
፷፫፡ ጉልማሶቻቸውን ፡ እሳት ፡ በላቻቸው ፡፡
ቈነጃጅቶቻቸውም ፡ አልተመሰገኑም ፡፡
፷፬፡ ካህናቶቻቸውም ፡ በሰይፍ ፡ ወደቁ ፡
ባልቴቶቻቸውም ፡ አላለቀሱላቸውም ፡፡
፷፭፡ እግዚአብሔርም ፡ ተነሣ ፡ ከምኝታ ፡ እንደሚነቃ ፡
በጸጅም ፡ ተሰክሮ ፡ እልል ፡ እንደሚል ፡ እንደ ፡ ኃያል ፡፡
፷፮፡ ጸላቶቹንም ፡ መታ ፡ በኋላቸው ፡፡
ለዓለምም ፡ ኀፍረት ፡ ሰጣቸው ፡፡
፷፯፡ የዮሴፍንም ፡ ድንኳን ፡ ተዋት ፡፡
የኤፍሬምንም ፡ ነገድ ፡ አልመረጸም ፡፡
፷፰፡ የይሁዳን ፡ ነገድ ፡ መረጸ ፡ እንጅ ፡
የፅዮንን ፡ ተራራ ፡ የወደደውን ፡፡
፷፱፡ እንደ ፡ ረጅም ፡ ቤትም ፡ መቅደሱን ፡ ሠራ ፡፡
ለዘላለምም ፡ እንደ ፡ መሠረታት ፡ ምድር ፡፡
፸፡ ባርያውንም ፡ ዳዊትን ፡ መረጸ ፡፡
ከበጎችም ፡ መንጋ ፡ ወሰደው ፡፡
፸፩፡ ከሚያጠቡ ፡ በኋላ ፡ ተቀበለው ፡፡
ሕዝቡን ፡ ያዕቆብን ፡ ርስቱንም ፡ እሥራኤልን ፡ ይጠብቅ ፡
ዘንድ ፡፡
፸፪፡ ጠበቃቸውም ፡ በልቡ ፡ ቅንነት ፡
በጆቹም ፡ ብልሀት ፡ መራቸው ፡፡



አሥራ ፡ ስድስተኛ ፡ ቀን ፡፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፸፱፡

፩፡ አቤቱ ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ ርስትኽ ፡ ገቡ ፡
የቅድስናኽንም ፡ መቅደስ ፡ አረከሱ ፡
የሩሳሌምን ፡ የፍራሾችን ፡ መደብ ፡ አደረጉ ፡፡
፪፡ የባሮችኽን ፡ በድን ፡ ለሰማይ ፡ ዎፎች ፡ መብል ፡ አደረጉ ፡
የጻድቃንኽንም ፡ ሥጋ ፡ ለምድር ፡ አራዊት ፡፡
፫፡ ደማቸውን ፡ በየሩሳሌም ፡ ዙርያ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ አፈሰሱ ፡
የሚቀብራቸውም ፡ የለም ፡፡
፬፡ ለጎረቤቶቻችን ፡ ነውር ፡ ሆነ ፡
በዙርያችንም ፡ ላሉ ፡ ለሳቅና ፡ ለሥላቅ ፡፡
፭፡ እስከ ፡ መቸ ፡ አቤቱ ፡ ትቈጣለኽ ፡፡ ለዘላለምን ፡፡
ቅንዓትኽስ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነደል ፡፡
፮፡ መዓትኽን ፡ በማያውቁኽ ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ አፍስስ ፡
ስምኽንም ፡ ባልጸሩ ፡ መንግሥታት ፡ ላይ ፡፡
፯፡ ያዕቆብን ፡ በልተውታልና ፡ ማደርያውንም ፡ አፍርሰዋልና ፡፡
፰፡ የቀደመውን ፡ ኃጢአታችንን ፡ አታስብልን ፡፡
እጅግ ፡ ተናውጸናልና ፡ መሀረትህ ፡ ቶሎ ፡ ትቀድመን ፡፡
፱፡ እርደነ ፡ የመድኃኒታችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ስለ ፡ ስምኽ ፡
ምስጋና ፡
አድነነ ፡ ኃጢአታችንንም ፡ ይቅር ፡ በል ፡ ስለ ፡ ስምኽ ፡፡
፲፡ ለምን ፡ አሕዛብ ፡ ሊበሉ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ አምላካቸው ፡፡
በአሕዛብ ፡ ይታወቅ ፡ በፊታችን ፡
የባሮችኽ ፡ የፈሰሰው ፡ የደማቸው ፡ በቀል ፡፡
፲፩፡ የታሠረት ፡ ልቅሶ ፡ ወደ ፡ ፊትኽ ፡ ይግባ ፡፡
እንደ ፡ ክንድኽ ፡ ታላቅነት ፡ ለሞት ፡ የተለዩትን ፡ አድን ፡፡
፲፪፡ ለጎረቤቶቻችንም ፡ የተላገዱኽን ፡ መላገዳቸውን ፡ አቤቱ ፡
ሰባት ፡ ዕፅፍ ፡ በብብታቸው ፡ ክፈልላቸው ፡፡
፲፫፡ እኛ ፡ ግን ፡ ሕዝብኽ ፡ የመሰማርያኽም ፡ በጎች ፡
ለዘላለም ፡ ልናመስግንኽ ፡፡
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ምስጋናኽን ፡ እንነግራለን ፡፡

## መዝሙር : ፹፡

፩፡ የእሥራኤል : ጠባቂ : አድምፅ ::
ዮሴፍን : እንደ : በግ : የምታደላድለው :
በኪሩቤል : ላይ : የምትቀመጥ : አብራ ::
፪፡ በኤፍሬም : በብንያምም : በምናሴመ : ፊት :
ኃይልኽን : አንሣ : እኛንም : ለማዳን : ና ::
፫፡ መልሰነ : አቤቱ : ፊትኽንም : አብራ : እንድንማለን ::
፬፡ አቤቱ : የሠራዊት : አምላክ : እስከ :መ ቼ : በወገኖች
ኽ : ጸሎት : ላይ : ትቈጣለኽ ::
፭፡ የንብን : እንጀራ : መገብኻቸው :
እንባቸውንም : በስፍር : አጠጣኻቸው ::
፮፡ ለጎረቤቶቻችን : ክርክር : አደረግኸነ ::
ጸላቶቻችነም : ተሣለቁብነ ::
፯፡ መልሰነ : አቤቱ : የሠራዊት : አምላክ ::
ፊትኽንም : አብራ : እንድንማለን ::
፰፡ ከምስር : የወይን : ጉንድ : አወጣኽ ::
አሕዛብንም : አውፅተኽ : ተክልኻት ::
፱፡ በፊትዋ : ስፍራውን : አበጀህ ::
ስርንም : አስያዝኻት : ምድርንም : መላች ::
፲፡ ጽላዋ : ተራሮችን : ከደነ ::
ጫፎችዋም : እንደ : እግዚአብሔር : ዛፎች : ሆኑ ::
፲፩፡ አረግዋን : እስከ : ባሕር : ዘረጋች :
እስከ : ታላቅ : ወንዙም : ብቋያዋን ::
፲፪፡ ለምን : አጥርዋን : አፈረስኽ ::
መንገድ : አላፊም : ሁሉ : ይቈርጣታል ::
፲፫፡ የዱር : እርያ : ይነክሳታል ::
የምድረ : በዳ : አርዊም : ይሰማራባታል ::
፲፬፡ እንጊዲህስ : ተመለስ : የሠራዊት : አምላክ ::
ከሰማይ : ተመለከት : እይም :
ይህችንም : የወይን : ጉንድ : ጉበኝ ::
፲፭፡ የወይንንም : አታክልት : ቀኝኽ : የተከለቻትን ::
ጫፍዋንም : ላንተ : ያጸናኸውን ::



፲፮፡ በእሳት : ተቃጥላለችና : ተቈርጣለችምና ::
ከፊትኽ : ዘለፋ : ይጠፋሉ ::
፲፯፡ እጅኽ : በቀኝኽ : ሰው : ላይ : ትሁን ::
በሰው : ልጅም : ላንተ : ባጸናኸው ::
፲፰፡ ካንተም : አንርቅም :: አድነነ : ስምኽንም : እንጸራለን ::
፲፱፡ መልሰነ : አቤቱ : የሠራዊት : አምላክ ::
ፊትኽን : አብራ : እንድንማለን ::

## መዝሙር : ፹፩፡

፩፡ ለእግዚአብሔር : ለጉልበታችን : እልል : በሉ ::
ለያዕቆብ : አምላክ : እልል : በሉ ::
፪፡ ዝማሬውን : ውሰዱ : ከበሮንም : አምጡ ::
ደስ : የሚያሰኘን : በገና : ከመሰንቆ : ጋራ ::
፫፡ በመባቻ : መለከት : ንፉ :: በታወቀ : በዓላችን : ቀን ::
፬፡ እርሱ : የእሥራኤል : ሥርዓት : ነውና ::
የያዕቆብም : አምላክ : ፍርድ ::
፭፡ በዮሴፍ : ለምስክር : ያቆመው : ከምስር : በወጣ : ጊዜ ::
የማላውቀውን : ቋንቋ : በሰማሁ : ጊዜ ::
፮፡ ከሸክም : ጫንቃውን : አራቅሁ ::
እጆቹንም : በሸክላ : ከመገዛት ::
፯፡ በመከራ : ጸራኸኝ : አደንሁኽም ::
በተሠወረ : በነጐድጓድ : ስፍራ : መለስሁልኽ ::
በክርክር : ውኃ : ፈተንሁኽ ::
፰፡ ስማ : ወገኔ : እመሰክርብኻለሁ ::
እሥራኤል : ሆይ : አንተ : ብትሰማኝ :
፱፡ ሌላ : አምላክ : አይሁንልኽ ::
ለባዕድ : አምላክም : አትስገድ ::
፲፡ እኔ : እግዚአብሔር : አምላክኽ : ነኝና :
ከምድረ : ግብጽ : ያወጣሁኽ ::
አፍኽን : አስፋ : እመላውማለሁ ::
፲፩፡ ሕዝቤ : ግን : ቃሌን : አልሰማኝም :
እሥራኤልም : እሺ : አላለኝም ::

፲፪፤ ተውኳቸውም ፡ እንደ ፡ ልባቸው ፡ ምቀኝነት ፡
በምክራቸውም ፡ ሔዱ ፡፡
፲፫፤ ወገኔስ ፡ ሰምቶኝ ፡ እንደ ፡ ሆን ፡
እሥራኤልም ፡ በመንገዴ ፡ ሒደ ፡ እንደ ፡ ሆን ፡
፲፬፤ ጸላቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ፈጥኜ ፡ ባዋረድሁላቸው ፡ ነበርሁ ፡
በሚያሳዝንዋቸውም ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ በጣልሁ ፡፡
፲፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ጸላቶች ፡ በተገዙለት ፡ ነበሩ ፡፡
ዘመናቸውም ፡ ለዘላለም ፡ በሆነ ፡፡
፲፮፤ የስንዴም ፡ ስብ ፡ ባበላው ፡ ነበር ፡፡
ካምባውም ፡ ማር ፡ ባጸገብሁኽ ፡፡

የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፹፪፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ባምላኮች ፡ ጉባዔ ፡ ይቆማል ፡፡
ባምላኮች ፡ ማኸል ፡ ይፈርደል ፡፡
፪፤ እስከ ፡ መቸ ፡ አሰት ፡ ትፈርደላችሁ ፡
ለኃጢአተኞችስ ፡ ፊት ፡ ታደላላችሁ ፡፡
፫፤ ለችጋረኛ ፡ አባትና ፡ እናትም ፡ ለሌለ ፡ ፍረዱ ፡፡
ምስኪኑንም ፡ ነደይንም ፡ አጽድቁ ፡፡
፬፤ ሰው ፡ የሌለውን ፡ ችጋረኛንም ፡ ርዱ ፡፡
ከኃጢአተኞች ፡ እጅ ፡ አስጥልዋቸው ፡፡
፭፤ አያውቁም ፡ አያስተውሉምም ፡፡ በጨለማ ፡ ይሔደሉ ፡
የምድር ፡ መሠረት ፡ ሁሉ ፡ ይናወጻል ፡፡
፮፤ እኔስ ፡ አማልክት ፡ ናችሁ ፡ አልሁ ፡
ሁላችሁም ፡ የልዑል ፡ ልጆች ፡፡
፯፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ትሞታላችሁ ፡፡
ካለቆችም ፡ እንደንዱ ፡ ትወድቃላችሁ ፡
፰፤ ተነሣ ፡ አቤቱ ፡ በምድር ፡ ፍረድ ፡፡
አንተ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ትወርሳለኽና ፡፡

መዝሙር ፡ ፹፫፤

፩፤ አቤቱ ፡ ዝም ፡ አትበል ፡፡
ዝም ፡ አትበል ፡ ቸል ፡ አትበልም ፡ አቤቱ ፡፡



፪፤ እነሆ ፡ ጸላቶችኽ ፡ ይጮኻሉና ፡፡
የሚጸሉኽም ፡ ራሳቸውን ፡ አነሡ ፡፡
፫፤ ሕዝብኽን ፡ በምክር ፡ ሸንግለዋልና ፡፡
በስውራንኽም ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ፡፡
፬፤ አሉም ፡ ኑ ፡ ከአሕዛብ ፡ እናጥፋቸው ፡፡
ደግሞም ፡ አይጸራ ፡ የእሥራኤል ፡ ስም ፡፡
፭፤ ተማክረውም ፡ ያንድ ፡ ልብ ፡ ሁነዋልና ፡፡
ባንተም ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡ ተገቡ ፡፡
፮፤ በኤደምያስ ፡ የሚኖሩ ፡ የእስማኤልም ፡ ወገን ፡፡
ሞአብም ፡ የአጋርም ፡ ወገኖች ፡፡
፯፤ ጌባልና ፡ ዓሞን ፡ ዓማሌቅም ፡፡
ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከጢሮስ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡፡
፰፤ አሶርም ፡ ከርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ሆነ ፡፡
ለሎጥ ፡ ልጆችም ፡ ረጅ ፡ ሆኑ ፡፡
፱፤ እንደ ፡ በምድያም ፡ እንደ ፡ በሢሣራም ፡ አድርግባቸው ፡፡
እንደ ፡ በያቢንም ፡ በቂሦን ፡ ወንዝ ፡
፲፤ በዓይን ፡ ደር ፡ በጠፉ ፡፡ እንደ ፡ ፈንዲያም ፡ የሆኑ ፡ በ
ምድር ፡ ላይ ፡፡
፲፩፤ አለቆቻቸውን ፡ እንደ ፡ ሖሬብ ፡ እንደ ፡ ዜብም ፡ አድርግ ፡፡
ታላላቆቻቸውንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ዛባ ፡ እንደ ፡ ሰልማ
ናም ፡፡
፲፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ማደርያ ፡ እንወርሳለን ፡ ያሉ ፡፡
፲፫፤ አምላኬ ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡ አድርጋቸው ፡፡
በንፋስ ፡ ፊትም ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡፡
፲፬፤ እሳት ፡ በድን ፡ እንደምትቃጠል ፡፡
ተራሮችንም ፡ እንደሚያቃጥል ፡ ነበልባል ፡፡
፲፭፤ እንዲሁም ፡ በቍጣኽ ፡ አሳደቸው ፡፡
በኵርፊትኽም ፡ አስደንግጣቸው ፡፡
፲፮፤ ፊታቸውንም ፡ እፍረት ፡ ምለው ፡፡
ስምህንም ፡ ይፈልጋሉ ፡ አቤቱ ፡፡
፲፯፤ ይፈሩ ፡ ለዘላለሙም ፡ ይታወኩ ፡፡
ያፍራሉም ፡ ይጠፋሉም ፡፡

፲፰፤ ስምኽም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቃሉ ፡፡
አንተም፡ብቻኽ፡ልዑል፡እንደ፡ሆንኽ፡በምድር፡ሁሉ፡ላይ፡፡

## መዝሙር ፡ ፹፬፤

፩፤ እንደ፡ምን፡ተወደደ፡ማደርያችኽ፡አቤቱ፡የሠራዊት፡ጌታ፡፡
፪፤ ነፍሴ፡የእግዚአብሔርን፡ስፍራ፡በመወደድ፡ትናፍቃለች፡፡
ልቤ ፡ ሥጋዬም ፡ በሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡፡
፫፤ ዎፍ ፡ ደግሞ ፡ ቤትን ፡ አገኘ ፡
ዋልያም ፡ ለራስዋ ፡ መኖርያውን ፡ አገኘች ፡ ጫጩቶችዋን ፡
ልታኖርባት ፡፡
እርሱም ፡ መሠውያኽ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ንጉ
ሢ ፡ አምላኬም ፡፡
፬፤ በቤትኽ ፡ የሚኖሩ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ፡፡
ሁልግዜ ፡ ያመሰግኑኻል ፡፡
፭፤ ኀይሉ ፡ ባንተ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡፡
መንገድኽ ፡ በልባቸው ፡ ያለ ፡፡
፮፤ በልቅሶ ፡ ወንዝ ፡ ሲያልፉ ፡ ለምንጭ ፡ ያደርጉታል ፡
ዝናምም ፡ በረከትን ፡ ይሰጣቸዋል ፡፡
፯፤ ከኀይል ፡ ወደ ፡ ኀይል ፡ ይሔዳሉ ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ በፅዮን ፡ ይታያሉ ፡፡
፰፤ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ፡
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አድምጽ ፡፡
፱፤ ተመልከት ፡ አቤቱ ፡ ጋሻችን ፡ ሆይ ፡
ቀብተኽ ፡ ወደነገሠኸውም ፡ ፊት ፡ እይ ፡፡
፲፤ አንዲት ፡ ቀን ፡ በቦታኽ ፡ ከሌሎች ፡ ሺሕ ፡ ትሻላለችና ፡፡
በአምላኬ ፡ ቤት ፡ ደጅን ፡ መጠበቅ ፡ መረጥሁ ፡
በኃጥአን ፡ ቤት ፡ ከመቀመጥ ፡፡
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ጸሐይና ፡ ጋሻ ፡ ነውና ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ሞገስና ፡ ክብር ፡ ይሰጣል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ በቅንነት ፡ የሚሔዱትን ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ አያ
ሳጣቸውም ፡፡
፲፪፤ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ባንተ ፡ የታመነ ፡ ሰ
ው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡፡



## መዝሙር ፡ ፹፭፤

፩፤ ለምድርኽ ፡ አቤቱ ፡ ሞገስ ፡ አደረግኽ ፡
የያዕቆብንም ፡ ምርኮ ፡ መለስኽ ፡፡
፪፤ የሕዝብኽን ፡ ኀጢአት ፡ አስቀርኽ ፡
ኀጢአታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ከደንኽ ፡፡
፫፤ መዓትኽን ፡ ሁሉ ፡ አስወገድኽ ፡
ከቍጣኽ ፡ እሳት ፡ ተመለስኽ ፡፡
፬፤ መልሰነ ፡ የመድኀኒታችን ፡ አምላክ ፡
መዓትኽንም ፡ ከኛ ፡ መልስ ፡፡
፭፤ በውኑ ፡ ለዘላለምን ፡ ትቈጣናለኽ ፡፡
ቍጣኽን ፡ ለልጅ ፡ ልጅን ፡ ታስረዝማለኽ ፡፡
፮፤ አንተ ፡ ተመልሰኽ ፡ አታድነነምን ፡፡
ሕዝብኽም ፡ ባንተ ፡ ደስ ፡ ሊበላቸው ፡፡
፯፤ ምህረትኽን ፡ አስየነ ፡ አቤቱ ፡፡
መድኀኒትኽንም ፡ ስጠነ ፡፡
፰፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ የሚናገረውን ፡ እሰማለሁ ፡፡
ሰላም ፡ ለሕዝቡ ፡ ይናገራልና ፡ ለቅዱሳኑም ፡፡
ወደ ፡ ስንፍናም ፡ አይመለሱ ፡፡
፱፤ በውነት ፡ ማዳኑ ፡ ለሚፈሩት ፡ ቅርብ ፡ ናት ፡፡
ክብር ፡ በምድራችን ፡ ያድር ፡ ዘንድ ፡፡
፲፤ ምህረትና ፡ እውነት ፡ ተገናኙ ፡፡
ጽድቅና ፡ ሰላምም ፡ ተሳሳሙ ፡፡
፲፩፤ እውነት ፡ ከምድር ፡ ትበቅላለች ፡፡
ጽድቅም ፡ ከሰማይ ፡ ትመለከታለች ፡፡
፲፪፤ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ይሰጣል ፡፡
ምድራችንም ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ፡፡
፲፫፤ ጽድቅ ፡ በፊቱ ፡ ትሔዳለች ፡፡
አረጋገጡንም ፡ በመንገድ ፡ ታኖራለች ፡፡

## አሥራ ፡ ሰባተኛ ፡ ቀን ።

---

### የጽዋት ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፹፭፡

፩፡ አቤቱ ፡ ጆሮኽን ፡ ወደኔ ፡ ጣል ፡ መልስልኝም ።
እኔ ፡ ችጋረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝና ።
፪፡ ነፍሴን ፡ ጠብቅ ፡ ቅዱስ ፡ ነኝና ።
አምላኬ ፡ አንተን ፡ የታመነውን ፡ ባርያኽን ፡ አድን ።
፫፡ ማረኝ ፡ አቤቱ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉን ፡ ወደንተ ፡ እጮኻለሁና ።
፬፡ የባርያኽን ፡ ነፍስ ፡ ደሳሰኛት ፡
ነፍሴን ፡ ወደንተ ፡ እዋላለሁና ።
፭፡ አንተ ፡ አቤቱ ፡ ቸር ፡ ይቅር ፡ ባይም ፡ ነኽና ።
ምሕረትኽም ፡ ወደንተ ፡ ለሚጸሩ ፡ ሁሉ ፡ በዝታለችና ።
፮፡ ጸሎቴን ፡ አድምፅ ፡ አቤቱ ። የልመናዬንም ፡ ነገር ፡ ስማ ።
፯፡ በመከራዬ፡ቀን፡ወደንተ፡እጮኻለሁ፡ትመልስለኛለኽና።
፰፡ በአማልክት ፡ የሚመስልኽ ፡ የለም ፡ አቤቱ ፡
እንደ ፡ ስራኽም ፡ ስራ ፡ የለም ።
፱፡ የፈጠርኻቸው ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይመጻሉ ፡
በፊትኽም ፡ አቤቱ ፡ ይሰግዳሉ ።
ስምኽንም ፡ ያከብራሉ ።
፲፡ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነኽና ፡ ድንቅም ፡ ታደርጋለኽና ።
አንተ ፡ ብቻኽን ፡ አምላክ ፡ ነህና ።
፲፩፡ አቤቱ ፡ መንገድኽን ፡ አስተምረኝ ።
በእውነትኽ ፡ ልሔድ ።
ልቤን ፡ ሁሉ ፡ ምራ ፡ ስምኽን ፡ ለመፍራት ፡ ግጠመው ።
፲፪፡ አመሰግንኻለሁ ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ።
ለዘላለሙም ፡ ስምኽን ፡ አከብራለሁ ።
፲፫፡ ምሕረትኽ ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ናትና ።
ነፍሴንም ፡ ከታቺኛ ፡ ሢኦል ፡ አድንኻልና ።
፲፬፡ ዐቡያን ፡ በላዬ ፡ ቆሙ ፡ አቤቱ ።
የብርቱቾችም ፡ ጉባዔ ፡ ነፍሴን ፡ አሸዋት ።



በፊታቸውም ፡ አላደረጉኽም ።
፲፭፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ መሓሪና ፡ ርሩ ፡ አምላክ ፡ ነኽ ።
መዓትኽ ፡ የራቀ ፡ ምሕረትኽም ፡ እውነትኽም ፡ የበዛ ።
፲፮፡ ወደኔ ፡ ተመልከት ፡ እዘንልኝም ።
ኃይልኽን ፡ ለባርያኽ ፡ ስጥ ፡ የሴት ፡ ባርያኽንም ፡ ልጅ ፡
አድን ።
፲፯፡ ምልክትንም ፡ ለደህንነት ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ አድርግ ።
የሚጸሉኝ ፡ አይተው ፡ ያፍሩ ፡ ዘንድ ።
አንተ ፡ አቤቱ ፡ ረድተኸኛልና ፡ አጽናንተኸኝማልና ።

### መዝሙር ፡ ፹፮፡

፩፡ መሠረቶቹ ፡ በተቀደሱ ፡ ተራሮች ፡ ሆኑ ።
፪፡ እግዚአብሔር ፡ የፅዮንን ፡ ደጆች ፡ ወደደ ፡
ከያዕቆብ ፡ መኖርዮች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ።
፫፡ ባንቺ ፡ የከበረ ፡ ነገር ፡ ይባላል ፡
የእግዚአብሔር ፡ አገር ፡ ሆይ ።
፬፡ ረሐብን ፡ ባቢሎንንም ፡ ለሚያውቁኝ ፡ አሳስባለሁ ።
እነሆ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ጢሮስም ፡ የኢትዮጲያም ፡
ወገን ።
ይኽም ፡ ከዚያ ፡ ተወለደ ።
፭፡ ለፅዮንም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሰዎች ፡ ተወለዱባት ፡ ይላሉ ።
እርሱም ፡ ልዑል ፡ ያጸናታል ።
፮፡ እግዚአብሔርም ፡ አሕዛብን ፡ በጽፈት ፡ ቈጥሮ ፡
ያም ፡ ከዚያ ፡ ይወለዳል ፡ ይላል ።
፯፡ መዘምራንና ፡ ዘፈነኞችም ፡ ባንቺ ፡ ይኖራሉ ።
ምንጮቼም ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ ናቸው ።

### መዝሙር ፡ ፹፯፡

፩፡ አቤቱ ፡ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡
በቀንና ፡ በሌት ፡ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ።
፪፡ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትኽ ፡ ትግባ ።
ጆሮኽን ፡ ወደ ፡ ጩኸቴ ፡ ጣል ።

፫፡ ነፍሴ ፡ መከራ ፡ ጸግባለችና ።
ሕይወቴም ፡ ወደ ፡ ሢኦል ፡ ደረሰች ።
፬፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋራ ፡ ተቈጠርሁ ።
ኃይልም ፡ እንደሌለው ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
፭፡ በሞቱት ፡ መኻከል ፡ ሐርነት ፡ የወፀሁ ፡ ነኝ ፡
በሰይፍ ፡ ሙተው ፡ በመቃብር ፡ እንደ ፡ ተኙ ።
ደግሞ ፡ የማታስባቸው ፡ እርሳቸው ፡ ከጅኽ ፡ ተቈረጡ ።
፮፡ በታችኛ ፡ ጕድጓድ ፡ አስቀመጥኸኝ ፡
በጨለማም ፡ በጥልቆችም ።
፯፡ በኔ ፡ ቍጣኽ ፡ ጸና ። ሞገድኽንም ፡ ሁሉ ፡ በላዬ ፡ አመጻኽ ።
፰፡ የሚያውቁኝን ፡ ከኔ ፡ አራቅኽ ።
ለርሳቸው ፡ ርኩስ ፡ አደረግኸኝ ።
እንደልወጣም ፡ ተከለከልሁ ።
፱፡ ዓይኖቼ ፡ ከመከራ ፡ ፈዘዙ ።
ምሉውን ፡ ቀን ፡ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ፡ አቤቱ ።
እጄንም ፡ ወደንተ ፡ ዘረጋሁ ።
፲፡ በውኑ ፡ ለሙታንን ፡ ታምራት ፡ ታደርጋለኽ ።
የሞቱትስ ፡ ሊያመሰግኑኽ ፡ ይነሣሉን ።
፲፩፡ በመቃብርስ ፡ ያሉ ፡ ቸርነትኽንን ፡ ይነግራሉ ።
እውነትኽንም ፡ በጥፋት ፡ ስፍራ ።
፲፪፡ በጨለማስ ፡ ታምራትኽን ፡ ትታወቃለች ።
ጽድቅኽምን ፡ በመርሳት ፡ ምድር ።
፲፫፡ እኔ ፡ ግን ፡ ወደንተ ፡ አቤቱ ፡ ጮኽሁ ።
በጽዋትም ፡ ጸሎቴ ፡ ትቀድምኻለች ።
፲፬፡ ለምን ፡ አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ ትጥላለኽ ።
ፊትኽንም ፡ ከኔ ፡ ትሰውራለኽ ።
፲፭፡ እኔ ፡ ከታናሽነቴ ፡ ጀምሬ ፡ ችጋረኛ ፡ ነኝ ፡ ለሞትም ፡ የቀ
ረብሁ ።
ድንጋጼህን ፡ ተሸክሜ ፡ አልቃለሁ ፡
፲፮፡ የቍጣህ ፡ እሳት ፡ አለፈችብኝ ።
ግርማኽም ፡ አስደነገፀችኝ ።
፲፯፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ከበበችኝ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ።



በዙርያዬ ፡ ባንድ ፡ ተሰበሰበች ።
፲፰፡ ወዳጆቼን ፡ ባልንጀሮቼንም ፡ ከኔ ፡ አራቅኽ ።
ዘመዶቼንም ፡ በጨለማ ፡ ሰወርኽ ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፹፰፡

፩፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሕረት ፡ ለዘላለም ፡ እቀኛለሁ ።
ባፌም ፡ እውነትኽን ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ አመሰግናለሁ ።
፪፡ ምሕረት ፡ ለዘላለም ፡ ትሠራለች ፡ ብያለሁና ።
እውነትኽንም ፡ በሰማይ ፡ ታጸናታለኽ ።
፫፡ ከመረጽሁት ፡ ጋራ ፡ ኪዳን ፡ አደረግሁ ፡
ለባርያዬም ፡ ለዳዊት ፡ ማልሁ ።
፬፡ ዘርኽን ፡ ለዘላለም ፡ እንደዘጋጅልኽ ፡
ዙፋንኽንም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሠራሁ ።
፭፡ ሰማዮችም ፡ ታምራትኽን ፡ ያመሰግናሉ ፡ አቤቱ ።
ደግሞም ፡ እውነትኽን ፡ በቅዱሳን ፡ ጉባዔ ።
፮፡ ማነው ፡ በሰማይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚተካከለው ።
ከአማልክት ፡ ልጆችም ፡ ማን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይመ
ስላል ።
፯፡ የተፈራ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ በቅዱሳን ፡ ሸንጎ ።
ታላቅ ፡ ነው ፡ ግሩምም ፡ ነው ፡ በዙርያው ፡ ባሉ ፡ ሁሉ ።
፰፡ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ማነው ፡ እንደንተ ፡ የበረታ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡
እውነትኽም ፡ ትከብኻለች ።
፱፡ የባሕርን ፡ ትዕቢት ፡ አንተ ፡ ትገዛለኽ ።
የሞገዱን ፡ መናወጥ ፡ አንተ ፡ ዝም ፡ ታሰኘዋለኽ ።
፲፡ አንተ ፡ ረሐብን ፡ ቀጠቀጥኽ ፡ እንደ ፡ ተወጋ ።
በኃይልኽም ፡ ክንድ ፡ ጸላቶችኽን ፡ በተንኽ ።
፲፩፡ ሰማዮች ፡ ያንተ ፡ ናቸው ፡ ምድርም ፡ ያንተ ፡ ናት ።
ዓለምን ፡ መላትዋንም ፡ አንተ ፡ መሠረትኽ ።
፲፪፡ ሰሜንን ፡ ደቡብንም ፡ አንተ ፡ ፈጠርኽ ።
ታቦርና ፡ አርሞንዔም ፡ በስምኽ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

፲፫፡ ላንተ ፡ ክንድ ፡ አለኽ ፡ ከኀይል ፡ ጋራ ።
እጅኽ ፡ ትበርታለች ፡ ቀኝኽም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላለች ።
፲፬፡ የመንበርኽ ፡ ደገፉ ፡ ጽድቅና ፡ ፍርድ ፡ ነው ፡
ምሕረትና ፡ እውነት ፡ በፊትኽ ፡ ይሔዳሉ ።
፲፭፡ እልልታ ፡ የሚያውቅ ፡ ወገን ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡
አቤቱ ፡ በፊትኽ ፡ ብርሃን ፡ ይሔዳሉ ።
፲፮፡ በስምኽ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡
በጽድቅኽም ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ።
፲፯፡ የኀይላቸው ፡ ትምክሕት ፡ አንተ ፡ ነኽና ፡
በጸጋኽም ፡ ቀንደችን ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፲፰፡ ጋሻችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነውና ፡
ንጉሣችንም ፡ በእሥራኤል ፡ ለተቀደሰ ።
፲፱፡ በዚያን ፡ ቀን ፡ ለቅዱስኽ ፡ በራእይ ፡ ተናገርኽ ።
ረዳትም ፡ በኀያል ፡ ላይ ፡ አኖርሁ ፡ አልኽ ፡
ከሕዝብ ፡ የተመረጠውን ፡ አነሣሁ ።
፳፡ ባሪያዬን ፡ ዳዊትን ፡ አገኘሁ ፡
በቅድስናዬ ፡ ዘይትም ፡ ቀባሁት ።
፳፩፡ እጄም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ትጸናለች ፡
ክንዴም ፡ ታጸናዋለች ።
፳፪፡ ጸላት ፡ በርሱ ፡ አይረባም ፡
የዐመፃም ፡ ልጅ ፡ ሊጎዳው ፡ አይችልም ።
፳፫፡ ጸላቶቹን ፡ ከፊቱ ፡ እቀጠቅጣለሁ ፡
የሚጸሉትንም ፡ እመታቸዋለሁ ።
፳፬፡ እውነቴ ፡ ግን ፡ ጸጋዬም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡
በስሜም ፡ ቀንዱ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፳፭፡ እጁንም ፡ በባሕር ፡ አኖራለሁ ፡ በፈሳሾችም ፡ ቀኙን ።
፳፮፡ እርሱ ፡ ይለኛል ፡ አንተ ፡ አባቴ ፡ ነኽ ፡ ብሎ ፡
አምላኬም ፡ የመድኀኒቴም ፡ አምባ ።
፳፯፡ እኔም ፡ የበኵር ፡ ልጄን ፡ አደርገዋለሁ ፡
ከምድር ፡ ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አኖረዋለሁ ።
፳፰፡ ለዘላለም ፡ ምሕረቴን ፡ ለርሱ ፡ እጠብቃለሁ ፡
ኪዳኔም ፡ ለርሱ ፡ የታመነ ፡ ነው ።



፳፱፡ ዘርዑንም ፡ ለዘላለም ፡ አደርጋለሁ ፡
ዙፋኑንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ዘመን ።
፴፡ ልጆቹስ ፡ ሕጌን ፡ ቢተው ፡ በፍርዴም ፡ ባይሔዱ ፡
፴፩፡ ሥርዓቴን ፡ ቢያረክሱ ፡ ትእዛዛቴንም ፡ ባይጠብቁ ፡
፴፪፡ ኀጢአታቸውን ፡ በጨንገር ፡ እጐበኛለሁ ፡
ግፋቸውንም ፡ በግርፋት ።
፴፫፡ ምሕረቴን ፡ ግን ፡ ከርሱ ፡ አላርቃትም ፡
በእውነቴም ፡ አልወነጅልም ።
፴፬፡ መሐላዬን ፡ አላረክስም ፡
ከከንፈሬም ፡ የወጣውን ፡ አልለውጥም ።
፴፭፡ አንደግዜ ፡ በቅዱስነቴ ፡ማልሁ ፡
በዳዊትም ፡ አሰተኛ ፡ አልሆንበትም ።
፴፮፡ ዘሩ ፡ ለዘላለሙ ፡ ይኖራል ፡
ዙፋኑም ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ በፊቴ ።
፴፯፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ጨረቃ ፡ ይጸናል ፡
እንደ ፡ ታመነም ፡ ምስክር ፡ በደመናት ።
፴፰፡ አንተ ፡ ግን ፡ ናቅኸው ፡ ጸላኸውም ፡
ቀብተኽ ፡ ያነገሥኸውንም ፡ ተቈጣኽ ።
፴፱፡ የባሪያኽን ፡ ኪዳን ፡ አፈረስኽ ፡
አክሊሉንም ፡ በምድር ፡ አረከስኽ ።
፵፡ ቅጥሩን ፡ ሁሉን ፡ ፈታህ ፡ አምባውንም ፡ ሁሉ ፡ አፈረስኽ ።
፵፩፡ መንገድ ፡ አላፊ ፡ ሁሉ ፡ ተናጠቀው ።
ለጎረቤቶቹም ፡ ስድብ ፡ ሆነ ።
፵፪፡ የጸላቶቹን ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ አደረግኽ ፡
የሚጸሉትንም ፡ ሁሉ ፡ ደሳሰኘኽ ።
፵፫፡ የሰይፉንም ፡ ስለት ፡ መለስኽ ፡
በሰልፍም ፡ አላቆምኸውም ።
፵፬፡ ከንጽሕናውም ፡ ሻርኸው ። ዙፋኑንም ፡ በምድር ፡ ጣልኽ ።
፵፭፡ የጕልማስነቱን ፡ ዘመን ፡ አሳነስኽ ፡
ኀፍረትንም ፡ አለበስኸው ።
፵፮፡ እስከ ፡ መቼ ፡ አቤቱ ፡ ከኛ ፡ ትመለሳለኽ ፡ ለዘላለምን ።
መዓትኽ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነዷልን ።

፵፯፡ ዘመኔ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ አስብ ።
የሰውን ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ለከንቱ ፡ ፈጠርኸ ።
፵፰፡ ማነው ፡ ሕያው ፡ ሁኖ ፡ የሚኖር ፡ ሰው ፡ ሞትንስ ፡ የማያይ ።
ነፍሱንስ ፡ ከሢኦል ፡ እጅ ፡ የሚያድን ።
፵፱፡ የቀደመች ፡ ምሕረትኸ ፡ ወዴት ፡ ናት ፡ አቤቱ ፡
ለዳዊት ፡ ለባርያኸ ፡ በ ውነትኸ ፡ የማልኸት ።
፶፡ አስብ ፡ አቤቱ ፡ የባሮችኸን ፡ ስድብ ፡
በብብቴ ፡ የተቀበልሁትን ፡ ከብርቱ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ።
፶፩፡ ጸላቶችኸ ፡ የሰደቡበትን ፡ አቤቱ ፡
ቀብተኸ ፡ ያነገሥኸውን ፡ መንገድ ፡ የሰደቡበትን ።
፶፪፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ። አሜን ። አሜን ።

---

አሥራ ፡ ስምንተኛ ፡ ቀን ።

የ ጽዋ ት ፡ ጸሎ ት ።

መዝሙር ፡ ፺፡

፩፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡ መኖርያ ፡ ሆንኸልነ ፡ በትውልድ ፡ ሁሉ ።
፪፡ ተራሮች ፡ ሳይወለዱ ፡ ምድርም ፡ ዓለምም ፡ ሳይፈጠር ።
ከዘላለምም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ አንተ ፡ አምላክ ፡ ነኸ ።
፫፡ ሰውን ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ትመልሳለኸ ፡
ተመለሱም ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ትላለኸ ።
፬፡ ሺኸ ፡ አመት ፡ በፊትኸ ፡ እንደለፈች ፡ እንደ ፡ ትላንት ፡ ቀን ፡
እንደ ፡ ሌትም ፡ ትጋት ፡ ናቸውና ።
፭፡ አጠፋኻቸው ፡ እንደ ፡ እንቅልፍም ፡ ናቸው ።
ማልደ ፡ እንደ ፡ ለመለመ ፡ እንደሚያልፍም ፡ እሳር ።
፮፡ ማልደ ፡ ያብባል ፡ ያልፋልም ፡
በሰርክም ፡ ይቆረጣልና ፡ ይደርቃል ።
፯፡ በቍጣኸ ፡ አልቀናልና ። በመዓትኸም ፡ ደነፀነ ።
፰፡ ኃጢአታችነነ ፡ በፊትኸ ፡ አስቀመጥኸ ፡
የተሰወረውንም ፡ ኃጢአታችን ፡ በፊትኸ ፡ ብርሃን ።
፱፡ ዘመናችን ፡ ሁሉ ፡ በመዓትኸ ፡ አልፋዋልና ፡
አመታታችነንም ፡ እንደ ፡ ጨወታ ፡ ፈጸምነ ።



፲፡ ያመታታችን ፡ ዘመን ፡ ሰብዓ ፡ አመት ፡ ነው ፡
በብርታትም ፡ ቢሆን ፡ ሰማንያ ፡ አመት ።
ኃይላቸው ፡ ግን ፡ ድካምና ፡ መከራ ፡ ነው ።
ቶሎ ፡ አልፋዋልና ፡ እኛም ፡ በረን ፡ እንሔዳለን ።
፲፩፡ ማነው ፡ የቍጣኸን ፡ ጽናት ፡ የሚያውቅ ።
እንደ ፡ ፍርሃትኸም ፡ እንደሁም ፡ ቍጣኸ ፡ እንደለ ።
፲፪፡ ዘመናችነን ፡ እንቈጥር ፡ ዘንድ ፡ አስታውቀነ ፡
ልባችን ፡ ወደ ፡ ጥበብ ፡ እንድናገባ ።
፲፫፡ ተመለስ ፡ አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቸ ። ለባሮችኸም ፡ እዘን ።
፲፬፡ ማልደ ፡ ምሕረኸን ፡ አጽግበነ ፡
ደስም ፡ ይለናል ፡ ሐሤትም ፡ እናደርጋለን ፡ በዘመናችን ፡ ሁሉ ።
፲፭፡ ደስ ፡ አሰኘነ ፡ መከራ ፡ በተቀበልነባት ፡ ቀን ፡ ፈንታ ።
ክፉም ፡ ባየነባቸው ፡ አመታት ፡ ፈንታ ።
፲፮፡ ባሮችኸ ፡ ስራኸን ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡
ልጆቻቸውም ፡ ምስጋናኸን ።
፲፯፡ የአምላካችንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሞገስ ፡ በላያችን ፡ ትሁን ፡
የጆቻችነንም ፡ ስራ ፡ በላያችን ፡ አቅና ።
የጆቻችነን ፡ ስራ ፡ አቅና ።

መዝሙር ፡ ፺፩፡

፩፡ በልዑል ፡ መጸጊ ፡ የሚኖር ፡
ሁሉን ፡ በሚችል ፡ በጽላው ፡ ያድራል ።
፪፡ እግዚአብሔርን ፡ መጸጊዬ ፡ አምባዬም ፡ አንተ ፡ ነኸ ፡
እለዋለሁ ፡
አምላኬም ፡ በርሱ ፡ አምናለሁ ።
፫፡ እርሱ ፡ ካደኚ ፡ ወጽመድ ፡ ያድንኻልና ፡
ከሚያጠፋም ፡ ቸነፈር ።
፬፡ በላባቹ ፡ ይሰውርኻል ፡ ከክንፎቹም ፡ በታች ፡ ትታመናለኸ ፡
እውነቱም ፡ ለጋሻና ፡ ለግምብ ፡ ትሆንልኻለች ፡
፭፡ ከሌሊት ፡ ግርማ ፡ አትፈራም ፡
ከፍላፃም ፡ በቀን ፡ ከሚበር ፡
፮፡ በጨለማም ፡ ከሚሔድ ፡ ቸነፈር ፡
በቀትርም ፡ ከሚያጠፋ ፡ በሽታ ።

፯፤ ባጠገብኽ ፡ ሺሕ ፡ ይወድቃሉ ፡ በቀኝኽም ፡ እልፍ ፡
ወደንተ ፡ ግን ፡ አይደርስም ።
፰፤ በዓይንኽ ፡ ትመለከታለኽ ፡ እንጂ ፡
የኃጥኣንንም ፡ ብድራት ፡ ታያለኽ ።
፱፤ አንተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መታመኛዬ ፡ ነህ ፡ ብለሃልና ፡
ልዑልንም ፡ ለመኖርያኽ ፡ አደረግኽ ።
፲፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ አይወድቅብህም ፡
መቅሠፍትም ፡ ወደ ፡ ቤትኽ ፡ አይቀርብም ።
፲፩፤ መላእክቱን ፡ ስላንተ ፡ ያዛልና ፡
በመንገድኽ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁኽ ፡ ዘንድ ።
፲፪፤ በእጃቸውም ፡ ላይ ፡ ያነሡኻል ፡
እግርኽ ፡ በደንጊያ ፡ እንዳትሰናከል ፡
፲፫፤ ባንበሳ ፡ በባብ ፡ ላይ ፡ ትጫማለኽ ፡
የንበሳንም ፡ ግልገል ፡ ዘንደንም ፡ ትረግጣለኽ ።
፲፬፤ በኔ ፡ ታምንዋልና ፡ አስጥለዋለሁ ፡
አሰውረዋለሁ ፡ ስሜን ፡ አውቋልና ።
፲፭፤ ወደኔም ፡ ይጮኻልና ፡ እመልስለታለሁ ፡
በመከራው ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነኝ ።
አድነውማለሁ ፡ አከብረውማለሁ ።
፲፮፤ ረጅምንም ፡ ዘመን ፡ አጸግበዋለሁ ።
ማዳኔንም ፡ አሳየዋለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፺፪፤

፩፤ እግዚአብሔርን ፡ ማመስገን ፡ መልካም ፡ ነው ፡
ለስምኽም ፡ ዝማሬ ፡ ማቅረብ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ።
፪፤ ማለደ ፡ በምሕረትኽ ፡ ማውራት ፡ በሌትም ፡ በቸርነትኽ ።
፫፤ አሥር ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ በገና ፡ በንብልታም ፡
ከምስጋና ፡ ጋራ ፡ በመሰንቆ ።
፬፤ በስራኽ ፡ ደስ ፡ አሰኘተኸኛልና ፡ አቤቱ ፡
በእጅኽም ፡ ስራ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፭፤ ስራኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ አቤቱ ።
አሳብኽም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ነው ።



፮፤ ደንቆር፡ሰው፡አያውቅም።ሰነፍም፡ይህን፡አያስተውልም ።
፯፤ ዐመፀኞች ፡ ሲጨበጨቡ ፡ እንደ ፡ ሣዕር ፡ ያብባሉ ፡
ደሮ፡ግፍን፡የሚያደርጉትን፡ሁሉ፡ላዘላለም፡ያጠፋቸዋል።
፰፤ አንተ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ት
ላለህ ።
፱፤ እነሆ ፡ ጸላቶችኽ ፡ አቤቱ ፡ እነሆ ፡ ጸላቶችኽ ፡ ይጠፋሉና፡
ግፍ ፡ የሚሰሩም ፡ ሁሉ ፡ ይበተናሉና ።
፲፤ ቀንዴ ፡ አንድ ፡ እንደ ፡ ሆነም ፡ ቀንዴ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
ራሴ ፡ በለመለመ ፡ ቅቤ ፡ ይቀባል ።
፲፩፤ ዓይኔም ፡ በጸላቶቼ ፡ በሚጠብቁኝ ፡ ታያለች ፡
በላዬም ፡ በክፉ ፡ በቆሙ ፡ ጆሮዬ ፡ ትሰማለች ።
፲፪፤ ጻድቅ ፡ እንደ ፡ ሰሌን ፡ ይለመልማል ፡
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዛፍም ፡ ያድጋል ።
፲፫፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የተተከሉ ፡ ባምላካችን ፡ ስፍራ ፡
ይለመልማሉ ።
፲፬፤ ደግሞም ፡ በሽምግልና ፡ ፍሬን ፡ ያፈራሉ ፡
ሰብተውና ፡ ለምልመው ፡ ይሆናሉ ።
፲፭፤ ይነግሩ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምባዬ ፡ እውነተኛ ፡ እ
ንደ ፡ ሆነ ፡
አድልዎም ፡ በርሱ ፡ የለበትም ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፺፫፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፡ ክብርንም ፡ ለበሰ ።
እግዚአብሔር ፡ ኃይልን ፡ ለበሰ ፡ ታጠቀባትም ።
ዓለምንም ፡ አጽንትዋታልና ፡ አትናወጽም ።
፪፤ ዙፋንኽ ፡ ከጥንት ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ።
አንተም ፡ ከዘላለም ፡ ነኽ ።
፫፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ፡ ፈሳሾች ፡ አቤቱ ፡
ፈሳሾች ፡ ቃላቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ።
ፈሳሾች ፡ ጩኸታቸውን ፡ ያነሣሉ ።

፬፡ ከብዙ ፡ ከውኃ ፡ ድምፅ ፡ ከባሕር ፡ ከኀረመ ፡ ሞገዱ ፡ ይልቅ ፡
እግዚአብሔር ፡ በላይ ፡ ግሩም ፡ ነው ።
፭፡ ምስክርኽ ፡ እጅግ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
ለቤትኽ ፡ ቅድስና ፡ ይገባል ፡ አቤቱ ፡
እስከ ፡ ረዥም ፡ ዘመን ፡ ድረስ ።

መዝሙር ፡ ፺፬ ።

፩፡ የበቀል ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡
የበቀል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ተገለጽ ።
፪፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ የምድር ፡ ፈራጅ ፡ ሆይ ፡
ዕቡያንም ፡ ፍዳቸውን ፡ መልስላቸው ።
፫፡ ኃጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ አቤቱ ፡
ኃጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይጓደዷሉ ።
፬፡ ትዕቢትን ፡ ያወጣሉና ፡ ይነግራሉ ፡
ግፍ ፡ አድራጎችም ፡ ሁሉ ፡ ይባላሉ ።
፭፡ ሕዝብኽን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ይሰባብራሉ ፡
ርስትህንም ፡ ያስቸግራሉ ።
፮፡ ባልቴቲቱን ፡ ስደተኛውንም ፡ ይገድላሉ ፡
አባት ፡ እናትም ፡ የሌለውን ፡ ይቀጠቅጣሉ ።
፯፡ እግዚአብሔርም ፡ አያይም ፡
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ አያስተውልም ፡ ይላሉ ።
፰፡ አስተውሉ ፡ እላንት ፡ የሕዝብ ፡ ድናቍርት ፡ ሆይ ።
እላንትም ፡ ሰነፎች ፡ መቼ ፡ በጅ ፡ ትላላችሁ ።
፱፡ ጆሮን ፡ የተከለ ፡ አይሰማምን ፡
ዓይንንም ፡ የፈጠረ ፡ አያይምን ።
፲፡ አሕዛብንስ ፡ የሚቀጣ ፡ አይዘልፍምን ፡
ለሰውም ፡ ዕውቀት ፡ የሚያስተምር ።
፲፩፡ እግዚአብሔር፡የሰውን፡አሳብ፡ያውቃል፡ምናምን፡እንደ፡ሆነ።
፲፪፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡ የገሠፅኸው ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡
ሕግኽንም ፡ ያስተማርኸው ።
፲፫፡ ከክፉ ፡ ዘመን ፡ ታሳርፈው ፡ ዘንድ ፡
ለኃጢአተኛ ፡ ጕድጓድ ፡ እስኪቈፈር ፡ ድረስ ።



፲፬፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አይጥልምና ፡
ርስቱንም ፡ አይተውምና ።
፲፭፡ ፍርድ ፡ ወደ ፡ ጽድቅ ፡ ትመለሳለችና ፡
ልባቸውም ፡ የቀና ፡ ሁሉ ፡ ይከተሉታል ።
፲፮፡ ማነው ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ የሚነሣ ፡ በክፎች ፡ ላይ ።
ማንስ ፡ ይቆምልኛል ፡ ግፍ ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ።
፲፯፡ እግዚአብሔር ፡ ለረዳት ፡ ባይሆንልኝ ፡
ነፍሴ ፡ ለጥቂት ፡ በዝምታ ፡ ባደረች ፡
፲፰፡ እግሮቼ ፡ ተሰናከሉ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ፡
ምሕረትኽ ፡ አቤቱ ፡ አጸናቸኝ ።
፲፱፡ የልቤ ፡ ትካዜ ፡ በበዛች ፡ ጊዜ ፡
ማጽናናትኽ ፡ ነፍሴን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ።
፳፡ የግፍ ፡ ዙፋን ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ያብራልን ፡
በሕግ ፡ ፈንታ ፡ ድካምን ፡ የሚፈጥር ።
፳፩፡ በጻድቅ ፡ ነፍስ ፡ ላይ ፡ ይሰበሰባሉ ፡
ንጹሕ ፡ ደምንም ፡ ይኰንናሉ ።
፳፪፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ መጠጊያ ፡ ሆነልኝ ፡
አምላኬም ፡ አምባዬ ፡ ተስፋዬም ፡ ነው ።
፳፫፡ ግፋቸውንም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ይመልሳል ።
በክፋታቸውም ፡ ያጠፋቸዋል ።
እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ያጠፋቸዋል ።

---

አሥራ ፡ ዘጠነኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፺፭ ።

፩፡ ኑ ፡ ደስ ፡ ይበለን ፡ በእግዚአብሔር ፡
እልልም ፡ እንበል ፡ ለመድኃኒታችን ፡ አምባ ።
፪፡ ወደ ፊቱ ፡ እንድረስ ፡ በምስጋና ፡
በዝማሬም ፡ እልል ፡ እንበልለት ።
፫፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡
ታላቅ ፡ ንጉሥም ፡ ባማልክት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ።

፬፡ የምድር ፡ ጥልቆች ፡ በእጁ ፡ ናቸውና ፡
የተራሮችም ፡ ከፍታዎች ፡ ለርሱ ፡ ናቸው ።
፭፡ ባሕር ፡ የርሱ ፡ ነው ፡ እርሱም ፡ ፈጠረው ።
እጆቹም ፡ ደርቅን ፡ ፈጠሩ ።
፮፡ ኑ ፡ እንስገድ ፡ እንገዛም ።
በፈጠረን፡በእግዚአብሔር፡ፊት ፡ በጕልበታችን፡እንበርክክ።
፯፡ እርሱ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ።
እኛም ፡ የመሰማርያው ፡ ሕዝብ ፡ ነን ፡ የመንጋውም ፡ በጎች ።
ዛሬ ፡ እላንት ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙ ፡
፰፡ ልባችሁን ፡ አታጽኑ ። በምሪባ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
በመሳም ፡ ቀን ፡ በምድረ ፡ በደ ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፱፡ አባቶቻችሁ ፡ በፈተኑኝ ፡ ጊዜ ፡
ፈተኑኝ ፡ ስራዬንም ፡ አዩ ።
፲፡ አርባ ፡ አመት ፡ በዚያች ፡ ትውልድ ፡ ደከምሁ ።
እሌህም ፡ ልባቸው ፡ የሚስት ፡ ሕዝብ ፡ ናቸው ፡
እርሳቸውም ፡ መንገዴን ፡ አያውቁም ፡ አልሁ ።
፲፩፡ ባቍጣዬም ፡ ማልሁባቸው ፡ ወደ ፡ ዕረፍቴ ፡ እንዳይገቡ ።

## መዝሙር ፡ ፺፮፡

፩፡ ለእግዚአብሔር ፡ አዲስ ፡ ቅኔን ፡ ቅኙለት ።
ቅኙ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ ሁሉ ።
፪፡ ቅኙ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስሙንም ፡ ባርኩ ።
ከቀን ፡ ወደ ፡ ቀን ፡ በማደኑ ፡ አውሩ ።
፫፡ ምስጋናውን ፡ ለአሕዛብ፡ንገሩ፡ለአሕዛብ፡ሁሉ፡ታምራቱን።
፬፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነውና፡ ምስጋናውም ፡ ብዙ ፡ ነውና።
የተፈራም ፡ ነውና ፡ በአማልክት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ።
፭፡ የአሕዛብ ፡ አምላኮች ፡ ሁሉ ፡ ጣዖታት ፡ ናቸውና ።
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ሰማዮችን ፡ ሰራ ።
፮፡ ምስጋናና ፡ ሸልም ፡ በፊቱ ፡ ናቸው ፡
ኃይልና ፡ ጌጽም ፡ በመቅደሱ ።
፯፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምጹ ፡ የአሕዛብ ፡ ነገዶች ።
ለእግዚአብሔር ፡ ክብርንና ፡ ኃይልን ፡ አምጹ ።



፰፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሰሙን ፡ ክብር ፡ አምጹ ።
መሥዋዕት ፡ ይዛችሁ ፡ ወደ ፡ ቦታው ፡ ግቡ ።
፱፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስገዱ ፡ በቅድስና ፡ ጌጽ ።
ምድር ፡ ሁልዋ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትፍራ ።
፲፡ በአሕዛብ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፡ በሉ ።
ዓለምንም ፡ አጸና ፡ እንደትናወጽ ።
በአሕዛብ ፡ በቅን ፡ ይፈርደል ።
፲፩፡ ሰማዮች ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ምድርም ፡ ሐሤት ፡ ታድርግ።
ባሕር ፡ ይናወጽ ፡ በርሱም ፡ ያለ ፡ ሁሉ ።
፲፪፡ ምድረ ፡ በደ ፡ ደስ ፡ ይበላት ፡ በርስዋም ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የዱር ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይላታል ።
፲፫፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ። ይገባልና ።
በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይገባልና ።
በዓለም ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርደል ፡ በአሕዛብም ፡ በእውነቱ ።

## መዝሙር ፡ ፺፯፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ። ምድር ፡ ሐሤት ፡ ታድርግ ።
ብዙ ፡ ደሴቶችም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፪፡ ደመና ፡ ጽጋግም ፡ በዙርያው ፡ ነው ።
ጽድቅና ፡ ፍርድ ፡ የዙፋኑ ፡ ደገፋ ፡ ነው ።
፫፡ እሳት ፡ በፊቱ ፡ ይሔደል። ጸላቶቹንም ፡ በዙርያው ፡ ያነደል።
፬፡ መብረቆቹ ፡ ለዓለም ፡ አበሩ ።
ምድር ፡ አየችና ፡ ተናወጸች ።
፭፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ሰምዕ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቀለጡ ፡
የምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ባለ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ።
፮፡ ሰማዮች ፡ ጽድቁን ፡ አወሩ ።
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ክብሩን ፡ አዩ ።
፯፡ ለጣዖት ፡ የሚሰግዱ ፡ ሁሉ ፡ ደፈሩ ፡
በጣዖታትም ፡ የሚመኩ ።
ስገዱለት ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ።
፰፡ ፅዮን ፡ ሰማች ፡ ደስም ፡ አላት ፡
የደሁዳም ፡ ልጆች ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ ስለ ፡ ፍርድኽ ፡ አቤቱ።

፱ ፡ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ ነህና ፡ በመድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
እጅግም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አልህ ፡ ካምላኮች ፡ ሁሉ ፡ በላይ ።
፲ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትወዱ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ ጽሉ ።
የቅዱሳኑን ፡ ነፍሶች ፡ ይጠብቃል ፡
ከኃጥኣን ፡ እጅ ፡ ያድናቸዋል ።
፲፩ ፡ ብርሃን ፡ ለጻድቃን ፡ ተዘራ ፡
ደስታም ፡ ልባቸው ፡ ቅን ፡ ለሆነ ።
፲፪ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ጻድቃን ፡ በእግዚአብሔር ፡
በቅድስናውም ፡ አሳብ ፡ አመስግኑት ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፺፰ ፡

፩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አዲስ ፡ ቅኔን ፡ ቅኙ ፡
እርሱ ፡ ድንቅ ፡ አድርጓልና ።
ቀኙ ፡ አድናለታለችና ፡ የተቀደሰችም ፡ ክንዱ ።
፪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማዳኑን ፡ አሰታወቀ ።
በአሕዛብ ፡ ፊትም ፡ ጽድቁን ፡ ገለጸ ።
፫ ፡ ምሕረቱን ፡ አሰበ ፡ እውነቱንም ፡ ለእሥራኤል ፡ ቤት ።
የምድር ፡ ዳር ፡ ሁሉ ፡ የአምላካችነን ፡ መድኃኒት ፡ አዩ ።
፬ ፡ አንቺ ፡ መድር ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በይ ።
አመስግኑ ፡ ደስም ፡ ይበላችሁ ፡ ዝማሬም ፡ አቅርቡ ።
፭ ፡ በመሰንቆ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ። በመሰንቆ ፡ በዝ
ማሬም ፡ ድምፅ ።
፮ ፡ በምስር ፡ ቃና ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡
በንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እልል ፡ በሉ ።
፯ ፡ ባሕር ፡ ትንቀሳቀስ ፡ በርስዋም ፡ ያለ ፡ ሁሉ ፡
ዓለም ፡ በርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ።
፰ ፡ ፈሳሾች ፡ እጅን ፡ ይጽፉ ። ተራሮች ፡ ባንድ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ። በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይመጻልና ፡
በዓለምም ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርዳል ፡ በአሕዛብም ፡ በቅን ።



መዝሙር ፡ ፺፱ ፡

፩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ። አሕዛብ ፡ ይደንግፁ ።
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ። ምድር ፡ ትናወጥ ።
፪ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፅዮን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡
እርሱም ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ።
፫ ፡ ታላቅ ፡ ስምህን ፡ ያመስግኑ ። የተፈራ ፡ የተቀደሰም ፡ ነውና ።
፬ ፡ የንጉሥንም ፡ ኃይል ፡ የፍርድ ፡ ወዳጅ ፡
አንተ ፡ ቅንነትን ፡ አጸናህ ።
አንተም ፡ በያዕቆብ ፡ ፍርድና ፡ ጽድቅን ፡ አደረግህ ።
፭ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምላካችነን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጉ ፡
ወደ ፡ እግሩም ፡ መቀመጫ ፡ ስገዱ ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።
፮ ፡ ሙሴ ፡ ሐሮንም ፡ በካህናቱ ፡ ሳሙኤልም ፡ ስሙን ፡ በሚጸሩ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ጸሩት ፡ እርሱም ፡ መለሰላቸው ።
፯ ፡ በደመና ፡ ዓምድ ፡ ተናገራቸው ።
ምስክሩን ፡ ጠበቁ ፡ የሰጣቸውንም ፡ ትእዛዝ ።
፰ ፡ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ አንተ ፡ መለስህላቸው ።
ይቅር ፡ ባይም ፡ አምላክ ፡ ሆንህላቸው ።
በስራቸው ፡ ግን ፡ ተበቀልህላቸው ።
፱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምላካችነን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጉ ።
ወደ ፡ ተቀደሰችም ፡ ተራራ ፡ ስገዱለት ።
እግዚአብሔር ፡ አመላካችን ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።

መዝሙር ፡ ፻ ፡

፩ ፡ አንቺ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በይ ።
፪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዙ ፡ በደስታ ፡ በፊቱም ፡ ግቡ ፡ በልልታ ።
፫ ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እወቁ ።
እርሱ ፡ ፈጠረን ፡ እኛም ፡ አይደለነም ።
እኛስ ፡ ሕዝቡ ፡ የመሰመርያውም ፡ በጎች ፡ ነን ።
፬ ፡ ወደ ፡ ደጆቹ ፡ በመገዛት ፡ ግቡ ፡ ወደ ፡ ቦቶቹም ፡ በምስጋና ።
አመስግኑት ፡ ስሙንም ፡ ባርኩ ።
፭ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነውና ።
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡ እውነቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ።

መዝሙር ፡ ፻፩፡

፩፡ ስለ ፡ ምሕረትና ፡ ስለ ፡ ፍርድ ፡ እቀኛለሁ ።
ላንተም ፡ አቤቱ ፡ ዝማሬን ፡ አቀርባለሁ ።
፪፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ በጅ ፡ ይለኛል ።
መቼ ፡ ወደኔ ፡ ትመጻለኽ ።
በልቤ ፡ ቅንነት ፡ እሔዳለሁ ፡ በቤቴ ፡ ውስጥ ።
፫፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አላኖርም ።
የሕግ ፡ አታላላፊን ፡ ስራ ፡ ጸላሁ ፡ አልተጠጋልኝምም ።
፬፡ ጠማማ፡ልብም፡ከኔ፡ይርቃል ። ክፉውንም፡አላውቅም ።
፭፡ ባልንጀራውን ፡ በቀስታ ፡ የሚያላክከው ፡ እርሱን ፡ አ
ጠፋለሁ ።
ዓይኑ፡የታበየ፡ልቡም፡የሳሳ፡እርሱን፡መታገሥ፡አይቻልኝም።
፮፡ ዓይኖቼ ፡ በምድር ፡ ምእመናን ፡ ላይ ፡ ናቸው ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡
ይቀመጡ ፡ ዘንድ ።
በቀና ፡ መንገድ ፡ የሚሔድ ፡ እርሱ ፡ ያገለግለኛል ።
፯፡ ትንኰል ፡ የሚያደርግ ፡ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ አይኖርም ።
ባሰት ፡ የሚናገር ፡ በፊቴ ፡ አይጸናም ።
፰፡ በማለደ ፡ የምድርን ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ አጠፋለሁ ።
ከእግዚአብሔር ፡ አገር ፡ ዐመፃ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሁሉ ፡
እቈርጥ ፡ ዘንድ ።

ህያ ፡ ቀን ።

---

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፻፪፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ።
ጩኸቴም ፡ ወደንተ ፡ ይግባ ።
፪፡ ፊትኽን ፡ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ከኔ ፡ አትሰውር ።
ጆሮኽን ፡ ወደኔ ፡ ጣል ።
በጸራሁኽ ፡ ቀን ፡ ፈጥነኽ ፡ መልስልኝ ።
፫፡ ዘመኔ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ አልቃለችና ።
አፅንቶቼም ፡ እንደ ፡ መቃጠያ ፡ ተኰሰዋልና ።



፬፡ ልቤ ፡ ተመታ ፡ እንደ ፡ ሣዕርም ፡ ደረቀ ።
እንጀራ ፡ መብላት ፡ ተረስቶኛልና ።
፭፡ ከልቅሶዬ፡ድምፅ፡የተነሣ፡አፅንቴ፡በሥጋዬ፡ይጣበቃል።
፮፡ የውድማውን ፡ ግድግዳ ፡ መሰልሁ ።
በፈረሰ ፡ ቤትም ፡ እንደለች ፡ እንደ ፡ ጉጉት ፡ ሆንሁ ።
፯፡ ተጋሁ ፡ በሰገነትም ፡ ብቻውን ፡ እንደሚኖር ፡ ዎፍ ፡ ሆንሁ ።
፰፡ ጸላቶቼ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ጸየፉኝ ፡
የሚያሳደኙም ፡ በላዬ ፡ ተማማሉ ።
፱፡ አመድን ፡ እንደ ፡ እንጀራ ፡ በልቻለሁና ።
መጠጤንም ፡ ከንቤ ፡ ጋራ ፡ ቀለቀልሁ ።
፲፡ ከቍጣኽ ፡ ከመዓትኽም ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡
አንሥተኽ ፡ ጥለኸኛልና ።
፲፩፡ ዘመኔ ፡ እንደ ፡ ጽላ ፡ ዘንብልዋልና ፡
እኔም ፡ እንደ ፡ ሣዕር ፡ ደርቂያለሁና ።
፲፪፡ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለኽ ፡
መታሰብያኽም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ።
፲፫፡ አንተ ፡ ትነሣለኽ ፡ ፅዮንንም ፡ ትምራለኽ ፡
የምህረትዋ ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፡ ዘመንዋም ፡ ደርስዋልና ።
፲፬፡ ባሮችኽ ፡ ደንጎችዋን ፡ ወደዋልና ፡
ለመሬትዋም ፡ አዝነዋልና ።
፲፭፡ አሕዛብም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ይፈራሉ ፡
የምድርም ፡ ነገሥት ፡ ሁሉ ፡ ክብርህን ።
፲፮፡ እግዚአብሔር ፡ ፅዮንን ፡ ይሠራልና ።
በምስጋናውም ፡ ይገለጻል ።
፲፯፡ ወደ ፡ ችጋረኞች ፡ ጸሎት ፡ አይትዋልና ፡
ልመናቸውንም ፡ እልናቀምና ።
፲፰፡ ይኽ ፡ ለምትመጣ ፡ ትውልድ ፡ ይጻፍ ።
የሚፈጠርም ፡ ሕዝብ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ ይላሉ ።
፲፱፡ ከቅድስና ፡ ከፍታ ፡ ዘንድ ፡ ተመልክትዋልና ፡
እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ በምድር ፡ አይትዋልና ፡
፳፡ የታሠረትን ፡ ልቅሶ ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡
ለሞት ፡ የተለዩትን ፡ ይፈታ ፡ ዘንድ ።

፳፩፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በፅዮን ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡፡
ምስጋናውንም ፡ በየሩሳሌም ፡፡
፳፪፤ አሕዛብ ፡ ባንድ ፡ ሲሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡
መንግሥታትም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡፡
፳፫፤ ኃይሌን ፡ በመንገድ ፡ አደከመ ፡፡ ዘመኔን ፡ አሳጠረ ፡፡
፳፬፤ አልሁም ፡ አምላኬ ፡ በዘመኔ ፡ እኩሌታ ፡ አታንሣኝ ፡፡
ዓመታትኽ ፡ ለልድ ፡ ልጅ ፡ ናቸው ፡፡
፳፭፤ አንተ ፡ ከጥንት ፡ ምድርን ፡ መሠረትኽ ፡
ሰማዮችም ፡ የጅኽ ፡ ስራ ፡ ናቸው ፡፡
፳፮፤ እርሳቸው ፡ ይጠፋሉ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ትቀማለኽ ፡፡
ሁላቸውም ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያርጃሉ ፡
እንደ ፡ መጐናጸፊያም ፡ ትለውጣቸዋለኽ ፡ ይለወጣሉም ፡፡
፳፯፤ አንተ ፡ ግን ፡ እንዲያው ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡፡
አመታትህም ፡ ከቶ ፡ አያልቁም ፡፡
፳፰፤ የባሮችኽ ፡ ልጆች ፡ ያድራሉ ፡ ዘሬቻቸውም ፡ በፊትኽ ፡ ትጸ
ናለች ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፫፤

፩፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡
በውሥጤም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ የተቀደሰውን ፡ ስሙን ፡፡
፪፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡
ላንቺም ፡ ያደረገውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አትርሺ ፡፡
፫፤ ኃጢአትሽን ፡ ሁሉ ፡ የሚተውልኽ ፡፡
ደዌሽንም ፡ ሁሉ ፡ የሚፈውስ ፡፡
፬፤ ሕይወትሽን ፡ ከጥፋት ፡ የሚበዠ ፡
በጸጋና ፡ በምህረትም ፡ የሚያከልልሽ ፡፡
፭፤ ፈቃድሽን ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ የሚያጸግብ ፡፡
ታድሳለችም ፡ እንደ ፡ ንስር ፡ ጐልማስነትሽ ፡፡
፮፤ እግዚአብሔር ፡ ጽድቅን ፡ አድራጊ ፡ ነው ፡ ፍርድንም ፡ ለ
ተበደሉ ፡ ሁሉ ፡፡
፯፤ ለሙሴ ፡ በመንገዱ ፡ አስታወቀ ፡
ለእሥራኤል ፡ ልጆችም ፡ ባደራረጉ ፡፡
፰፤ እግዚአብሔር ፡ መሓሪና ፡ ምህረተኛ ፡ ነው ፡



ቍጣው ፡ የራቀ ፡ ምሕረቱም ፡ የበዛ ፡፡
፱፤ ለወትሮ ፡ አይጣላም ፡ ለዘላለሙም ፡ አይቈጣም ፡፡
፲፤ እንደ ፡ ኃጢአታችን ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ አልሰራም ፡
እንደ ፡ መበደላችንም ፡ አልከፈለልነም ፡፡
፲፩፤ እንደ ፡ ሰማይም ፡ ከፍታ ፡ ከምድር ፡
እንዲሁም ፡ በረታች ፡ ምሕረቱ ፡ በሚፈሩት ፡ ላይ ፡፡
፲፪፤ ምሥራቅ ፡ ከምዕራብም ፡ እንደሚርቅ ፡
እንዲሁ ፡ ኃጢአታችነን ፡ ከኛ ፡ አራቀ ፡፡
፲፫፤ አባት ፡ ለልጆቹ ፡ እንዲራራ ፡
እንዲሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚፈሩት ፡ ይራራል ፡፡
፲፬፤ እርሱ ፡ ፍጥረታችነን ፡ አውቋልና ፡
አፈርም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስብዋልና ፡፡
፲፭፤ ሰውስ ፡ ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ሣዕር ፡ነው ፡
እንደ ፡ በረኻም ፡ አበባ ፡ እንዲህ ፡ ያብባል ፡፡
፲፮፤ ንፋስ ፡ ሲነፍስበት ፡ ጊዜ ፡ ጠፍትዋልና ፡
ስፍራውም ፡ ደግሞ ፡ አያውቀውም ፡፡
፲፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ምሕረት ፡ ግን ፡ እርስዋ ፡ ከዘላለም ፡ ጀ
ምራ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ናት ፡ በሚፈሩት ፡ ላይ ፡፡
ጽድቁም ፡ በልጅ ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ነው ፡፡
፲፰፤ ኪዳኑን ፡ ለሚጠብቁ ፡
ትእዛዙንም ፡ ለሚያስቡ ፡ ያደርጓት ፡ ዘንድ ፡፡
፲፱፤ እግዚአብሔር ፡ ዙፋኑን ፡ በሰማይ ፡ አዘጋጀ ፡፡
መንግሥቱም ፡ ሁሉን ፡ ትገዛለች ፡፡
፳፤ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ፡ እላንት ፡ መላእክቱ ፡ ብርቶች ፡
ኃያላኑ ፡
ቃሉን ፡ የምታደርጉ ፡ የነገሩን ፡ ድምፅ ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡፡
፳፩፤ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡
አገልጋዮቹ ፡ ፈቃዱን ፡ የምታደርጉ ፡፡
፳፪፤ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ፡ ፍጥረቶቹ ፡ ሁሉ ፡ በግዛቱ ፡ ስ
ፍራ ፡ ሁሉ ፡፡
እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡

የማታ ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፻፬

፩ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነህ ፡
ምስጋናንና ፡ ሽልምን ፡ ለበስኽ ።
፪ ብርሃን ፡ እንደ ፡ ቁረን ፡ ለበስኽ ፡
ሰማይንም ፡ እንደ ፡ መጋረጃ ፡ ዘረጋኽ ።
፫ የቤትህ ፡ ማደርዮች ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ናቸው ።
ደመናን ፡ ሠረገላህን ፡ ያደረግህ ።
በንፋስ ፡ ክንፍም ፡ የምትሔድ ።
፬ መላእክቱን ፡ መናፍስትን ፡ የሚያደርግ ።
አገልጋዮቹንም ፡ የምትነደድ ፡ እሳት ፡
፭ ምድርን ፡ በጽናትዋ ፡ ላይ ፡ መሠረታት ፡
ለዘላለም ፡ እንደትናወጽ ።
፮ በቀላይ ፡ እንደ ፡ በልብስ ፡ ከደንኻት ፡
በተራሮችም ፡ ላይ ፡ ውኆች ፡ ይቆማሉ ።
፯ ከመዝለፍህም ፡ ይሸሻሉ ፡
ከነጐድጓድኽም ፡ ድምፅ ፡ ይኰበላሉ ።
፰ ተራሮችም ፡ ይወፃሉ ፡ ቈሎችም ፡ ይወርዳሉ ።
ወደ ፡ መሠረትኽላቸው ፡ ስፍራ ።
፱ ደርቻ ፡ አደረግኽላቸው ፡ አያልፏትምም ፡
አይመለሱምም ፡ ምድርን ፡ ይከድኑ ፡ ዘንድ ።
፲ ምንጮችን ፡ ወደ ፡ ቈሎች ፡ የሚልክ ።
በተራሮች ፡ መኻከል ፡ ውኆች ፡ ያልፋሉ ።
፲፩ የዱርን ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ ያጠጣሉ ፡
የበደ ፡ አህዮችም ፡ ጽማታቸውን ፡ ይሰብራሉ ።
፲፪ የሰማይ ፡ ዎፎች ፡ በርስዋ ፡ ዘንድ ፡ ይኖራሉ ፡
በጫፎች ፡ ማኽልም ፡ ይጮኻሉ ።
፲፫ ተራሮችን ፡ ከላይ ፡ የሚያጠጣ ፡
ከስራኽ ፡ ፍሬ ፡ ምድር ፡ ትጸግባለች ።
፲፬ ሣዕር ፡ ለእንስሳ ፡ የሚያበቅል ፡
መስክንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ለማገልገል ።



እንጀራውን ፡ ከምድር ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ።
፲፭ የወይን ፡ ፀጅም ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡
ፊቱ ፡ በቅቤ ፡ ይበራ ፡ ዘንድ ፡
እንጀራም ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ ያጸናል ።
፲፮ የእግዚአብሔር ፡ ዛፎችም ፡ ይጸግባሉ ፡
የልባኖስም ፡ ዛፎች ፡ እርሱ ፡ የተከላቸው ።
፲፯ ከዚያ ፡ አዕዋፍ ፡ ይዋልዳሉ ።
የለቅለቅ ፡ ቤትም ፡ የበሮሽ ፡ ዛፍ ፡ ነው ።
፲፰ ረጃጅም ፡ ተራሮች ፡ ለዋሎች ፡ አምቦችም ፡ የፈቆች ፡ መ
ሸሻ ፡ ነው ።
፲፱ ጨረቃን ፡ ፈጠረ ፡ ለጊዜያት ።
ፀሐይም ፡ መግቢያውን ፡ ያውቃል ።
፳ ጨለማ ፡ አድርገኽ ፡ ሌት ፡ ይሆናል ፡
በርሱም ፡ ይንቀሳቀሳሉ ፡ የዱር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ።
፳፩ ያንበሳ ፡ ግልገሎች ፡ ለመንጠቅ ።
ከእግዚአብሔርም ፡ ምግባቸውን ፡ ይለምናሉ ።
፳፪ ፀሐይ ፡ ወፃችና ፡ ይሰበሰባሉ ።
በጕድጓደቻቸውም ፡ ይተኛሉ ።
፳፫ ሰውም ፡ ወደ ፡ ተግባሩ ፡ ይወጣል ፡
ወደ ፡ ስራውም ፡ እስኪመሽ ፡ ድረስ ።
፳፬ እንደ ፡ ምን ፡ ይበዛል ፡ ስራኽ ፡ አቤቱ ፡
ሁሉን ፡ በጥበብ ፡ አደረግኽ ፡
ምድርም ፡ ከንገዘብኽ ፡ መላች ።
፳፭ ይኽ ፡ ባሕር ፡ ታላቅ ፡ ሰፊም ፡ ያለ ።
ከዚያ ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ አለ ።
ታናናሽ ፡ እንስሳ ፡ ከታላላቆች ፡ ጋራ ።
፳፮ በዚያ ፡ መርከቦች ፡ ይሔዳሉ ፡
ይኽም ፡ ለዋታን ፡ የፈጠርኸው ፡ ይጫወትበታል ።
፳፯ እለዚኽ ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋሉ ፡
ምግባቸውን ፡ በየጊዜው ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ።
፳፰ አንተ ፡ በሰጠኻቸው ፡ ጊዜ ፡ ይለቅሙታል ፡
እጅኽን ፡ ትከፍታለኽ ፡ ከበበጎ ፡ ነገርህም ፡ ይጸግባሉ ።

፳፱፡ ፊትኽን ፡ ስትሰውር ፡ ይደነግፃሉ ፡፡
ነፍሳቸውን ፡ ታወፃለኽ ፡ ያልቃሉም ፡
ወደ ፡ ወሬታቸውም ፡ ይመለሳሉ ፡፡
፴፡ እስትንፋስኽን ፡ ትልካለኽ ፡ ይፈጠራሉም ፡
የምድርንም ፡ ፊት ፡ ታድሳለኽ ፡፡
፴፩፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ለዘላለሙ ፡ ይሁን ፡
እግዚአብሔር ፡ በስራው ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡፡
፴፪፡ ወደ ፡ ምድር ፡ የሚያይ ፡ ትንቀጠቀጣለችም ፡
ተራሮችን ፡ ቢደስ ፡ ይጤሳሉ ፡፡
፴፫፡ በሕይወቴ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፡፡
ለአምላኬም ፡
እዘምራለሁ ፡ የምኖርበቱን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡፡
፴፬፡ ነገሬ ፡ ይጻፈጥለት ፡፡
እኔ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡፡
፴፭፡ ኃጥኣን፡ከምድር፡ይጥፉ፡፡ ዐመፀኞችም፡እንዳይገኙባት፡፡
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡፡
ሀሌሉያ ፡፡

ህያ ፡ አንደኛ ፡ ቀን ፡፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፭፡

፩፡ እግዚአብሔርን፡አመስግኑ ፡፡ ስሙን ፡ ጽሩ፡፡
ለአሕዛብም ፡ ስራውን ፡ አውሩ ፡፡
፪፡ ቅኙለት ፡ ዘምሩለትም ፡፡ ተአምራቱን ፡ ሁሉ ፡ አጫውቱ ፡፡
፫፡ በቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ተጓደዱ ፡፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚሹት ፡ ልቦች ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡፡
፬፡ እግዚአብሔርን ፡ እሹት ፡ ኃይሉንም ፡
ሁለግዜ ፡ ፊቱን ፡ እሹት ፡፡
፭፡ የሰራትን፡ድንቅ፡አስቡ፡ተአምራቱንም፡ያፉንም፡ፍርድ፡፡
፮፡ የአብርሃም ፡ የባርያው ፡ ዘር ፡
የያዕቆብም ፡ ልጆች ፡ ለርሱ ፡ የተመረጹ ፡፡
፯፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ነው ፡፡



ፍርዱ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡፡
፰፡ ኪዳኑን ፡ ለዘላለም ፡ አሰበ ፡
እስከ ፡ ሺኽ ፡ ትውልድም ፡ ያዘዘበቱን ፡ ቃሉን ፡
፱፡ ለአብርሃም ፡ ይተካየደውን ፡ ለይስሐቅም ፡ የማለውን ፡
፲፡ ለያዕቆብም ፡ ሕግ ፡ ሁኖ ፡ ያቆመውን ፡
ለእሥራኤልም ፡ የዘላለም ፡ ኪዳን ፡፡
፲፩፡ ላንተ ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡ እሰጣለሁ ፡ ብሎ ፡
የርስታችሁ ፡ ገመድ ፡ ትሆንበት ፡ ዘንድ ፡፡
፲፪፡ በቍጥር ፡ ጥቂት ፡ ሳሉ ፡
እጅግ ፡ ጥቂቶችም ፡ በርስዋም ፡ ስደተኞች ፡፡
፲፫፡ ከሕዝብ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ አለፉ ፡
ከመንግሥትም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡፡
፲፬፡ ሰውም ፡ ግፍ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልተወውም ፡
ስለርሳቸውም ፡ ነገሥታትን ፡ ዘለፈ ፡፡
፲፭፡ ቀብቼ ፡ ያነገሥኋቸውን ፡ አትደርሱ ፡
በነቢያቴም ፡ ክፉ ፡ አታድርጉ ፡፡
፲፮፡ በምድር ፡ ላይም ፡ ራብን ፡ ጸራ ፡
የኽልን ፡ ጕልበት ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ፡፡
፲፯፡ በፊታቸው ፡ ሰውን ፡ ላከ ፡
ዮሴፍም ፡ ለባርነት ፡ ተሸጠ ፡፡
፲፰፡ በግር ፡ ብረት ፡ እግሮቹን ፡ አደከሙ ፡
በብረት ፡ ነፍሱ ፡ ገባች ፡፡
፲፱፡ ቃሉ፡እስኪመጻለት፡ድረስ፡፡የእግዚአብሔር፡ቃል፡ፈተነው፡፡
፳፡ ንጉሥ ፡ ላከ ፡ ፈታውም ፡
የአሕዛብም ፡ አለቃ ፡ አስፈታውም ፡፡
፳፩፡ ለቤቱ ፡ ጌታ ፡ አደረገው ፡፡ በጥሪቱም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡፡
፳፪፡ አለቆቹን ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያሥር ፡ ዘንድ ፡
ሽማግሎቹንም ፡ አዋቆች ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡፡
፳፫፡ እሥራኤልም ፡ ወደ ፡ ምሥር ፡ ገባ ፡
ያዕቆብም ፡ በካም ፡ አገር ፡ አደረ ፡፡
፳፬፡ ሕዝቡንም ፡ እጅግ ፡ አበዛ ፡
ከጸላቶቻቸውም ፡ ይልቅ ፡ አበረታቸው ፡፡
፳፭፡ ልባቸውን ፡ መለሰ ፡ ሕዝቡን ፡ ይጸሉ ፡ ዘንድ ፡

በባሮቹም ፡ ላይ ፡ ይተነኰሉ ፡ ዘንድ ።
፳፮ ሙሴንም ፡ ባሪያውን ፡ ላከ ፡
ሐሮንንም ፡ ለነፍሱ ፡ የመረጸውን ።
፳፯ የተአምራቱን ፡ ነገር ፡ አደረጉባቸው ፡
ድንቁንም ፡ በካም ፡ ምድር ።
፳፰ ጨለማ ፡ ላከ ፡ ጨለመችባቸውም ፡
ቃሉንም ፡ አላሳዘኑም ።
፳፱ ውኆቻቸውን ፡ ለደም ፡ ለወጠ ፡
ዓሦቻቸውንም ፡ ገደለ ።
፴ ምድራቸው ፡ ባንጓጉቸር ፡ መላች ፡
ወደ ፡ ንጉሦቻቸውም ፡ ቤት ፡ ገባች ።
፴፩ አለም ፡ የውሻ ፡ ዝምብም ፡ መጻ ፡
ትንኝም ፡ በደርቻቸው ፡ ሁሉ ።
፴፪ ዝናማቸውን ፡ በረዶ ፡ አደረገው ፡
የምትቃጠልም ፡ እሳት ፡ በምድራቸው ፡
፴፫ ወይናቸውንም ፡ በለሳቸውንም ፡ መታ ፡
ያገራቸውንም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ።
፴፬ አለም ፡ አንበጣም ፡ መጻ ፡
ቍጥርም ፡ የሌለው ፡ ኩብኩባ ።
፴፭ ያገራቸውንም ፡ ለምለም ፡ ሁሉ ፡ በላ ፡
የምድራቸውንም ፡ ፍሬ ፡ በላ ።
፴፮ ያገራቸውን ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ፡
የኵብታቸውን ፡ ሁሉ ፡ መጀመርያ ።
፴፯ በወርቅና ፡ በብርም ፡ አወጣቸው ፡
በነገዶቻቸውም ፡ ደካማ ፡ አልነበረባቸውም ።
፴፰ ምሥርም ፡ በመውጣታቸው ፡ ደሳላት ።
ፍርሃታቸው ፡ ወድቆባቸው ፡ ነበረና ።
፴፱ ደመና ፡ ለመሸፈኛ ፡ ዘረጋባቸው ፡
እሳትንም ፡ በሌት ፡ ያበራላቸው ፡ ዘንድ ።
፵ ለመኑ ፡ ድርጭትም ፡ አስመጻላቸው ፡
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ አጸገባቸው ።
፵፩ አምባውንም ፡ ከፈተ ፡ ውኃም ፡ ፈሰሰች ፡
ፈሳሾችም ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ ስፍራ ፡ አለፉ ።



፵፪ ቅዱስ ፡ ቃሉን ፡ አስብዋልና ፡
ለአብርሃም ፡ ለባሪያው ፡ የነገረውን ።
፵፫ ሕዝቡንም ፡ በደስታ ፡ አወፃ ። የተመረጹትንም ፡ በልልታ ።
፵፬ የአሕዛብንም ፡ አገር ፡ ሰጣቸው ፡
አሕዛብም ፡ የደከሙበትን ፡ ወረሱ ።
፵፭ ሕጉን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ። ሥርዓቱንም ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ።
ሀሌሉያ ።

የ ማ ታ ፡ ጸ ሎ ት ።
መዝሙር ፡ ፻፮፡

፩ ሀሌሉያ ።
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ፡ ምሕረቱም ፡ ለ
ዘላላም ፡ ነውና ።
፪ የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ ማን ፡ ይናገራል ፡
ምስጋናውም ፡ ሁሉ ፡ ማን ፡ ያሰማል ።
፫ ፍርድ ፡ የሚጠብቁ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ፡
ሁለግዜም ፡ ጽድቅን ፡ የሚያደርግ ።
፬ አስበኝ፡አቤቱ፡በሕዝብኽ፡ጸጋ።በመድኃኒትህም፡ጐብኘኝ።
፭ የመረጥኻቸውን ፡ በጐነት ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡
በሕዝብኽም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ዘንድ ፡
ከርስትኽ ፡ ጋራ ፡ እጓደድ ፡ ዘንድ ።
፮ ካባቶቻችን፡ጋራ፡ኃጢአት፡ሰራን።በደልነም፡ግፍም፡አደረግን።
፯ አባቶቻችን ፡ በምሥር ፡ ሳሉ ፡ ተአምራትኽን ፡ አላስተ
ውሉም ፡
የምሕረትኽንም ፡ ብዛት ፡ አላሰቡም ፡
በባሕርም ፡ ዐመፁብኽ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በኵል ።
፰ ስለ ፡ ስሙም ፡ አደናቸው ። ጕልበቱን ፡ ለማስታወቅ ።
፱ የኤርትራንም ፡ ባሕር ፡ ዘለፈ ፡ እርሱም ፡ ደረቀ ።
በጥልቅም ፡ መራቸው ፡ እንደ ፡ በምድረ ፡ በዳ ።
፲ ከሚጸላቸውም ፡ እጅ ፡ አደናቸው ፡
ከጸላትም ፡ እጅ ፡ ተበዣቸው ።
፲፩ ያሳደድዋቸውንም ፡ ውኃ ፡ ደፈናቸው ።

ከርሳቸውም ፡ አንድ ፡ አልቀረም ።
፲፪፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በቃሉ ፡ አመኑ ፡
በምስጋናውም ፡ ቀኙለት ።
፲፫፤ ደግሞም ፡ ስራውን ፡ መርሳት ፡ አፈጠኑ ፡
በምክሩም ፡ አልታገሡም ።
፲፬፤ በምድረ ፡ በደም ፡ ማማር ፡ አማሬቸው ፡
እግዚአብሔርን ፡ በውድማ ፡ ተፈታተኑት ።
፲፭፤ የለመኑትንም፡ሰጣቸው።ለነፍሳቸው፡ግን፡ጥፋትን፡ላከ።
፲፮፤ ሙሴንም ፡ ተቀኑ ፡ በሰፈር ፡
ሐሮንንም ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀደሰውን ፡
፲፯፤ ምድርም ፡ ተከፈተች ፡ ዳታንንም ፡ ዋጠች ፡
የአቤሮንንም ፡ ወገን ፡ ደፈነች ።
፲፰፤ በማኅበሬቸውም ፡ እሳት ፡ ነደደች ፡
ነበልባል ፡ ኃጥአንን ፡ አቃጠላቸው ።
፲፱፤ በኮሬብም ፡ ጥጃውን ፡ አደረጉ ። ለጣዖትም ፡ ሰገዱ ።
፳፤ ክብሬቸውንም ፡ ለወጡ ፡ ሣር ፡ በሚበላ ፡ በበሬ ፡ ምሳሌ ።
፳፩፤ ያዳናቸውንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ረሱት ፡
በግብጽ ፡ ታላቅ ፡ ነገርን ፡ ያደረገውን ።
፳፪፤ ድንቅም፡በካም፡ምድር።ግሩም፡ነገርንም፡በኤርትራ፡ባሕር።
፳፫፤ አለም ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡
ለርሱ ፡ የተመረጸ ፡ ሙሴ ፡ በፊቱ ፡ በፍራሽ ፡ ባይቆም ፡
ቍጣውን ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ እንዳያጠፋቸው ።
፳፬፤ የተወደደችንም ፡ ምድር ፡ ናቁ ፡
በቃሉም ፡ አልታመኑም ።
፳፭፤ በድንኳኖቻቸውም ፡ አንጐረጐሩ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ አልሰሙም ።
፳፮፤ እጁንም፡አነሣባቸው፡በምድረ፡በዳ፡ይጥላቸው፡ዘንድ።
፳፯፤ ዘሬቸውንም ፡ በአሕዛብ ፡ መኻከል ፡ ይጥል ፡ ዘንድ ፡
በምድሮችም ፡ ይበትናቸው ፡ ዘንድ ።
፳፰፤ ከብዔል ፡ ፌጎርም ፡ ጋራ ፡ ተገናኙ ፡
የሙትንም ፡ መሥዋዕት ፡ በሉ ።
፳፱፤ በስሬቸውም ፡ አስቈጡት ። ቸነፈርም ፡ ወደቀባቸው ።



፴፤ ፊንሐስ ፡ ግን ፡ ተነሣ ፡ ፈረደባቸውም ።
ቸነፈርም ፡ ከርሳቸው ፡ ተከለከለች ።
፴፩፤ ያም ፡ ጽድቅ ፡ ሁኖ ፡ ተቈጠረለት ፡
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ።
፴፪፤ በክርክር፡ውኃም፡አስቈጡት።ስለርሳቸውም፡ሙሴ፡ተጐዳ።
፴፫፤ መንፈሱን፡አሳዝነዋልና፡በከንፈሮቹም፡በስንፍና፡ተናገረ።
፴፬፤ እግዚአብሔር ፡ ያላቸውንም ፡ አሕዛብ ፡ አላጠፉም ።
፴፭፤ ከአሕዛብም ፡ ጋራ ፡ ተደበለቁ ፡ ስሬቸውንም ፡ ተማሩ ።
፴፮፤ ለጣዖታቸውም ፡ ተገዙ ። ለወጽመድም ፡ ሆኑባቸው ።
፴፯፤ ወንዶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ለሰይ
ጣናት ፡ ሠው ።
፴፰፤ ንጹሕ ፡ ደምንም ፡ አፈሰሱ ፡
የወንዶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ የሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ደም ፡
ለከነዓን ፡ ጣዖታት ፡ የሠውዋቸውን ።
ምድርም ፡ በደም ፡ ረኰሰ ።
፴፱፤ በስሬቸውም ፡ ረኰሱ ። በማድረጋቸውም ፡ አመነዘሩ ።
፵፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነደደ ፡
ርስቱንም ፡ ተጸየፈ ።
፵፩፤ ባሕዛብም ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፡
የሚጸልዋቸውም ፡ ገዝዋቸው ።
፵፪፤ ጸላቶቻቸውም፡ተጋፏቸው።ከጃቸውም፡በታች፡ተዋረዱ።
፵፫፤ ስንተግዜ ፡ ያዳናቸው ፡
እርሳቸው ፡ ግን ፡ በምክሬቸው ፡ አስመረሩት ።
በኃጢአታቸውም ፡ ተዋረዱ ።
፵፬፤ እርሱም፡እንደ፡ተጨነቁ፡አየ።ጩኸታቸውን፡በሰማ፡ጊዜ።
፵፭፤ ለርሳቸውም፡ኪዳኑን፡አሰበ። እንደ፡ምሕረቱም፡ብዛት፡
አዘነላቸው ።
፵፮፤ ሞገስንም ፡ ሰጣቸው ፡ በማረኳቸው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ።
፵፯፤ አድነነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡
ከአሕዛብም ፡ ማኸል ፡ ሰብስበነ ፡
ቅዱስ ፡ ስምኽን ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡
በምስጋናኽም ፡ እንመካ ፡ ዘንድ ።

፵፰፤ እግዚአብሔር ፡ የእሥራኤል ፡ አምላክ ፡ ይባረክ ፡ ከዘላ
ለም ፡ ለዘላለም ።
ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይበል ። ሃሌሉያ ።

ሀያ ፡ ሁለተኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፻፯ ፤

፩፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ፡
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፪፤ ይበሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የዳኑ ፡
ከጸላታቸው ፡ እጅ ፡ ያደናቸው ፡
፫፤ ከብዙ ፡ ምድርም ፡ ሰበሰባቸው ፡
ከምሥራቅ ፡ ከምዕራብም ፡ ከሰሜንም ፡ ከደቡብም ።
፬፤ ተቅበዘበዙ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ መንገድ ፡
የደመቀችውንም ፡ አገር ፡ አላገኙም ።
፭፤ ተራቡ ፡ ተጸሙም ፡ ነፍሳቸውም ፡ ተጨነቀችባቸው ።
፮፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፡ በጨነቃቸው ፡ ጊዜ ፡
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፯፤ የቀናም ፡ መንገድ ፡ መራቸው ፡
ሰው ፡ ወደሚኖርባት ፡ አገር ፡ ይሔዱ ፡ ዘንድ ።
፰፤ የእግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ ያመስግኑ ፡
ድንቁንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ።
፱፤ የተቅበዘበዘችን ፡ ነፍስ ፡ አጽግብዋልና ፡
የተራበችንም ፡ ነፍስ ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ መልትዋልና ።
፲፤ በጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጽላ ፡ የነበሩ ፡
በችጋር ፡ በብረትም ፡ የታሠሩ ።
፲፩፤ ለእግዚአብሔር ፡ ነገር ፡ እምቢ ፡ ብለዋልና ፡
የልዑልንም ፡ ምክር ፡ አቃለዋልና ።
፲፪፤ ልባቸውንም ፡ በድካም ፡ አዋረደ ፡
ተሰናከሉ ፡ የሚረዳቸውንም ፡ አጡ ።
፲፫፤ እርሳቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡



ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፲፬፤ ከጨለማም ፡ ከሞትም ፡ ጽላ ፡ አወፃቸው ፡
እሥራታቸውንም ፡ ቊረጠላቸው ።
፲፭፤ የእግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ ያመስግኑ ፡
ድንቁንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ።
፲፮፤ የናሱን ፡ ደጆች ፡ ሰብርዋልና ፡
የብረቱንም ፡ መወርወርያ ፡ ቊርጥዋልና ።
፲፯፤ ሰነፎች ፡ ስለ ፡ ዓመፃቸው ፡ ስለ ፡ ኀጢአታቸውም ፡ ተቸገሩ ።
፲፰፤ መብልን ፡ ሁሉ ፡ ሰውነታቸው ፡ ጸላች ፡
ወደ ፡ ሞትም ፡ ደጆች ፡ ደረሱ ።
፲፱፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳፤ ቃሉን ፡ ላከ ፡ ፈወሳቸውም ፡ ከጥፋታቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳፩፤ የእግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ ያመስግኑ ፡
ድንቁንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ።
፳፪፤ የምስጋና ፡ መሥዋዕትንም ፡ ይሠውለት ፡
በልልታም ፡ ስራውን ፡ ይንገሩ ።
፳፫፤ በመርከቦች ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የሚወርዱ ፡
በብዙ ፡ ውኃ ፡ ተግባራቸውን ፡ የሚሰሩ ።
፳፬፤ እርሳቸውስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስራ ፡ አዩ ፡
በጥልቅም ፡ ያለችውን ፡ ድንቁን ።
፳፭፤ አለም ፡ ዓውሎ ፡ ንፈስም ፡ ተነሣ ፡
ሞገድም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
፳፮፤ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይወጣሉ ፡ ወደ ፡ ጥልቅም ፡ ይወርዳሉ ፡
ነፍሳቸውም ፡ በጉስቊልና ፡ ቀለጠች ።
፳፯፤ እንደ ፡ በስካርም ፡ ተንከባለሉ ፡ ተናወጡም ፡
ጥበባቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተዋጠች ።
፳፰፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳፱፤ ዓውሎንም ፡ ጸጥ ፡ አሰኘቶ ፡ አቆመ ፡
ሞገድም ፡ አረፈች ።
፴፤ ደስም ፡ አላቸው ፡ አርፈለችና ።

ወደ ፡ ወደዱትም ፡ ወደብ ፡ መራቸው ፡፡
፴፩፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ ያመስግኑ ፡
ድንቁንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡፡
፴፪፡ በአሕዛብ ፡ ጉባዔ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያድርጉት ፡
በሽማግሎችም ፡ መቀመጫ ፡ ያመስግኑት ፡፡
፴፫፡ ፈሳሾችን ፡ መድረ ፡ በዳ ፡ አደረጋቸው ፡፡
የውኃውንም ፡ ምንጮች ፡ መጸምያ ፡፡
፴፬፡ የምታፈራን ፡ ምድር ፡ ጨው ፡ አደረጋት ፡
ከተቀመጡባት ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡፡
፴፭፡ ምድረ ፡ በዳን ፡ ለውኃ ፡ መቆምያ ፡ አደረገ ፡
ውኃ ፡ የሌለበቱንም ፡ ምድር ፡ የውኃ ፡ ምንጮች ፡ አደረገው ፡፡
፴፮፡ ከዚያም ፡ የተራቡትን ፡ አስቀመጠ ፡፡
የሚኖሩበትንም ፡ አገር ፡ ሠሩ ፡፡
፴፯፡ እርሾቹን ፡ ዘሩ ፡ ወይኖችንም ፡ ተከሉ ፡
የፍሬንም ፡ ብዛት ፡ አደረጉ ፡፡
፴፰፡ ባረካቸውም ፡ እጅግም ፡ በዙ ፡፡
እንስሳቸውንም ፡ አላሳነሰባቸውም ፡፡
፴፱፡ ደግሞም ፡ አነሱ ፡ ተጐሰቈሉም ፡
በክፉ ፡ ጕስቍልና ፡ ባዘንም ፡፡
፵፡ ባለቆች ፡ ላይ ፡ እፍረት ፡ አፈሰሰ ፡፡
መንገድም ፡ በሌለበት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አሳታቸው ፡፡
፵፩፡ ችጋረኛንም ፡ ከችጋሩ ፡ አነሣው ፡፡
ወገኖችንም ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ መንጋ ፡ አደረገ ፡፡
፵፪፡ ቅኖች ፡ ያነን ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡
ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አፉዋን ፡ ትዘጋለች ፡፡
፵፫፡ አዋቂ ፡ የሆነ ፡ ይህነን ፡ ይጠብቃል ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ምሕረት ፡ ያስተውላል ፡፡

የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፯፡

፩፡ ልቤ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ፡ አቤቱ ፡፡
እቀኛለሁ ፡ በክብሬም ፡ እዘምራለሁ ፡፡



፪፡ ተነሣ ፡ በገና ፡ ሆይ ፡ መሰንቆም ፡፡
ማልጄ ፡ እነሣለሁ ፡፡
፫፡ ባሕዛብ ፡ መካከል ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ አቤቱ ፡
በሰዎችም ፡ መካከል ፡ እዘምርልሃለሁ ፡፡
፬፡ ምሕረትኽ ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብላለችና ፡
እውነትህም ፡ ወደ ፡ ደመናት ፡ ትደርሳለችና ፡፡
፭፡ አቤቱ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ በሰማዮች ፡ ላይ ፡
ምስጋናኽም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ፡፡
፮፡ ወዳጆችኽ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡
በቀኝኽ ፡ አድነኝ ፡ መልስልኝም ፡፡
፯፡ እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ተናገረ ፡፡
ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሴኬምንም ፡ እካፈላለሁ ፡
የሳኩትንም ፡ ቈላ ፡ እሰፍራለሁ ፡፡
፰፡ ገለዓድ ፡ የኔ ፡ ነው ፡፡ ምናሴም ፡ የኔ ፡ ነው ፡፡
ኤፍሬም ፡ የራሴ ፡ ኃይል ፡ ነው ፡፡ ይሁዳም ፡ አዛዤ ፡ ነው ፡፡
፱፡ ሞአብ ፡ መታጠቢያዬ ፡ ነው ፡፡ በኤዶምያስ ፡ ላይ ፡ ጫማ
ዬን ፡ አረግፋለሁ ፡፡
የፍልስጥኤምን ፡ ሰዎች ፡ ድል ፡ ነሣሁ ፡፡
፲፡ ወደ ፡ ጸናች ፡ አገር ፡ ማን ፡ ይወስደኛል ፡፡
ማን ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ፡ ይመራኛል ፡፡
፲፩፡ አንተ ፡ አይደለኽምን ፡ አቤቱ ፡ የጣልኸነ ፡
ከሠራዊታችንም ፡ ጋራ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አትወፃም ፡፡
፲፪፡ ከመከራችን፡ረድኤት፡ስጠነ፡፡የሰው፡ማዳን፡ከንቱ፡ነውና፡፡
፲፫፡ በእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ እናደርጋለን ፡፡
እርሱም ፡ ጸላቶቻችነን ፡ ይረግጻል ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፰፡

፩፡ የምስጋናዬ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ዝም ፡ አትበል ፡፡
፪፡ የከፋውን ፡ አፍ ፡ የተንኰልንም ፡ አፍ ፡ ከፍተውብኛልና ፡፡
በላዬም ፡ በሽንግላ ፡ መላስ ፡ ተናገሩ ፡፡
፫፡ በመጽላትም ፡ ነገር ፡ ከበቡኝ ፡፡ በከንቱም ፡ ይዋጉኛል ፡፡
፬፡ ስለ ፡ ወደድኋቸው ፡ አጻሉኝ ፡፡ እኔ ፡ ግን ፡ እጸልያለሁ ፡፡

፭፡ በበጐነትም ፡ ፈንታ ፡ ክፉ ፡ መለሱልኝ፡
በወደጅነትም ፡ ፈንታ ፡ ጸላትነት ፡፡
፮፡ በላዩ ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ሹምበት ፡፡
ሰይጣንም ፡ በቀኙ ፡ ይቁም ፡፡
፯፡ በተምዋገተ ፡ ጊዜ ፡ ተረትቶ ፡ ይውጣ ፡፡
ጸሎቱም ፡ ኃጢአት ፡ ትሁንበት ፡፡
፰፡ ዘመኖቹም፡ጥቂት፡ይሁኑ፡፡ሹመቱንም፡ሌላ፡ይውሰደት፡፡
፱፡ ልጆቹ ፡ የተተው ፡ ይሁኑ ፡፡ ምሽቱም ፡ መበለት ፡ ትሁን ፡፡
፲፡ ልጆቹም ፡ ተቅበዝብዘው ፡ ይዙሩ ፡ ይለምኑም ፡
ከተፈታም ፡ ከቤታቸው ፡ እንጀራ ፡ ይሹ ፡፡
፲፩፡ አራጭም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይበርብረው ፡
እንግዶችም ፡ ድካሙን ፡ ይንጠቁት ፡፡
፲፪፡ ምሕረት ፡ የሚያደርገውን ፡ አያግኝ ፡፡
ለተጣሉ ፡ ልጆቹም ፡ የሚራራ ፡ አይሁን ፡፡
፲፫፡ ልጆቹ ፡ ይቍረጡ ፡፡ በሁለተኛም ፡ ትውልድ ፡ ስማቸው ፡ ይደምሰስ ፡፡
፲፬፡ ያባቶቹ ፡ ኃጢአት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትታሰብ ፡
የናቱም ፡ ኃጢአት ፡ አትጥፋ ፡፡
፲፭፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሁልግዜ ፡ ይኑር ፡
መጸሪታቸውንም ፡ ከምድር ፡ ያጥፋ ፡፡
፲፮፡ ምሕረት ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ አላሰበምና ፡፡
ችጋረኛንም ፡ ምስኪንንም ፡ ሰው ፡ አሳደደ ፡
ልቡ ፡ የተሰበረውን ፡ ሊገለው ፡፡
፲፯፡ መርገምን ፡ ወደደ ፡ መጣችበትም ፡፡
በረከትንም ፡ አልወደደም ፡ ከርሱም ፡ ራቀች ፡፡
፲፰፡ መርገምንም ፡ እንደ ፡ ቈረሌ ፡ ለበሰ ፡፡
እንደ፡ውኃም፡ወደንጀቱ፡ገባች፡እንደ፡ቅቤም፡ወደጥንቱ፡፡
፲፱፡ እንደሚለብሰው ፡ ልብስ ፡ ትሁንበት ፡፡
ለመታጠቅያውም ፡ ወትሮ ፡ ይታጠቀው ፡፡
፳፡ ይኽ ፡ ስራ ፡ በሚያጻሉኝ ፡ ላይ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ይድረስ ፡፡
በነፍሴም ፡ ክፉ ፡ በሚናገሩ ፡ ላይ ፡፡



፳፩፡ አንተ፡ግን፡አቤቱ፡ጌታዬ፡ከኔ፡ጋራ፡አድርግ፡ስለ፡ስምኽ፡፡
ምሕረትኽ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡ አድነኝ ፡፡
፳፪፡ እኔ ፡ ችጋረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝና ፡
ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ቍሰለ ፡፡
፳፫፡ እንደለፈ ፡ ጽላ ፡ ሒጀለሁና ፡፡ እንደንበጣም ፡ ተነደሁ ፡፡
፳፬፡ ጕልበቶቼ ፡ በጾም ፡ ደከሙ ፡፡
ሥጋዬም ፡ ተለወጠ ፡ ቅቤ ፡ በማጣት ፡፡
፳፭፡ እኔም ፡ ለርሳቸው ፡ ለነውር ፡ ሆንሁ ፡፡
አዩኝም ፡ ራሳቸውንም ፡ ነቀነቁ ፡፡
፳፮፡ እርዳኝ ፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡፡
እንደ ፡ ምሕረትኽም ፡ አድነኝ ፡፡
፳፯፡ እጅኽም ፡ ይኽች ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ ይወቁ ፡
አንተም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ይህነን ፡ እንደ ፡ አደረግህ ፡፡
፳፰፡ እርሳቸው ፡ ይረግማሉ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ባርክ ፡፡
በኔ ፡ የሚነሡ ፡ ይፈሩ ፡ ባርያኽ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይበለው ፡፡
፳፱፡ የሚያጻሉኝ ፡ ኀፍረትን ፡ ይልበሱ ፡፡
ነወራቸውንም ፡ እንደ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይጐናጸፉዋት ፡፡
፴፡ እግዚአብሔርን ፡ ባፌ ፡ እጅግ ፡ አመሰግናለሁ ፡፡
በታላቆች ፡ ማኸልም ፡ እልል ፡ እልለታለሁ ፡፡
፴፩፡ በድኃ፡ቀኝ፡ቁምዋልና፡፡ነፍሱን፡ከፈራጆች፡ያድን፡ዘንድ፡፡

ህያ ፡ ሶስተኛ ፡ ቀን ፡፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፲፡፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ ጌታዬን ፡ በቀኜ ፡ ተቀመጥ ፡ አለው ፡፡
ጸላቶችኽን ፡ ለግርህ ፡ መቀመጫ ፡ እስካድርግ ፡ ድረስ ፡፡
፪፡ እግዚአብሔር፡የኃይልኽን፡በትር፡ከፅዮን፡ይልክልኻል ፡፡
በጸላቶችኽ ፡ ማኸል ፡ ግዛ ፡፡
፫፡ ሕዝብኽ ፡ እሽተኞች ፡ ይሆናሉ ፡
በብርታትኽ ፡ ቀን ፡ በቅድስና ፡ ጌጽ ፡፡
ከነግህ ፡ ሆድ ፡ እንደሚወጣ ፡ ጠል ፡ ልጆችኽ ፡ ይወለዱልሃል ፡፡
፬፡ እግዚአብሔር ፡ ማለ ፡ አያዝንበትምም ፡

አንተ ፡ ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡
እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሥርዓት ፡ ብሎ ፡፡
፭፡ እግዚአብሔር ፡ በቀኝኽ ፡ ሁኖ ፡ ነገሥታትን ፡ በቍጣው ፡
ይቀጠቅጣል ፡፡
፮፡ በአሕዛብ ፡ ማኽል ፡ ይፈርደል ፡ ሬሶችንም ፡ ያበዛል ፡፡
የብዞችን ፡ ሬሶች ፡ ይቀጠቅጣል ፡ በምድር ፡ ላይ ፡፡
፯፡ ከፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ በመንገድ ፡ ይጠጣል ፡፡
ስለዚኽ ፡ ራሱን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፲፩፡

፩፡ ሀሌሉያ፡፡እግዚአብሔር፡በፍጹም፡ልቤ፡አመሰግንሃለሁ፡፡
በቅኖች ፡ ሸንጎ ፡ በጉባያቸውም ፡፡
፪፡ የእግዚአብሔር ፡ ስራ ፡ ታላቅ ፡ ናት ፡
ለሚሸዋትም ፡ ሁሉ ፡ ያመረች ፡ ናት ፡፡
፫፡ ስራው ፡ ክብርና ፡ ጌጽ ፡ ነው ፡
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለች ፡፡
፬፡ ለድንቁ፡ዝክር፡አደረገ፡፡እግዚአብሔር፡መሐሪና፡ሩሩ፡ነው፡፡
፭፡ ለሚፈሩት ፡ ምግብ ፡ ሰጣቸው ፡
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ ያስባል ፡፡
፮፡ ለሕዝቡ ፡ የስራውን ፡ ብርታት ፡ አሳየ ፡
የአሕዛብን ፡ ርስት ፡ የሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡፡
፯፡ የጀቹ ፡ ስራ ፡ እውነትና ፡ ፍርድ ፡ ነው ፡
ትእዛዙም ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡፡
፰፡ ለዘላለምም ፡ የጸና ፡ ነው ፡፡
በውነትና ፡ በቅንም ፡ የተሰራ ፡ ነው ፡፡
፱፡ መድኃኒትንም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሰደደ ፡፡
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ አዘዘ ፡፡
ስሙ ፡ የተቀደሰ ፡ የተፈራም ፡ ነው ፡፡
፲፡ የጥበብ ፡ መጀመርያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነው ፡፡
ለሚያደርጏት ፡ ሁሉ ፡ ደህና ፡ ማስተዋል ፡ አላቸው ፡፡
ምስጋናው ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፡፡



## መዝሙር ፡ ፻፲፪፡

፩፡ ሀሌሉያ፡፡እግዚአብሔርን፡የሚፈራ፡ሰው፡ምስጉን፡ነው፡
ትእዛዙን ፡ እጅግ ፡ የሚወድ ፡፡
፪፡ ዘሩ ፡ በምድር ፡ ብርቱ ፡ ይሆናል ፡፡
የቅኖች ፡ ትውልድ ፡ ትባረካለች ፡፡
፫፡ ከብትና ፡ ባለጠግነት ፡ በቤቱ ፡ ነው ፡፡
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፡፡
፬፡ ለቅኖች ፡ ብርሃን ፡ በጨለማ ፡ ወጣ ፡፡
መሐሪ ፡ ሩሩም ፡ ጻድቅም ፡ ነው ፡፡
፭፡ ቸር ፡ ሰው ፡ የሚራራ ፡ ነው ፡ የሚያበድርም ፡ ነው ፡፡
በፍርድም ፡ ነገሩን ፡ ይፈጽማል ፡፡
፮፡ ለዘላለም ፡ አይናወጽምና ፡፡
የጻድቅ ፡ መታሰብ ፡ ለዘላለም ፡ ይሆናል ፡፡
፯፡ ክፉን ፡ ከመስማት ፡ አይፈራም ፡፡
ልቡም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታምኖ ፡ ይጸናል ፡፡
፰፡ ልቡ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፡ አይፈራምም ፡
በጸላቶቹ ፡ እስኪያይ ፡ ድረስ ፡፡
፱፡ በተነ፡ለችጋረኞችም፡ሰጠ፡፡ጽድቁ፡ለዘላለም፡ይኖራል፡፡
ቀንደም ፡ በክብር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፡፡
፲፡ ኃጢአተኛም ፡ አይቶ ፡ ይቈጣል ፡፡
ጥርሱንም ፡ ይፈጨል ፡ ይቀልጣልም ፡፡
የኃጢአተኛ ፡ ፈቃድ ፡ ትጠፋለች ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፲፫፡

፩፡ ሀሌሉያ ፡፡ አመስግኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ፡ ሆይ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ አመስግኑ ፡፡
፪፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡፡
፫፡ ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያው ፡ ድረስ ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይመስገን ፡፡
፬፡ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፡፡
ምስጋናውም ፡ በሰማዮች ፡ ላይ ፡፡

፭፡ ማነው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ አምላካችን ፡
በላይ ፡ የሚኖር ፡
፮፡ በታችም ፡ ያለውን ፡ የሚያይ ፡ በሰማይም ፡ በምድርም ።
፯፡ ችጋረኛን ፡ ከመሬት ፡ የሚያነሣ ።
ምስኪንንም ፡ ከፋንድያ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የሚያደርገው ።
፰፡ ካለቆች ፡ ጋራ ፡ ሊያስቀምጠው ። ከሕዝቡ ፡ አለቆች ፡ ጋራ ።
፱፡ መካኒቱን ፡ በቤት ፡ የሚያኖር ።
የልጆች ፡ እናት ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ በደስታ ። ሀሌሉያ ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፻፲፬፡

፩፡ እሥራኤል ፡ ከምስር ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ።
የያዕቆብ ፡ ቤትም ፡ ከንግደ ፡ ሕዝብ ።
፪፡ ይሁዳ ፡ መቅደሱ ፡ ነበረ ፡
እሥራኤልም ፡ ግዛቱ ።
፫፡ ባሕር ፡ አየው ፡ ሸሸም ።
ዮርዳኖስ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመለሰ ።
፬፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ደንግሌ ፡ ዘለሉ ፡
ኮረፍቶችም ፡ እንደ ፡ በግ ፡ ጥቦቶች ።
፭፡ ምን ፡ ሆንሽ ፡ አንች ፡ ባሕር ፡ የሸሸሽ ።
አንተስ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ የተመለስኽ ።
፮፡ እላንት ፡ ተራሮችስ ፡ ለምን ፡ እንደ ፡ ደንግሌ ፡ ዘለላችሁ ፡
ኮረፍቶችስ ፡ እንደ ፡ በግ ፡ ጥቦቶች ።
፯፡ ከጌታው ፡ ፊት ፡ ምድር ፡ ሆይ ፡ ትናወጫ ።
ከያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ፊት ።
፰፡ አምባውን ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ መቆምያ ፡ የለወጠ ።
ጭንጫውንም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ጉድጓድ ።

### መዝሙር ፡ ፻፲፭፡

፩፡ ለኛ ፡ አይደለም ፡ አቤቱ ፡ ለኛ ፡ አይደለም ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ለስምኽ ፡ ምስጋና ፡ ስጥ ።
ስለ ፡ ምሕረትኽ ፡ ስለ ፡ እውነትኽም ።



፪፡ አሕዛብ ፡ ለምንድር ፡ አምላካቸው ፡ የታለ ፡ ሊበሉን ።
፫፡ አምላካችንስ ፡ በሰማይ ፡ ነው ።
የወደደውንም ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።
፬፡ ጣዖታታቸው ፡ ወርቅ ፡ ብርም ፡ ናቸው ፡
የሰው ፡ እጅም ፡ ስራ ።
፭፡ አፍ ፡ አላቸው ፡ አይናገሩምም ።
ዓይን ፡ አላቸው ፡ አያዩምም ።
፮፡ ጆሮ ፡ አላቸው ፡ አይሰሙምም ።
አፍንጫ ፡ አላቸው ፡ አያሸቱምም ።
፯፡ እጅ ፡ አላቸው ፡ አይዳሰሱምም ።
እግር ፡ አላቸው ፡ አይሔዱምም ።
በጉሮሮቸውም ፡ አይናገሩም ።
፰፡ የሚያደርጓቸውም ፡ እንደርሳቸው ፡ ይሆናሉ ፡
የሚያምንባቸውም ፡ ሁሉ ።
፱፡ እሥራኤል ፡ ሆይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመን ።
ረዳታቸውና ፡ ጋሻቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፲፡ የሐሮን ፡ ቤትም ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመኑ ።
ረዳታቸውና ፡ ጋሻቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፲፩፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመኑ ።
ረዳታቸውና ፡ ጋሻቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ አሰበነ ። እርሱ ፡ ይባርከናል ።
የእሥራኤልን ፡ ወገን ፡ ይባርካል ፡
የሐሮንን ፡ ወገን ፡ ይባርካል ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ የሚፈሩትን ፡ ሁሉ ፡ ይባርካል ፡
ታናሾችን ፡ ከታላቆች ፡ ጋራ ።
፲፬፡ እግዚአብሔር ፡ በላያችሁ ፡ ይጨምር ፡
በላያችሁ ፡ በልጆቻችሁም ፡ ላይ ።
፲፭፡ እላንት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተባረካችሁ ፡ ሰማይንና ፡ ምድ
ርን ፡ ለፈጠረ ።
፲፮፡ የሰማዮች ፡ ሰማይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ።
ምድርንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ሰጣት ።
፲፯፡ የሞቱስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ አይበሉለትም ።

ወደ ፡ ዝምታም ፡ የሚወርዱ ፡ ሁሉ ።
፲፰፡ እኛ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንባርካለን ።
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙም ። ሀሌሉያ ።

---

## ህያ ፡ አራተኛ ፡ ቀን ።

## የጽዋት ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፻፲፮፡

፩፡ እግዚአብሔር ፡ የልቅሶዬን ፡ ቃል ፡
ሰምትዋልና ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፪፡ ጆሮውን ፡ ወደኔ ፡ ጥልዋልና ።
በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ እጸራዋለሁ ።
፫፡ የሞት ፡ ማሠርያ ፡ ይዞኛለችና ።
የሢኦልም ፡ ጭንቀት ፡ አገኙኝ ።
ጭንቀትም ፡ መከራም ፡ አገኘሁ ።
፬፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ ጸራሁ ፡
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ አድን ፡ ብዬ ።
፭፡ እግዚአብሔር ፡ መሓሪና ፡ ጻድቅ ፡ ነው ።
አምላካችንም ፡ ይምራል ።
፮፡ እግዚአብሔር ፡ የዋሃንን ፡ ይጠብቃል ።
ተቸገርሁ ፡ እኔንም ፡ ያድናል ።
፯፡ ወደረፍትሽ ፡ ተመለሺ ፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፡
እግዚአብሔር ፡ መልካም ፡ አድርጎልሻልና ።
፰፡ ነፍሴን ፡ ከሞት ፡ አድኖኻልና ።
ዓይኔንም ፡ ከንብ ። እግሬንም ፡ ከመሰናከል ።
፱፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እሔደለሁ ፡ በሕያዋን ፡ አገር ።
፲፡ አመንሁ፡ስለዚያም፡ተናገርሁ ።እኔም፡እጅግ፡ደከምሁ።
፲፩፡ እኔ ፡ በመደነቄ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ አሰተኛ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፲፪፡ ምን ፡ እመልሳለሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ባደረገልኝ ፡ ሁ
ሉ ፡ ፈንታ ።
፲፫፡ የመድኃኒትን ፡ ጽዋ ፡ እወስደለሁ ።
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጸራለሁ ።



፲፬፡ ስለቴን፡ለእግዚአብሔር፡በሕዝቡ፡ሁሉ፡ፊት፡እፈጽማለሁ።
፲፭፡ የቅዱሳኑ ፡ ሞት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የከበረ ፡ ነው ።
፲፮፡ አቤቱ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ ባርያኽ ፡ ነኝ ።
ባርያኽ ፡ ነኝ ፡ የሴት ፡ ባርያኽ ፡ ልጅም ። እስራቴን ፡ ፈታኽ ።
፲፯፡ ላንተ ፡ የምስጋና ፡ መሥዋዕት ፡ እሠዋለሁ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጸራለሁ ።
፲፰፡ ስለቴን፡ለእግዚአብሔር፡በሕዝቡ፡ሁሉ፡ፊት፡እፈጽማለሁ።
፲፱፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ስፍራ ።
በማኽልሽ ፡ የሩሳሌም ፡ ሆይ ። ሀሌሉያ ።

### መዝሙር ፡ ፻፲፯፡

፩፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ።
ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ አመስግኑት ።
፪፡ ምሕረቱ ፡ ወደኛ ፡ በርትታለችና ።
የእግዚአብሔርም፡እውነት፡ለዘላለም፡ትኖራለች፡ሀሌሉያ።

### መዝሙር ፡ ፻፲፰፡

፩፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ።
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።
፪፡ ይንገር ፡ እሥራኤል ፡ ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ።
፫፡ ይንገሩ ፡ የሐሮን ፡ ወገን ፡
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ።
፬፡ ይንገሩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ።
፭፡ በተጨነቅሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጸራሁ ።
እግዚአብሔርም ፡ መለሰልኝ ፡ አሰፋልኝም ።
፮፡ እግዚአብሔር ፡ ለኔ ፡ ነውና ። አልፈራም ፡
ሰው ፡ ምን ፡ ያደርግብኛል ።
፯፡ እግዚአብሔር ፡ በሚረዱኝ ፡ ለኔ ፡ ነው ፡
እኔም ፡ በጸላቶቼ ፡ አያለሁ ።
፰፡ በእግዚአብሔር፡መታመን፡በሰው፡ከመታመን፡ይሻላል።
፱፡ በእግዚአብሔር፡መታመን፡በገዦች፡ከመታመን፡ይሻላል።

፲፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከበቡኝ ። በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ እ
ቈርጣቸዋለሁ ።
፲፩፡ በጣም ፡ ከበቡኝ ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ እቈርጣቸዋለሁ ።
፲፪፡ እንደ ፡ ንብም ፡ ከበቡኝ ።
ጠፉ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ በሾኽ ፡ ማኽል ።
በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ እቈርጣቸዋለሁ ።
፲፫፡ ታስወድቀኝ ፡ ዘንድ ፡ ብለኽ ፡ ደፋህኝ ፡
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ደረደኘል ።
፲፬፡ ጕልበቴና ፡ ዝማሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
እርሱም ፡ መድኀኒቴ ፡ ደሆነልኘል ።
፲፭፡ የልልታና ፡ የመድኀኒት ፡ ድምፅ ፡ በጻድቃን ፡ ድንኳን ፡ ነው ።
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኀይልን ፡ አደረገች ።
፲፮፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ።
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኀይልን ፡ አደረገች ።
፲፯፡ አልሞትም ፡ በሕይወት ፡ እኖራለሁ ፡ እንጂ ።
የእግዚአብሔርንም ፡ ስራ ፡ እነግራለሁ ።
፲፰፡ መገሠፅ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገሠፀኝ ።
ለሞት ፡ ግን ፡ አልሰጠኝም ።
፲፱፡ የጽድቅ ፡ ደጆችን ፡ ክፈቱልኝ ፡
ወደርሳቸው ፡ ገብቼ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግን ፡ ዘንድ ።
፳፡ ይኽ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ነው ። ጻድቃን ፡ ይገቡበታል ።
፳፩፡ አመሰግንኻለሁ ፡ መለስህልኘለና ፡
መድኀኒትም ፡ ሁንኽልኘልና ።
፳፪፡ አናጾች ፡ የናቁት ፡ ደንጊያ ፡
እርሱ ፡ የማዝን ፡ ራስ ፡ ሆነ ።
፳፫፡ ይኽች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሆነች ።
ይኽችም ፡ ባይናችን ፡ ድንቅ ፡ ናት ።
፳፬፡ እግዚአብሔር ፡ የሰራው ፡ ቀን ፡ ይኽ ፡ ነው ።
በርሱ ፡ ሐሤትም ፡ እናድርግ ፡ ደስ ፡ ይበለን ።
፳፭፡ አድነነ ፡ አቤቱ ፡ እለምንኻለሁ ።
አቤቱ ፡ አቅናናልን ።



፳፮፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚመጻ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ።
ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መረቅናችሁ ።
፳፯፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እርሱም ፡ አበራልን ።
በዓልን ፡ አድርጉ ፡ ቅጠልን ፡ አሥራችሁ ፡
እስከ ፡ መሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ድረስ ።
፳፰፡ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ፡ አመሰግንኽማለሁ ።
አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግኻለሁ ።
፳፱፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ።
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፱፡

ℵ አሌፍ ።

፩፡ በመንገዳቸው ፡ የቀኑ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ።
በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ የሚሔዱ ።
፪፡ ምስክሩን ፡ የሚጠብቁ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ።
በፈጹም ፡ ልባቸው ፡ የሚሹት ።
፫፡ መታላለፍንምም ፡ አያደርጉም ። በመንገዱም ፡ ይሔዳሉ ።
፬፡ አንተ ፡ ትእዛዛትኽን ፡ እጅግ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ አዘዝኽ ።
፭፡ መንገዴ ፡ ቀንቶ ፡ ቢሆን ፡ ሕጋጋትህን ፡ ለመጠበቅ ፡
እጅግ ፡ ብወደው ፡ ነበርሁ ።
፮፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አላፈርም ፡
ሕግኽን ፡ ሁሉ ፡ ስመለከት ፡ ጊዜ ።
፯፡ በቅን ፡ ልብ ፡ አመሰግንኻለሁ ። የጽድቅኽን ፡ ፍርድ ፡
ስማር ፡ ጊዜ ።
፰፡ ትእዛዝኽን ፡ እጠብቃለሁ ። በጣም ፡ አጣለኝ ።

ב ቤት ።

፱፡ ጕልማሳ ፡ በምን ፡ መንገዱን ፡ ያነጻል ።
ነፍሱን ፡ እንደ ፡ ቃልኽ ፡ በመጠበቅ ።
፲፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ እሻሁኽ ።
ከትእዛዛትኽ ፡ እስት ፡ ዘንድ ፡ አተወኝ ።
፲፩፡ ነገርኽን ፡ በልቤ ፡ ሰወርሁ ። አንተን ፡ እንዳልበድል ።

፲፪ አንተ ፡ የተባረክኽ ፡ ነኽ ፡ አቤቱ ።
ሕግኽን ፡ አስተምረኝ ።
፲፫ ያፍኽን ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ በከንፈሬ ፡ ነገርሁ ።
፲፬ በምስክርኽ ፡ መንገድ ፡ ደስ ፡ አለኝ ፡
እንደ ፡ በሁሉ ፡ ባለጠግነት ።
፲፭ በትእዛዝኽ ፡ አስባለሁ ። መንገድኽንም ፡ እይዛተለሁ ።
፲፮ በትእዛዛኽ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ። ቃልኽን ፡ አልረሳም ።

## ג ጋሜል ።

፲፯ ለባርያኽ ፡ ምሕረት ፡ አድርግ ። ሕያው ፡ እንድሆን ፡
ነገርኽንም ፡ እንድጠብቅ ።
፲፰ ዓይኔን ፡ ክፈት ፡ የሕግኽን ፡ ታአምራት ፡ አይ ፡ ዘንድ ።
፲፱ እኔ ፡ በምድር ፡ እንግዳ ፡ ነኝ ።
ትእዛዛትኽን ፡ ከኔ ፡ አትሰውር ።
፳ ፍርድህን ፡ ወትሮ ፡ ለመናፈቅ ፡ ነፍሴ ፡ አለቀች ።
፳፩ ዕቡያንና ፡ ርጉማንን ፡ ዘለፍኽ ፡ ከትእዛዛትኽ ፡ የሳቱትን ፡
፳፪ ስድብንና ፡ ነውርን ፡ ከኔ ፡ አስወግድ ፡
ምስክርኽን ፡ ጠብቅያለሁና ።
፳፫ አለቆችም ፡ ተቀምጠው ፡ በኔ ፡ ተጫወቱ ።
ባርያኽ ፡ ግን ፡ በሕግኽ ፡ ያስብ ፡ ነበረ ።
፳፬ ምስክሮችህ ፡ ደስታዬ ፡ ናቸውና ፡ መካሮቼም ።

## ד ደሌጥ ።

፳፭ ነፍሴ ፡ ላፈር ፡ ትጣብቃለች ። አድነኝ ፡ እንደ ፡ ነገርኽ ።
፳፮ መንገዴን ፡ ነገርሁ ፡ መለስኽለኝም ።
ሕግኽን ፡ አስተምረኝ ።
፳፯ የትእዛዛትኽን ፡ መንገድ ፡ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡
በድንቅኽም ፡ አስባለሁ ።
፳፰ ነፍሴ ፡ ካዘን ፡ አልቃለች ። እንደ ፡ ነገርኽ ፡ አጽናኝ ።
፳፱ ያሰትን ፡ መንገድ ፡ ከኔ ፡ አርቅ ፡ በምሕረትኽም ፡ ሕግኽን ፡
ስጠኝ ።
፴ የውነትን ፡ መንገድ ፡ መረጽሁ ። ፍርድኽንም ፡ በፊቴ ፡
አኖርሁ ።



፴፩ ለምስክሮችህ ፡ ተጣበቅሁ ።
አቤቱ ፡ አታሳፍረኝ ።
፴፪ በትእዛዛትኽ ፡ መንገድ ፡ እሮጻለሁ ። ልቤን ፡ ስታሰፋ ፡ ጊዜ ።

## ህያ ፡ አምስተኛ ፡ ቀን ።

## የጽዋት ፡ ጸሎት ፡

## ה ሄ ።

፴፫ የሕግኽን ፡ መንገድ ፡ አስተምረኝ ፡ አቤቱ ፡
ለመጨረሻም ፡ እጠብቀዋለሁ ።
፴፬ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ሕግኽንም ፡ እመለከታለሁ ፡
በፍጹም ፡ ልቤም ፡ እጠብቃታለሁ ።
፴፭ የትእዛዛትኽ ፡ መንገድ ፡ ምራኝ ፡
እርስዋን ፡ ወድጃለሁና ።
፴፮ ልቤን ፡ ወደ ፡ ምስክርኽ ፡ መልስ ፡
ወደ ፡ ስስትም ፡ አይደለም ።
፴፯ ዓይኖቼን ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ከማየት ፡ አርቅ ፡
በመንገድኽመ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፴፰ ለባርያኽ ፡ ነገርኽን ፡ አጽና ፡ ለፍርሃትኽ ፡ ያለውን ።
፴፱ የጸላሁትን ፡ ስድብ ፡ ከኔ ፡ አርቅ ፡
ፍርድኽ ፡ መልካም ፡ ናትና ።
፵ እነሆ ፡ ትእዛዝኽን ፡ ተናፈቅሁ ።
በጽድቅኽም ፡ ሕይወት ፡ ስጠኝ ።

## ו ዋው ።

፵፩ አቤቱ ፡ ምሕረትኽ ፡ ትምጻልኝ ፡
መድኃኒትኽም ፡ እንደ ፡ ነገርኽ ።
፵፪ የሚሰድበኝንም ፡ በነገር ፡ እምልስለታለሁ ፡
በቃላኽ ፡ ታምኛለሁና ።
፵፫ የውነትንም ፡ ነገር ፡ ካፌ ፡ ፈጽመኽ ፡ አታርቅ ፡
ለፍርድኽ ፡ ደጅ ፡ ጸንቻለሁና ።
፵፬ ሕግኽንም ፡ በጊዜው ፡ ሁሉ ፡ እጠብቃለሁ ፡
ለዘላለሙ ፡ ለፍጻሜውም ።

፵፭ አስፋቴም ፡ እሔደለሁ ፡ ትእዛዛትኽን ፡ ሸቻለሁና ።
፵፮ በምስክርኽም ፡ በነገሥታት ፡ ፊት ፡
እናገራለሁ ፡ አላፍርምም ።
፵፯ እጅግም ፡ በወደድኋቸው ፡ በትእዛዛትኽ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፵፰ እጄንም፡ወደ፡ወደድኋቸው፡ወደ፡ትእዛዛትኽ፡አነሣለሁ።
በሕግኽም ፡ አስባለሁ ።

ז ዛይ ።

፵፱ ቃልኽን ፡ አስብ ፡ ለባርያኽ ፡ ተስፋ ፡ ያስደረግኸኝን ።
፶ ይኽች ፡ ደስታዬ ፡ ሆነች ፡ በመከራዬ ። ቃልኽ ፡ አድኖኛልና ።
፶፩ ዕቡያን ፡ ፈጽመው ፡ ተላገዱኝ ።
እኔ ፡ ግን ፡ ከሕግኽ ፡ አልዘነበልሁም ።
፶፪ ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ የነበረውን ፡ ፍርድኽን ፡ አሰብሁ ፡
አቤቱ ፡ ተጸናናሁም ።
፶፫ ግርማ ፡ ያዘኝ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሕግኽን ፡ ስለ ፡ ተዉ ።
፶፬ ፍርድኽ ፡ ዝማሬ ፡ ሆነችኝ ፡ በንግድነቴ ፡ ቤት ።
፶፭ በሌት ፡ ስምኽን ፡ አሰብሁ ፡ አቤቱ ፡ ሕግኽንም ፡ ጠበቅሁ ።
፶፮ ይህችም ፡ ሆነችልኝ ፡ ትእዛዛትኽን ፡ ጠብቂያለሁና ።

ח ሔት ።

፶፯ አቤቱ ፡ ነገርህን ፡ ለመጠበቅ ፡ ፈንታዬ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፶፰ ወደ ፡ ፊትኽ ፡ ተማለልሁ ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ።
እንደ ፡ ነገር ኽ ፡ ማረኝ ።
፶፱ በመንገዴ ፡ አሰብሁ ፡
እግሬንም ፡ ወደ ፡ ምስክሮችኽ ፡ መለስሁ ።
፷ ጨከንሁ ፡ አልዘገይሁምም ፡ ትእዛዝኽን ፡ ለመጠበቅ ።
፷፩ የኃጥኣን ፡ ገመዶች ፡ ከበቡኝ ።
ሕግኽን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
፷፪ በኩል ፡ ሌት ፡ አመሰግንኽ ፡ ዘንድ ፡ እነሣለሁ ።
ስለ ፡ ጽድቅኽ ፡ ፍርድ ።
፷፫ እኔ ፡ ለሚፈሩኽ ፡ ሁሉ ፡ ባልንጀራ ፡ ነኝ ።
ትእዛዛትኽንም ፡ ለሚጠብቁ ።
፷፬ ምህረትኽ ፡ በምድር ፡ መላች ፡ አቤቱ ።
ሕጋጋትኽን ፡ አስተምረኝ ።



ט ጤት ።

፷፭ ከባርያኽ፡ጋራ፡መልካም፡ሰራኽ፡አቤቱ፡እንደ፡ቃልኽ።
፷፮ መልካምን ፡ እሉንታና ፡ እውቀት ፡ አስተምረኝ ።
በትእዛዛትኽ ፡ አምኛለሁና ።
፷፯ እኔ ፡ ሳልዋረድ ፡ ተገደፍሁ ። አሁን ፡ ግን ፡ ነገርኽን ፡ ጠበቅሁ ።
፷፰ አንተ ፡ ቸር ፡ ነኽ ፡ አቤቱ ፡ ቸርነትንም ፡ የምታደርግ ።
ሕጋጋትኽን ፡ አስተምረኝ ።
፷፱ ዕቡያን ፡ በላዬ ፡ አሰትን ፡ ጣሉብኝ ።
እኔ ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ትእዛዝኽን ፡ ጠበቅሁ ።
፸ ልባቸው ፡ እንደ ፡ ቅቤ ፡ ሰባ ። እኔ ፡ ግን ፡ በሕግኽ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።
፸፩ የቸገረኝ ፡ ደህና ፡ ነበረልኝ ፡
ሕጋጋትኽን ፡ ተምሬበታለሁና ።
፸፪ ያፍኽ ፡ ሕግ ፡ ይሻለኛል ፡ ከወርቅና ፡ ከብር ፡ አእላፋት ።

የማታ ፡ ጸሎት ።

י ዮድ ።

፸፫ እጆችኽ ፡ አደረጉኝና ፡ አዘጋጁኝ ።
እንደስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ትእዛዛትኽንም ፡ እማራለሁ ።
፸፬ የሚፈሩኽ ፡ አይተውኝ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡
ለነገርኽ ፡ ቈይቻለሁና ።
፸፭ አቤቱ ፡ ፍርድኽ ፡ ጽድቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አወቅሁ ።
በምነትኽምም ፡ አዋረድኸኝ ።
፸፮ ምሕረትኽ ፡ ለመጽናናቴ ፡ ትሁንልኝ ፡
እንደ ፡ ነገርኽ ፡ ለባርያኽ ።
፸፯ ምህረትኽ ፡ ትምጻልኝ ፡ ሕያውም ፡ እሆናለሁ ።
ሕግኽ ፡ ደስታዬ ፡ ናትና ።
፸፰ ዕቡያን ፡ ይፈሩ ፡ በአሰት ፡ ጠመውብኛልና ።
እኔ ፡ ግን ፡ በትእዛዝኽ ፡ እጫወታለሁ ።
፸፱ ወደኔ ፡ ይመለሱ ፡ የሚፈሩኽ ፡
ምስክርኽንም ፡ የሚያውቁ ።
፹ ልቤ ፡ በሕጋጋትኽ ፡ ቀንቶ ፡ ይሁን ፡ እንዳላፍር ።

ነ ካፍ ፡፡

፹፩፡ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ መድኀኒትኽ ፡ ናፈቀች ፡፡
ለነገርኽም ፡ ደጅ ፡ ጸናሁ ፡፡
፹፪፡ ደከሙ ፡ ዓይኖቼ ፡ ወደ ፡ ቃልኽ ፡
መቼ ፡ ታጸናናኛለኽ ፡ ኢያሉ ፡፡
፹፫፡ በጢስ ፡ እንደለ ፡ አቁማዳ ፡ ሁኛለሁና ፡፡
ሕግኽን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ፡፡
፹፬፡ የባሪያኽ ፡ ዘመን ፡ ስንት ፡ ናት ፡፡
መቼስ ፡ በሚያሳድዱኝ ፡ ትፈርድልኛለኽ ፡፡
፹፭፡ ዐቡያን፡ጕድጓድን፡ቈፈሩልኝ፡፡እንደ፡ሕግኽም፡ያደደለ፡፡
፹፮፡ ትእዛዛትኽ ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ናቸው ፡፡
ባሰት ፡ አሳደዱኝ ፡ እርዳኝም ፡፡
፹፯፡ እንደሁ ፡ ለጥቂት ፡ በምድር ፡ ያጠፉኝ ፡ ነበሩ ፡፡
እኔ ፡ ግን ፡ ትእዛዛትኽን ፡ አልተውሁም ፡፡
፹፰፡ እንደ ፡ ምሕረትኽ ፡ አድነኝ ፡
ያፍኽንም ፡ ምስክር ፡ እጠብቃለሁ ፡፡

ለ ላሜድ ፡፡

፹፱፡ አቤቱ ፡ ቃልኽ ፡ ለዘላለም ፡ በሰማይ ፡ ይኖራል ፡፡
፺፡ ጽድቅኽ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ናት ፡፡
ምድርን ፡ መሠረትኻት ፡ እርስዋም ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች ፡፡
፺፩፡ እስከ ፡ ዛሬም ፡ በሥርዓትኽ ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉ ፡፡
ሁላቸው ፡ ባሮችህ ፡ ናቸውና ፡፡
፺፪፡ ሕግኽስ፡ደስታዬ፡ባይሆን፡ድሮ፡በጕስቍልናዬ፡በጠፋሁ፡፡
፺፫፡ ለዘላለም ፡ ፍርድኽን ፡ አልረሳም ፡፡
በርሱ ፡ አድነኸኛልና ፡፡
፺፬፡ እኔ ፡ ያንተ ፡ ነኝ ፡ አድነኝ ፡ ፍርድኽን ፡ ሸቻለሁና ፡፡
፺፭፡ እኔን ፡ ለማጥፋት ፡ ኃጥአን ፡ ቈዩልኝ ፡፡
ምስክርኽን ፡ አስተውያለሁ ፡፡
፺፮፡ የስራን ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ አየሁ ፡፡
ትእዛዝኽ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ ነው ፡፡



መ ሜም ፡፡

፺፯፡ ሕግኽን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እጅግ ፡ ወደድሁ ፡፡
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ አሳቤ ፡ ነው ፡፡
፺፰፡ በትእዛዝኽ ፡ ከጸላቶቼ ፡ ይልቅ ፡ ጠቢብ ፡ አደረግኸኝ ፡፡
ለዘላለም ፡ ለኔ ፡ ነውና ፡፡
፺፱፡ ካስተማሩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ፡፡
ምስክርኽ ፡ አሳቤ ፡ ነውና ፡፡
፻፡ ከሽማግሎች ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ፡፡
ትእዛዝኽን ፡ እጠብቃለሁና ፡፡
፻፩፡ ከክፉ ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ እግሬን ፡ ከለከልሁ ፡፡
ነገርኽን ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡፡
፻፪፡ ከፍርድኽ ፡ አልራቅሁም ፡፡ አንተ ፡ አስተምረኸኛልና ፡፡
፻፫፡ ነገርኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ላንደበቴ ፡ ደጻፍጣል ፡፡
ከማር ፡ ይልቅ ፡ ላፌ ፡ ጣፈጠኝ ፡፡
፻፬፡ በትእዛዝኽ ፡ ብልህ ፡ ሆንሁ ፡፡
ስለዚኽ ፡ ያሰትን ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ጸላሁ ፡፡

ህያ ፡ ስድስተኛ ፡ ቀን ፡፡

የጽዋት ፡ ጸሎት ፡፡

ነ ኑን ፡፡

፻፭፡ ሕግኽ ፡ ለግሬ ፡ መብራት ፡ ነው ፡፡ ለመንገዴም ፡ ብርሃን ፡፡
፻፮፡ ማልሁ ፡ አጸናዋለሁም ፡ የጽድቅህን ፡ ፍርድ ፡ እጠብቅ ፡
ዘንድ ፡፡
፻፯፡ እጅግ ፡ መከራ ፡ ተቀበልሁ ፡፡
እንደ ፡ ነገርኽ ፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ፡፡
፻፰፡ ካፌ ፡ የሚወጣውን ፡ የፈቃዴን ፡ መሥዋዕት ፡
በሞገስ ፡ ተቀበለው ፡ አቤቱ ፡፡
ፍርድኽንም ፡ አስተምረኝ ፡፡
፻፱፡ ነፍሴ ፡ በጇ ፡ ናት ፡ ሁለግዜ ፡ ሕግኽን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ፡፡
፻፲፡ ኃጢአተኞች ፡ ወጽመድ ፡ ዘረጉብኝ ፡፡
ከትእዛዝኽም ፡ አልተገደፍሁም ፡፡

፻፲፩፡ ምስክርኽን ፡ ለዘላላም ፡ ወረስሁ ፡፡ የልቤ ፡ ደስታ ፡ ናትና ፡፡
፻፲፪፡ ልቤን ፡ መለስሁ ፡ ትእዛዝኽን ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡
ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ፡፡

ፀ ሳሜክ ፡፡

፻፲፫፡ ወስላቶችን ፡ ጸላሁ ፡፡ ሕግኽን ፡ ግን ፡ ወደድሁ ፡፡
፻፲፬፡ መሰወርያዬና ፡ ጋሻዬ ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡፡
ቃልህንም ፡ ተሰፋ ፡ አደረግሁ ፡፡
፻፲፭፡ ከኔ ፡ ራቁ ፡ እላንት ፡ በደለኞች ፡፡
ያምላኬን ፡ ትእዛዛት ፡ ልጠብቅ ፡፡
፻፲፮፡ እንደ ፡ ነገርኽ ፡ ደግፈኝ ፡ ልደንም ፡፡
ካለኝታዬም ፡ አታሳፍረኝ ፡፡
፻፲፯፡ መሠርተኝ፡እድናለሁም፡፡ወደ፡ሕግኽም፡ሁለግዜ፡አያለሁ፡፡
፻፲፰፡ ከፍርድኽ ፡ የሚርቁን ፡ ሁሉ ፡ ረገጥኽ ፡፡
ተንኰላቸው ፡ አሰት ፡ ነውና ፡፡
፻፲፱፡ የምድር ፡ ኃጢአተኞችን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ርኵሰት ፡ አጠ
ፈኻቸው ፡፡
ስለዚኽ ፡ ምስክርኽን ፡ ወደድሁ ፡፡
፻፳፡ ሥጋዬ ፡ ከፍርሃትኽ ፡ ደነገፀ ፡፡ ከፍርድኽም ፡ ፈርቻለሁ ፡፡

ሃ ዓይን ፡፡

፻፳፩፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ ሰራሁ ፡፡
መከራ ፡ ለሚያመጹብኝ ፡ አሳልፈኽ ፡ አትስጠኝ ፡፡
፻፳፪፡ ባርያኽን ፡ በመልካም ፡ ተዋሰው ፡፡ ዕቡያን ፡ እንዳይጋፉኝ ፡፡
፻፳፫፡ ዓይኖቼ ፡ ወደ ፡ ማደንኽ ፡ ኢያዩ ፡ ደከሙ ፡
ወደ ፡ ጽድቅኽም ፡ ነገር ፡፡
፻፳፬፡ ከባርያኽ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ምሕረትኽ ፡ አድርግ ፡፡
ሕግኽንም ፡ አስተምረኝ ፡፡
፻፳፭፡ እኔ ፡ ባርያኽ ፡ ነኝ ፡፡ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡
ምስክርኽንም ፡ አውቃለሁ ፡፡
፻፳፮፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያደርግበት ፡ ጊዜ ፡ አለው ፡፡ ሕግኽን ፡
ሽረዋልና ፡፡
፻፳፯፡ ስለዚኽ ፡ ትእዛዛትኽን ፡ ወደድሁ ፡፡



ከወርቅ ፡ ከጽሩም ፡ ወርቅ ፡ ይልቅ ፡፡
፻፳፰፡ ስለዚኽ ፡ በትእዛዝኽ ፡ ሁሉ ፡ ነገርን ፡ ሁሉን ፡ አቀናሁ ፡፡
ያሰትንም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ጸላሁ ፡፡

ፀ ፌ ፡፡

፻፳፱፡ ምስክሮችኽ ፡ ድንቅ ፡ ናቸው ፡፡
ስለዚኽ ፡ ነፍሴ ፡ ትጠብቃቸዋለች ፡፡
፻፴፡ የቃልህ ፡ መፍታት ፡ ያበራል ፡፡
የዋሃንንም ፡ አዋቆች ፡ ያደርጋል ፡፡
፻፴፩፡ አፌን ፡ ከፈትሁ ፡ ሲጥም ፡ አልሁ ፡፡
ወደ ፡ ትእዛዝኽ ፡ ናፍቅያለሁና ፡፡
፻፴፪፡ ወደኔ ፡ ተመልከት ፡ ማረኝም ፡
ስምኽን ፡ ለሚወዱ ፡ እንድትፈርድላቸው ፡፡
፻፴፫፡ አረጋገጤን ፡ እንደ ፡ ነገርኽ ፡ አቅና ፡፡
ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አይግዛኝ ፡፡
፻፴፬፡ ከሰው ፡ ግፍ ፡ አድነኝ ፡፡ ትእዛዝኽንም ፡ እጠብቃለሁ ፡፡
፻፴፭፡ ፊትኽን፡አብራ፡በባርያኽ፡ላይ፡፡ሕግኽንም፡አስተምረኝ፡፡
፻፴፮፡ የውኃ ፡ ፈሻሽ ፡ ካይኔ ፡ ፈሰሰ ፡፡ ሕግኽን ፡ አልጠበቁምና ፡፡

ሄ ጻዴ ፡፡

፻፴፯፡ አንተ ፡ ጻድቅ ፡ ነኽ ፡ አቤቱ ፡፡ ፍርድኽም ፡ የቀና ፡ ነው ፡፡
፻፴፰፡ ያዘዝኻት ፡ ምስክር ፡ ጽድቅ ፡ በጣምም ፡ እውነት ፡ ናት ፡፡
፻፴፱፡ ቅንዓቴ ፡ አጠፋችኝ ፡ ጸላቶቼ ፡ ቃልኽን ፡ ረስተዋልና ፡፡
፻፵፡ ቃልኽ ፡ እጅግ ፡ የጸራ ፡ ነው ፡፡ ባርያኽም ፡ ወደደው ፡፡
፻፵፩፡ ታናሽ ፡ ነኝ ፡ የተናቅሁም ፡ ነኝ ፡፡
ሕግኽን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ፡፡
፻፵፪፡ ጽድቅኽ ፡ ለዘላለም ፡ ጽድቅ ፡ ናት ፡፡
ሕግኽም ፡ እውነት ፡ ናት ፡፡
፻፵፫፡ መከራና ፡ ችጋር ፡ አገኙኝ ፡፡
ትእዛዛትኽ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ አሰኙኝ ፡፡
፻፵፬፡ የምስክርኽ ፡ ጽድቅ ፡ ለዘላለም ፡ ናት ፡፡
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ እድናለሁም ፡፡

የማታ : ጸሎት ::

ק ቆፍ ::

፻፵፭፡ በፍጹም : ልቤ : ጮኽሁ ::
መልስልኝ : አቤቱ : ፍርድኽን : እጠብቃለሁ ::
፻፵፮፡ ወደንተ : ጮኽሁ :: አድነኝ ::
ምስክርኽንም : እጠብቃለሁ ::
፻፵፯፡ ከጽዋት : በፊት : ቀድሜ : እጮኻለሁ ::
ቃልህንም : ተስፋ : አደርጋለሁ ::
፻፵፰፡ ዓይኖቼ : የሌት : ትጋቶችን : ቀደሙ :
ነገርኽን : ያስቡ : ዘንድ ::
፻፵፱፡ ድምፄን : ስማ : እንደ : ምሕረትኽ : አቤቱ ::
እንደ : ፍርድኽም : አድነኝ ::
፻፶:: ኃጢአትን : የሚከተሉ : ቀረቡ : ከሕግኽ : ግን : ራቁ ::
፻፶፩፡ አንተ : ቅርብ : ነኽ : አቤቱ ::
ትእዛዛትኽም : ሁሉ : እውነት : ናቸው ::
፻፶፪፡ ምስክርኽን : ከድሮ : አወቅሁ ::
ለዘላለም : እንደ : ሠራኻት ::

ר ሬስ ::

፻፶፫፡ መዋረዴን : ተመልከት : አድነኝም ::
ሕግኽን : አልረሳሁምና ::
፻፶፬፡ ፍርዴን : ፍረድ : አድነኝም :: እንደ : ነገርኽ : አድነኝ ::
፻፶፭፡ ድኅንነት : ከኃጥኣን : የራቀች : ናት ::
ትእዛዛትኽን : አልሹምና ::
፻፶፮፡ ምህረትኽ : እጅግ : ናት : አቤቱ ::
እንደ : ፍርድኽ : አድነኝ ::
፻፶፯፡ አሳዳጆቼና : ጸላቶቼ : ብዙ : ናቸው ::
ከምስክርኽ : ግን : አልዘነበልሁም ::
፻፶፰፡ ግብዞችን : አይቼ : አዘንሁ :: ቃልኽን : አልጠበቁምና ::
፻፶፱፡ ትእዛዛትኽን : እንደ : ወደድሁ : ተመልከት ::
በምህረትኽ : አድነኝ : አቤቱ ::
፻፷:: የነገርኽ : መጀመርያ : እውነት : ነው ::
የጽድቅኽም : ፍርድ : ሁሉ : ለዘላለም : ነው ::



ש ሢን ::

፻፷፩፡ ገዦች : በከንቱ : አሳደዱኝ ::
ከቃልኽ : ግን : የተነሣ : ልቤ : ደነገፀብኝ ::
፻፷፪፡ በነገርኽ : ደስ : ይለኛል :
ብዙ : ምርኮ : እንደገኘ : ሰው ::
፻፷፫፡ አሰትን : ጸላሁ : ተጸየፍሁም :: ሕግኽን : ግን : ወደድሁ ::
፻፷፬፡ ሰባት : ጊዜ : በቀን : አመሰገንሁኽ :: ስለ : ጽድቅኽ : ፍርድ ::
፻፷፭፡ ስምኽን : ለሚወዱ : ብዙ : ሰላም : ይሆናል ::
ዕንቅፋትም : የላቸውም ::
፻፷፮፡ ማደንኽን : ተስፋ : አደረግሁ : አቤቱ ::
ትእዛዛትኽንም : ፈጸምሁ ::
፻፷፯፡ ነፍሴ : ምስክርኽን : ጠበቀች :: እጅግም : ወደድሁት ::
፻፷፰፡ ትእዛዛትኽንና : ምስክርኽን : ጠበቅሁ ::
መንገዴ : ሁሉ : በፊትኽ : ነውና ::

ת ታው ::

፻፷፱፡ ጩኸቴ : ወደ : ፊትኽ : ትቅረብ : አቤቱ ::
እንደ : ቃልኽም : አስተውል : ዘንድ : አድርገኝ ::
፻፸:: ልመናዬ : ወደ : ፊትኽ : ትድረስ ::
እንደ : ቃልኽም : አድነኝ ::
፻፸፩፡ ከንፈሮቼ : ምስጋና : ያፈሳሉ ::
ሕጋጋትኽን : አስተምረኸኛልና ::
፻፸፪፡ መላሴ : ቃልኽን : ይናገራል ::
ትእዛዛትኽ : ሁሉ : ጽድቅ : ናቸውና ::
፻፸፫፡ እጅኽ : እኔን : ለመርዳት : ትሁን ::
ትእዛዛትኽን : መርጫለሁና ::
፻፸፬፡ አቤቱ : ወደ : ማደንኽ : ናፈቅሁ ::
ሕግኽም : ደስታዬ : ናት ::
፻፸፭፡ ነፍሴ : ትደን : ታመሰግንኽማለች ::
ፍርድኽም : ትርደኝ ::
፻፸፮፡ እንደ : ጠፋ : በግ : ሳትሁ :: ባርያኽን : እሻ :
ትእዛዛትኽን : አልረሳሁምና ::

## ህያ : ሰባተኛ : ቀን ::

## የ ጽዋት : ጸሎት ::

### መዝሙር : ፻፳፤

፩፤ ወደ : እግዚአብሔር : ጮኽሁ : በተጨነቅሁ : ጊዜ :
እርሱም : መለሰልኝ ::
፪፤ አቤቱ : ነፍሴን : ታደግ :
ካሰተኛ : ከንፈር : ከሸንጋይም : መላስ ::
፫፤ ምን : ይሰጡኻል : ምንስ : ይጨመርልኻል :
የሸንገላ : ልሳን : ሆይ ::
፬፤ የተሳሉ : የብርቱ : ፍላፆች : ከጽድ : ፍም : ጋራ ::
፭፤ ወዮልኝ : በሜሴክ : ስደተኛ : ነኝና ::
በቄደርም : ድንኳኖች : አደርሁ ::
፮፤ እጅግ : ቀን : አድራ : ሰነበተች : ነፍሴ :
ሰላም : ከሚጸላ : ጋራ ::
፯፤ እኔስ : የሰላም : ሰው : ነኝ :
ደሮ : ስናገር : ጊዜ : እርሳቸው : ለዘምቻ : ናቸው ::

### መዝሙር : ፻፳፩፤

፩፤ ወደ : ተራሮች : ዓይኔን : አነሣሁ ::
ከወዴት : ትመጻለች : ረድኤቴ ::
፪፤ ረድኤቴ : ከእግዚአብሔር : ዘንድ : ትመጣለች :
ሰማይንና : ምድርን : ከፈጠረ ::
፫፤ እግርኽን:ለመናወጥ:አይስጥ::የሚጠብቅኽም:አይተኛ::
፬፤ እነሆ : አይተኛምም : አያንቀላፋም : እሥራኤልን : የ
ሚጠብቅ ::
፭፤ እግዚአብሔር : ጠባቂኽ : ነው ::
እግዚአብሔርም : በቀኝ : እጅኽ : ለጽላኽ : ነው ::
፮፤ ፀሐይ : በቀን : አይመታኽም : ጨረቃም : በሌት ::
፯፤ እግዚአብሔር : ከክፉ : ሁሉ : ይጠብቅኻል ::
ነፍስኽን : ይጠብቃል ::
፰፤ እግዚአብሔር : መውጣትኽንና : መግባትኽን : ይጠብቃ
ል : ከዛሬ : ጀምሮ : እስከ : ዘላለም : ድረስ ::



### መዝሙር : ፻፳፪፤

፩፤ ወደ:እግዚአብሔር:ቤት:እንሒድ:ባሉኝ:ጊዜ:ደስ:አለኝ::
፪፤ እግሮቻችን:በደጆችሽ:ቁመው:ይሆናሉ:የሩሳሌም:ሆይ::
፫፤ የሩሳሌም : እርሱ : በርስዋ : እንደ : ተጋጠመች : አገር :
ተሠራች ::
፬፤ ከዚያ : ነገዶች : ይወጣሉ :
የእግዚአብሔር : ነገዶች : ለእሥራኤል : ምስክር ::
የእግዚአብሔርን : ስም : ያመሰግኑ : ዘንድ ::
፭፤ ከዚያ : ዙፋኖች : ለፍርድ : ተቀምጠዋልና ::
የዳዊት : ቤት : ዙፋኖች ::
፮፤ የየሩሳሌምን : ደኅንነት : ለምኑ ::
የሚወዱሽ : በጅ : ይላቸዋል ::
፯፤ ደኅንነት : በቅጽርሽ : ውሥጥ : ትሁን ::
ደስታም : በጌጸኛ : ቤቶችሽ ::
፰፤ ስለ : ወንድሞቼ : ስለ : ዘመዶቼም :
ደህንነት : ትሁንልሽ : እላለሁ ::
፱፤ ስለ : አምላካችን : ስለ : እግዚአብሔር : ቤት ::
ላንች : መልካም : ያለውን : ነገር : እሻለሁ ::

### መዝሙር : ፻፳፫፤

፩፤ ወደንተ : ዓይኔን : አነሣሁ : በሰመይ : የምትኖር : ሆይ ::
፪፤ እነሆ : እንደ : ባሮች : ዓይኖች : ወደ : ጌቶቻቸው : እጅ ::
እንደ : ባርያይቱም : ዓይን : ወደ : እመቤትዋ : እጅ ::
እንዲሁም : ዓይኖችን : ወደ : እግዚአብሔር : ወደ : አምላ
ካችን : ነው :
እስኪምረን : ድረስ ::
፫፤ ማረን : አቤቱ : ማረን :: እጅግ : መናቅ : ጸግበናልና ::
፬፤ ነፍሳችንም : እጅግ : የሴሰኞችን : ጨወታ : ጸግባለችና :
የዕቡያንንም : መናቅ ::

### መዝሙር : ፻፳፬፤

፩፤ እግዚአብሔር : ለኛ : ባይኖር : ዛሬ : ይበል : እሥራኤል :
፪፤ እግዚአብሔር : ለኛ : ባይኖር :

ሰው ፡ በላያችን ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡፡
፫፤ እንኪያስ ፡ በቁማችን ፡ በዋጡን ፡ ነበር ፡፡
ቍጣቸው ፡ በላያችን ፡ በነደደ ፡ ጊዜ ፡፡
፬፤ እንኪያስ ፡ ውኃ ፡ ባሰጠመን ፡ ነበር ፡፡
በነፍሳችን ፡ ላይም ፡ ወንዝ ፡ ባለፈ ፡፡
፭፤ የዕቡያን ፡ ሞገድ ፡ በነፍሳችን ፡ ላይ ፡ ባለፈች ፡፡
፮፤ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ፡ ለጥርሳቸው ፡ ጽማድ ፡ ያላደረገን ፡፡
፯፤ ነፍሳችን ፡ እንደ ፡ ዎፍ ፡ ከአዳኞች ፡ ወጥመድ ፡ አመለጠች ፡፡
ወጥመዱ ፡ ተሰበረ ፡ እኛም ፡ አመለጥን ፡፡
፰፤ ረድኤታችን ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በፈጠረ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ነው ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፳፭፤

፩፤ በእግዚአብሔር ፡ የታመኑ ፡ እንደ ፡ ፅዮን ፡ ተራራ ፡ ናቸው ፡፡
የማይታወክ ፡ ለዘላለሙም ፡ የሚኖር ፡፡
፪፤ ተራሮች ፡ በየረሳሌም ፡ ዙርያ ፡ ናቸው ፡፡
እግዚአብሔርም ፡ በሕዝቡ ፡ ዙርያ ፡ ነው ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡
ለዘላለም ፡፡
፫፤ የኃጥአን ፡ በትር ፡ በጻድቃን ፡ ጕልት ፡ ላይ ፡ አይኖርምና ፡፡
ጻድቃን ፡ እጃቸውን ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይዘርጉ ፡፡
፬፤ መልካም ፡ አድርግ ፡ አቤቱ ፡ ለቸሮች ፡ ልባቸውም ፡ ለቀና ፡፡
፭፤ ወደ ፡ ጠማምነት ፡ ግን ፡ ያሉትን ፡
እግዚአብሔር ፡ ግፍን ፡ ከሚሰሩ ፡ ጋራ ፡ ያወጣቸዋል ፡፡
ደኅንነትም ፡ በእሥራኤል ፡ ላይ ፡ ትሁን ፡፡

የማታ ፡ ጸሎት ፡፡
መዝሙር ፡ ፻፳፮፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ የፅዮንን ፡ ምርኮ ፡ ሲመልስ ፡ ጊዜ ፡
እንደሚያልሙ ፡ እንሆናለን ፡፡
፪፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሳቅ ፡ አፋችንን ፡ ይመላል ፡ መላሳችንንም ፡
እልልታ ፡፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡



እግዚአብሔር፡ከሌህ፡ጋራ፡አደራረጉን፡ታላቅ፡አደረገ፡ይላሉ፡፡
፫፤ እግዚአብሔር ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ አደራረጉን ፡ ታላቅ ፡ አደረገ ፡፡
ባለደስተኞችም ፡ ሆን ፡፡
፬፤ ምርኳችነን ፡ መልስ ፡ አቤቱ ፡ በደቡብ ፡ እንደሉ ፡ ፈሳሾች ፡፡
፭፤ ኢያለቀሱ ፡ የሚዘሩ ፡ በደስታ ፡ ያጭዳሉ ፡፡
፮፤ መሔድስ ፡ ይሔዳልና ፡ ያለቅሳል ፡
ዘሩንም ፡ ይዞ ፡ ይዘራል ፡፡
ተመልሶ ፡ ግን ፡ በደስታ ፡ ይመጻል ፡ ነዶውን ፡ ተሸክሞ ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፳፯፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ቤትን ፡ ካልሠራ ፡
ሠሮች ፡ በከንቱ ፡ ይደክሙበታል ፡፡
እግዚአብሔር ፡ አገርን ፡ ካልጠበቀ ፡
ጠባቂ ፡ በከንቱ ፡ ይተጋል ፡፡
፪፤ ከንቱ ፡ ነው ፡ መማለዳችሁ ፡
እስከ ፡ ሌትም ፡ ድረስ ፡ መቀመጣችሁ ፡
የትካዜም ፡ እንጀራ ፡ መብላታችሁ ፡፡
ለወዳጆቹ ፡ እንዲህ ፡ እንቅልፍ ፡ ይሰጣልና ፡፡
፫፤ እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡
የሆድ ፡ ፍሬም ፡ ደመወዜው ፡፡
፬፤ በብርቱ ፡ እጅ ፡ እንደሉ ፡ ፍላጾች ፡
እንዲህ ፡ የጕልማስነት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡፡
፭፤ በርሳቸው ፡ አቃውን ፡ የመላ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡፡
በደጅ ፡ ጸላቶቻቸውን ፡ በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ አያፍሩም ፡፡

መዝሙር ፡ ፻፳፰፤

፩፤ ምስጉን ፡ ነው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሁሉ ፡
በመንገዱ ፡ የሚሔድ ፡፡
፪፤ የጅህን ፡ ድካም ፡ ትበላለኽ ፡፡
ምስጉን ፡ ነኽ ፡ ደህንነትም ፡ ትሆንልሃለች ፡፡
፫፤ ምሽትኽ ፡ እንደ ፡ ፍርያም ፡ ወይን ፡ በቤትኽ ፡ አጸገብ ፡
ልጆችኽም ፡ እንደ ፡ ወይራ ፡ አታክልት ፡ በማዕድኽ ፡ ዙ
ርያ ፡ ይሆናሉ ፡፡

፬፤ እነሆ፡እግዚአብሐርን፡የሚፈራ፡ሰው፡እንደህ፡ይባረካል።
፭፤ እግዚአብሐር ፡ ከፅዮን ፡ ዘንድ ፡ ይባርክኻል ፡
የየሩሳሌምንም ፡ በጐነት ፡ ታያለኽ ፡
የሕይወትህን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ።
፮፤ የልጆችኽን ፡ ልጆችም ፡ ታያለኽ ።
ደኅንነት ፡ በእሥራኤል ፡ ላይ ፡ ትሁን ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፱፤

፩፤ ከታናሽነቴ፡ጀምሮ፡ብዙ፡ጊዜ፡ተጋፉኝ፡ይበል፡እሥራኤል።
፪፤ ከታናሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተጋፉኝ ፡
ነገር ፡ ግን ፡ አላሸነፉኝም ።
፫፤ አራሾች፡በጀርባዬ፡ላይ፡አረሱ።ትልማቸውንም፡አስረዘሙ።
፬፤ እግዚአብሐር ፡ ጻድቅ ፡ ነው ።
የኃጢአተኞችን ፡ ገመዶች ፡ ቈረጠ ።
፭፤ ይፈሩ ፡ ወደ ፡ ኋላም ፡ ይመለሱ ፡ ፅዮንን ፡ የሚጸሉ ፡ ሁሉ ።
፮፤ እንደ ፡ ሰገነት ፡ ሣዕር ፡ ይሁኑ ። ሳይታጨድ ፡ እንደሚደርቅ ።
፯፤ አርሱንም ፡ የሚያጭድ ፡ እጁን ፡ እንደማይመላ ።
ብብቱንም ፡ የማይመላ ፡ ነዶውን ፡ ለሚያሥር ።
፰፤ መንገድም ፡ የሚያልፉ ፡ የእግዚአብሐር ፡ በረከት ፡
ከላንት ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡ አይሉም ።
መረቅናችሁ ፡ በእግዚአብሐር ፡ ስም ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፤

፩፤ ከጥልቅ ፡ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ፡ አቤቱ ።
፪፤ አቤቱ ፡ ቃሌን ፡ ስማ ።
ጆሮችኽ ፡ የልመናዬን ፡ ነገር ፡ የሚያደምፁ ፡ ይሁኑ ።
፫፤ ኃጢአትንስ፡ብትጠባበቅ፡አቤቱ። አቤቱ፡ማን፡ይቆማል።
፬፤ ይቅርታ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ ሰዎች ፡ ይፈሩኽ ፡ ዘንድ ።
፭፤ እግዚአብሐርን፡ተስፋ፡አደረግሁ።ነፍሴ፡ተስፋ፡አደረገች።
በነገሩም ፡ ታመንሁ ።
፮፤ ነፍሴ ፡ ለእግዚአብሐር ፡ ታገሠች ፡
ንጋትን ፡ ከሚጠብቁ ፡ ይልቅ ።
ንጋትን ፡ ከሚጠብቁ ፡ ይልቅ ።



፯፤ እሥራኤል ፡ በእግዚአብሐር ፡ ይታመን ።
ጸጋ ፡ በእግዚአብሐር ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡
ከርሱም ፡ ብዙ ፡ መደኀን ፡ ነውና ።
፰፤ እርሱም ፡ እሥራኤልን ፡ ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ያድናል ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፩፤

፩፤ አቤቱ ፡ ልቤ ፡ አይታበይብኝም ።
ዓይኖቼም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አይሉብኝም ።
ታላቂቱን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አላሰብሁም ፡
ከኔም ፡ የሚበልጠውን ፡ ነገር ።
፪፤ ነፍሴን ፡ አረጋሁ ፡ እንጅ ፡ ዝምም ፡ አሰኘኋት ፡
የናቱን ፡ ጡት ፡ እንደስተዉት ።
የናቱን ፡ ጡት ፡ እንደስተዉት ፡ ነፍሴ ፡ በኔ ፡ ሆነች ።
፫፤ እሥራኤል ፡ በእግዚአብሐር ፡ ይመን ፡
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ለዘላለም ።

---

## ህያ ፡ ስምንተኛ ፡ ቀን ።

### የጽዋት ፡ ጸሎት ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፪፤

፩፤ አቤቱ ፡ ደዊትን ፡ አስብ ፡ መከራውንም ፡ ሁሉ ።
፪፤ ለእግዚአብሐር ፡ እንደ ፡ ማለ ።
ለያዕቆብ ፡ ግረምም ፡ እንደ ፡ ተሳለ ።
፫፤ በውነት ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ድንኳን ፡ አልገባም ፡ ብሎ ።
ወደ ፡ ምንጻፊም ፡ አልጋ ፡ አልወፃም ።
፬፤ ላይኔም ፡ ምኝታ ፡ አልሰጥም ፡ ለቅንድቤም ፡ እንቅልፍ
፭፤ ለእግዚአብሐር ፡ ስፍራ ፡ እስካገኝ ፡ ድረስ ፡
ለያዕቆብ ፡ ግረምም ፡ ማደሪያ ።
፮፤ እነሆ ፡ በኤፍራታ ፡ ሰማናት ።
በዱንም ፡ ምድረ ፡ በዷ ፡ አገኘናት ።
፯፤ ወደ ፡ ማደርዮቹ ፡ እንግባ ፡
በግሮቹም ፡ መቀመጫ ፡ እንስገድለት ።
፰፤ ተነሣ፡አቤቱ፡ወደ፡ዕረፍትኽ።አንተ፡የኃይልኽም፡ታቦት።

፱፡ ካህናቶችኽ ፡ ጽድቅን ፡ ይልበሱ ፡
ቅዱሳንህም ፡ እልል ፡ ይበሉ ::
፲፡ ስለ፡ዳዊት፡ስለ፡ባርያኽ::የመሢኽኽን፡ፊት፡አትመልስ::
፲፩፡ እግዚአብሔር ፡ ለዳዊት ፡ በውነት ፡ ማለ ፡ አያብልምም ፡ በርሱ ::
ከሆድኽ ፡ ፍሬ ፡ በዙፋንኽ ፡ ላይ ፡ አስቀምጣለሁ ፡ ብሎ ::
፲፪፡ ልጆችኽ ፡ ኪዳኔን ፡ ቢጠብቁ ፡
እርስዋንም ፡ የማስተምራቸውን ፡ ምስክሬን ::
ልጆቻቸው፡ደግሞ፡በዙፋንኽ፡ላይ፡ለዘላለም፡ይቀመጣሉ::
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ ፅዮንን ፡ መርጽዋልና ::
ለርሱም ፡ ለማደርያ ፡ ወድዋታልና ::
፲፬፡ ይህች ፡ ማረፊያዬ ፡ ናት ፡ ለዘላለም ፡ ብሎ ::
ከዚኽ ፡ አድራለሁ ፡ መርጫታለሁና ::
፲፭፡ ቀለብዋን ፡ አጅግ ፡ አባርካለሁ ::
ድኆችዋንም ፡ እንጀራ ፡ አጸግባለሁ ::
፲፮፡ ካህናትዋንም ፡ መድኃኒት ፡ አለብሳቸዋለሁ ::
ቅዱሳንዋም ፡ በደስታ ፡ እልል ፡ ይላሉ ::
፲፯፡ ከዚያ ፡ ለዳዊት ፡ ቀንድን ፡ አበቅላለሁ ::
መብራትንም ፡ አዘጋጀሁ ፡ ቀብቼ ፡ ላነገሥሁት ::
፲፰፡ ጸላቶቹንስ ፡ እፍረት ፡ አለብሳቸዋለሁ ::
በርሱ ፡ ግን ፡ አክሊሉ ፡ ታበባለች ::

## መዝሙር ፡ ፻፴፫፡

፩፡ እነሆ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እጅግም ፡ ያመረ ፡ ነው ፡
ወንድሞች ፡ ባንድ ፡ ቢቀመጡ ::
፪፡ እንደ ፡ መልካም ፡ ሽቱ ፡ በራስ ፡ ላይ ::
በፅም ፡ ላይ ፡ እንደሚወርድ ፡ በሐሮን ፡ ፅም ::
በልብሱ ፡ ዘርፍ ፡ እንደሚወርድ ::
፫፡ በፅዮን ፡ ተራሮችም ፡ ላይ ፡ እንደሚወርድ ፡ እንደርሞንዔም ፡ ጠል ::
ከዚያ ፡ እግዚአብሔር ፡ በረከቱን ፡ አዝዋልና ፡
ሕይወትንም ፡ ለዘላለም ::



## መዝሙር ፡ ፻፴፬፡

፩፡ እነሆ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ፡ ሁላችሁ ::
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በሌሊት ፡ የምትቆሙ ::
፪፡ በመቅደስ፡እጆችሁን፡አንሡ፡እግዚአብሔርንም፡ባርኩ::
፫፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ የፈጠረ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከፅዮን ፡ ይባርክኽ ::

## መዝሙር ፡ ፻፴፭፡

፩፡ ሀሌሉያ :: የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ አመስግኑ ::
እላንት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ፡ ሆይ ፡ አመስግኑት ::
፪፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የምትቆሙ ፡
ባምላካችን ፡ ቤት ፡ ስፍራ ::
፫፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነውና ::
ለስሙ ፡ ዝማሬ ፡ አቅርቡ ፡ ያመራልና ::
፬፡ እግዚአብሔር ፡ ያዕቆብን ፡ ለርሱ ፡ መርጾታልና ፡
እሥራኤልንም ፡ ለመዝገቡ ::
፭፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቃያለሁና ፡
ጌታችንም ፡ ካምላኮች ፡ ሁሉ ፡ ይበልጣል ::
፮፡ እግዚአብሔር ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ አድርጓልና ፡ በሰማይና ፡ በምድር ::
በባሕርም ፡ በቀላይም ፡ ሁሉ ::
፯፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ ጉም ፡ ያወጣል ፡
መብረቅን ፡ ለዝናም ፡ ያደርጋል ::
ነፋሳትንም ፡ ከመዝገቡ ፡ ያወፃል ::
፰፡ የምስርን ፡ የበኩር ፡ ልጅች ፡ የመታ ፡
ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ::
፱፡ ታምራትንም፡ድንቅንም፡ሰደደ፡በማኸልሽ፡ምስር፡ሆይ::
በፈርዖን ፡ ላይ ፡ በባሮቹም ፡ ሁሉ ::
፲፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ የመታ ፡ ብርቶችንም ፡ ነገሥት ፡ የገደለ ::
፲፩፡ ሲሆንን ፡ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ዖግንም ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ::

የከነዓንንም ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ።
፲፪፤ ምድራቸውንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሰጠ ።
ለእሥራኤል ፡ ርስት ፡ ለሕዝቡ ።
፲፫፤ ስምኽ ፡ አቤቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ።
ዝክርኽም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፲፬፤ እግዚአብሔር፡ለወገኑ፡ይፈርድልና።ለባሮቹም፡ያዝናል።
፲፭፤ የአሕዛብ ፡ ጣዖታት ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ናቸው ። የሰው ፡
እጅም ፡ ስራ ።
፲፮፤ አፍ ፡ አላቸው ፡ አይናገሩም ።
ዓይንም ፡ አላቸው ፡ አያዩምም ።
፲፯፤ ጆሮም ፡ አላቸው ፡ አያደምጹምም ።
እስትንፋስም ፡ ባፋቸው ፡ የለምና ።
፲፰፤ እንደርሳቸው ፡ ይሆናሉ ፡ የሚያደርጓቸው ።
የሚታመኑባቸውም ፡ ሁሉ ።
፲፱፤ የእሥራኤል ፡ ቤት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ።
የሐሮን ፡ ቤትም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ።
፳፤ የሌዊ ፡ ቤትም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ።
፳፩፤ በየሩሳሌም ፡ የሚያድር ፡ እግዚአብሔር ፡
ከፅዮን ፡ የተባረከ ፡ ነው ። ሀሌሉያ ።

## የማታ ፡ ጸሎት ።

### መዝሙር ፡ ፻፴፮፤

፩፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ።
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፪፤ ያምላኮችን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፫፤ የጌቶችን ፡ ጌታ ፡ አመስግኑ ።
ምሕረቱ ፡ ላዘላለም ፡ ነውና ።
፬፤ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ታላቅ ፡ ድንቅ ፡ ያደረገውን ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።



፭፤ ሰማያን ፡ በብልሃት ፡ የሰራ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፮፤ ምድርን ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ የዘረጋ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፯፤ ታላላቆችን ፡ ብርሃናችን ፡ የፈጠረ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፰፤ ፀሐዩን ፡ በቀን ፡ ሊያሠለጥነው ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፱፤ ጨረቃውንና፡ከዋክብትንም፡በሌት፡ሊያሠለጥናቸው።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፤ የምስርን ፡ ሰዎች ፡ በበኽር ፡ ልጆቻቸው ፡ የመታ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፩፤ እሥራኤልንም ፡ ከመኻከላቸው ፡ ያወፃ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፪፤ በጸናች ፡ እጅ ፡ በተዘረጋችም ፡ ክንድ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፫፤ የኤርትራን ፡ ባሕር ፡ ለክፍሎች ፡ የከፈለ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፬፤ እሥራኤልንም ፡ በውስጡ ፡ ያሳለፈ ።
ምሕረቱ ፡ አዘላለም ፡ ነውና ።
፲፭፤ ፈርዖንን ፡ ሠራዊቱንም ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ የገለበጠ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፮፤ ሕዝቡን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የመራ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፯፤ ታላላቆችን ፡ ነገሥታት ፡ የመታ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፰፤ ክቡራንንም ፡ ነገሥታት ፡ የገደለ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፲፱፤ ሲሆንን ፡ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፤ ዖግንም ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

፳፩ ምድራቸውንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ የሰጠ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፪ ለእሥራኤል ፡ ለባርያው ፡ ርስት ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፫ እኛን ፡ በመዋረዳችን ፡ ጊዜ ፡ ያሰበን ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፬ ከጸላቶቻችንም ፡ የለየን ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፭ ምግብ ፡ የሚሰጥ ፡ ለሥጋ ፡ ሁሉ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፮ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ።
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

መዝሙር ፡ ፻፴፯ ፡

፩ በባቢሎን ፡ ወንዞች ፡ ከዚያ ፡ ተቀመጥን ።
ፅዮንንም ፡ ባሰብናት ፡ ጊዜ ፡ አለቀስን ።
፪ በውስጥዋ ፡ ባለ ፡ ዛፍ ፡ መሰንቆቻችንን ፡ ሰቀልን ።
፫ ከዚያ ፡ የማረኩን ፡ ቅኔን ፡ ፈልገውብናልና ።
የሚነዱንም ፡ ደስታ ፡
ከጽዮን ፡ ቅኖች ፡ አንዱን ፡ ቅኙልን ፡ ብለው ።
፬ እንዴት፡የእግዚአብሔርን፡ቅኔ፡በንግዳ፡ምድር፡እንቀኛለን።
፭ ብረሳሽስ ፡ የሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ ቀኜ ፡ ትርሳኝ ።
፮ ባላስብሽ ፡ መላሴ ፡ ባንደበቴ ፡ ይጣበቅ ።
የሩሳሌምን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባላደርጋት ፡ በሌላ ፡ ደስታዬ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ።
፯ አስብ ፡ አቤቱ ፡ የኤዶምን ፡ ልጆች ፡ በየሩሳሌም ፡ ቀን ፡
ፈቃት ፡ ፈቃት ፡ እስከ ፡ መሠረትዋ ፡ ድረስ ፡ ፈቃት ፡ ያል
ዋትን ።
፰ አንች ፡ የምትፈርሽ ፡ የባቢሎን ፡ ልጅ ።
ያደርግሽብነን ፡ ብድራት ፡ የሚመልስብሽ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው።
፱ ሕፃናትሽን፡ይዞ፡በጭንጫ፡የሚደቍሳቸው፡ምስጉን፡ነው።



መዝሙር ፡ ፻፴፰ ፡

፩ ከለልቢ ፡ አመሰግንኻለሁ ። ባማልክትም ፡ ፊት ፡ እዘም
ርልኻለሁ ።
፪ ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ መቅደስ ፡ እሰግድልኻለሁ ፡
ስምህንም ፡ ስለ ፡ ጸጋህና ፡ ስለ ፡ እውነትህ ፡ አመሰግናለሁ ።
ስለ ፡ ስምህ ፡ ሁሉ ፡ የነገርሀውን ፡ ነገር ፡ ታላቅ ፡ አድርገኻልና ።
፫ በጸራሁኽ ፡ ቀን ፡ መለስህልኝ ።
በነፍሴም ፡ ኀይል ፡ ሰጥተኽ ፡ ልብ ፡ አደረግህልኝ ።
፬ የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ አቤቱ ፡ ያፏኽን ፡ ነገር ፡ ሰ
ምተው ፡ ያመሰግኑሃል ።
፭ በእግዚአብሔርም ፡ መንገድ ፡ ይቀኛሉ ።
የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ታላቅ ፡ ናትና ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነውና ፡ ዝቅ ፡ ያለውንም ፡ ያያል ።
የታበየውንም ፡ ከሩቅ ፡ ያውቃል ።
፯ በመከራ ፡ ማኽል ፡ እንኳ ፡ ብሔድ ፡ አንተ ፡ ታድነኛለኽ ።
በጸላቶቼ ፡ ቍጣ ፡ ላይ ፡ እጅኽን ፡ ትዘረጋለኽ ፡
ቀኝኽም ፡ ታድነኛለች ።
እግዚአብሔር ፡ ጕዳዬን ፡ ይፈጽማል ፡
፰ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ ምሕረትህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡
የጅኽን ፡ ስራ ፡ ቸላትበል ።

---

ህያ ፡ ዘጠኝኛ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፻፴፱ ፡

፩ አቤቱ ፡ አንተ ፡ መረመርኸኝ ፡ አወቅኸኝም ።
፪ አንተ ፡ መቀመጤን ፡ መነሣቴንም ፡ አወቅኽ ።
አንተ ፡ አሳቤን ፡ ከሩቅ ፡ አስተዋልኽ ።
፫ መንገዴን ፡ ዕረፍቴንም ፡ አንተ ፡ በረበርኽ ።
መንገዴን ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ፈጽመኽ ፡ አወቅኽ ።
፬ አንዲት ፡ ነገር ፡ በመላሴ ፡ የለችምና ፡
አንተ ፡ ፈጽመኽ ፡ የማታውቃት ፡ አቤቱ ።

፭፡ በፊትና ፡ በኋላ ፡ ከበብኸኝ ፡ እጅኽንም ፡ በላዬ ፡ አደረግኽ ።
፮፡ እውቀትኽ ፡ ትገርመኛለች ።
ትበልጠኝማለች ፡ እደርስላት ፡ ዘንድም ፡ አይቻለኝም ።
፯፡ ወዴት ፡ እሔዳለሁ ፡ ከመንፈስኽ ።
ከፊትኽም ፡ ወዴት ፡ እሸሻለሁ ።
፰፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ብወፃ ፡ አንተ ፡ ከዚያ ፡ ነኽ ።
በሲኦልም ፡ ባነጽፍልኝ ፡ እነሆኽ ፡ አንተ ፡ ከዚያም ፡ ነኽ ።
፱፡ የጽዋትን ፡ ክንፎች ፡ ብወስድ ፡
እስከ ፡ ባሕር ፡ ዳርም ፡ ብቀመጥ ።
፲፡ ከዚያም ፡ እጅኽ ፡ ትመራኛለች ፡
ቀኝኽም ፡ ትይዘኛለች ።
፲፩፡ በውነት ፡ ጨለማ ፡ ትሰውረኝ ፡ ብዬ ፡ ብል ፡
ሌትም ፡ በዙርያዬ ፡ ብርሃን ፡ ትሆናለች ።
፲፪፡ ጨለማም ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ አይጨልምምና ፡
ሌሊቱም ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ ያበራል ።
እንደ ፡ ጨለማ ፡ እንደሁም ፡ ብርሃኑ ፡ ነው ።
፲፫፡ አንተ ፡ ኵላሊቴን ፡ ገዝተኻልና ፡
በናቴም ፡ ሆድ ፡ ሰውረኸኛልና ።
፲፬፡ አመሰግንኻለሁ ፡ አቤቱ ፡ ገረምና ፡ ድንቅ ፡ ሁኜ ፡ ተፈጥ
ርያለሁና ።
ስራኽ ፡ ድንቅ ፡ ናት ፡ ነፍሴም ፡ እጅግ ፡ ታውቃታለች ።
፲፭፡ በስውር ፡ በተሰራሁ ፡ ጊዜ ፡ አጥንቴ ፡ ካንተ ፡ አልተሰወረም ።
አካሌም ፡ በብልሃት ፡ በምድር ፡ ታች ፡ በተሰራ ፡ ጊዜ ።
፲፮፡ የፍጥረቴን ፡ መጀመርያ ፡ ዓይኖችኽ ፡ አዩ ፡
በመጽሐፍኽም ፡ ቀኖቼ ፡ ሁሉ ፡ ተጻፉ ፡
ተፈጠሩም ፡ ከርሳቸው ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ሳይኖር ።
፲፯፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እጅግ ፡ ከበረ ፡ አሳብኽ ፡ ሁሉ ፡
አቤቱ ።
ቍጥሩም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደበዛል ።
፲፰፡ ብቈጥረው ፡ ካሸዋ ፡ ደበዛል ።
ትነሣሁ ፡ እኔም ፡ ደግሞ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ነኝ ።
፲፱፡ አንተ ፡ በውነት ፡ ኃጥኣንን ፡ ትገድላለኽ ፡ አቤቱ ።



የደም ፡ ሰዎች ፡ ከኔ ፡ ፈቀ ፡ በሉ ።
፳፡ በተንኰል ፡ ደናገሩብኻል ፡
አገሮችኽን ፡ በከንቱ ፡ ደወሰዱ ፡ ዘንድ ።
፳፩፡ የሚጸሉኽን ፡ የጸላሁ ፡ አይደለሁምን ፡ አቤቱ ።
በሚነሡብህም ፡ እደክማለሁ ።
፳፪፡ ፍጹም ፡ ጽል ፡ ጸላኋቸው ። ጸላቶችም ፡ ሆኑኝ ።
፳፫፡ ምርመረኝ ፡ አቤቱ ፡ ልቤንም ፡ እወቅ ።
ፈትነኝ ፡ አሳቤንም ፡ እወቅ ።
፳፬፡ ክፉ ፡ መንገድም ፡ እንደለብኝ ፡ እይ ።
የዘላለሙንም ፡ መንገድ ፡ ምራኝ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፡

፩፡ ከክፉ ፡ ሰው ፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ። ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ ጠብቀኝ ።
፪፡ በልባቸው ፡ ክፉ ፡ ያሰቡ ፡
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ለሰልፍ ፡ የሚከማቹ ።
፫፡ መላሳቸውን ፡ እንደ ፡ ባብ ፡ ሳሉ ።
በከንፈራቸው ፡ ታች ፡ የባብ ፡ መርዝ ፡ ነው ።
፬፡ ከኃጢአተኛ ፡ እጅ ፡ ጠብቀኝ ፡ አቤቱ ።
ከግፈኞችም ፡ ጠብቀኝ ።
ሰኰናዬን ፡ ሊያሰናክሉ ፡ የመከሩ ።
፭፡ ትቢተኞች ፡ ወጽመድ ፡ ሸሸጉብኝ ፡ ገመድም ።
ለግሬ ፡ መርበብን ፡ ዘረጉ ፡ በመንገዴ ፡ አጸገብ ።
ወጽመድንም ፡ አኖሩብኝ ።
፮፡ እግዚአብሔርንም ፡ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ፡ አልሁት ።
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ አድምፅ ፡ አቤቱ ።
፯፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ የመድኃኒቴ ፡ ጕልበት ።
በሰልፍ ፡ ቀን ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ ሰወርኽ ።
፰፡ ለኃጢአተኞች ፡ መውደድ ፡ አሳልፈኽ ፡ አትስጠኝ ፡ አቤቱ ።
በላዬ ፡ ተማከሩ ። አተወኝ ፡ እንደደጊደዱ ።
፱፡ የሚከቡኝን ፡ የከንፈራቸው ፡ ድካም ፡ ደቀበራቸው ፡
በራሳቸው ፡ ላይ ።
፲፡ የሳት ፡ ፍም ፡ ደውደቅባቸው ። ወደ ፡ ታች ፡ ደጣላቸው ፡

ወደ ፡ ጉድጓድም ፡ አይንሡምም ፡፡
፲፩ ሁለት ፡ መላስ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አይጸናም ፡፡
ግፈኛን ፡ ሰው ፡ ክፉ ፡ ለጥፋት ፡ ያድነዋል ፡፡
፲፪ እኔ ፡ ግን ፡ አወቅሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለችጋረኞች ፡ ፍርድ ፡
ለድሆችም ፡ በቀል ፡ እንዲያደርግ ፡፡
፲፫ ጻድቃንም ፡ ስምኽን ፡ ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ ፡፡
ቅኖች ፡ በፊትኽ ፡ ይኖራሉ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፵፩

፩ አቤቱ ፡ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ፈጠንልኝ ፡፡
ቃሌንም ፡ አድምፅ ፡ ወደንተ ፡ ስጮኽ ፡፡
፪ ጸሎቴ ፡ በፊትኽ ፡ እንደጣን ፡ ትቅና ፡፡
የጄም ፡ መነሣት ፡ የሰርክ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሁን ፡፡
፫ ለፌ ፡ ጠባቂን ፡ አድርግ ፡ አቤቱ ፡፡
የከንፈሮቼንም ፡ ደጅ ፡ ጠብቅ ፡፡
፬ ልቤን ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትመልስ ፡
ከበደለኞች ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አደራረጌን ፡ ባመፃ ፡ ለማደራረግ ፡
ከሚያመርላቸውም ፡ መብል ፡ እንዳልበላ ፡፡
፭ ጻድቅ ፡ ይምታኝ ፡ ቸርነት ፡ ነውና ፡
ይዝለፈኝም ፡ እንደ ፡ ቅቤ ፡ ለራሴ ፡ ነውና ፡
ራሴን ፡ አይሰበር ፡ እንጂ ፡
ገና ፡ በመከራቸው ፡ እጸልይላቸዋለሁና ፡፡
፮ ፈራጆቻቸው ፡ በደንጊያ ፡ ተገለበጡ ፡
ነገሬንም ፡ ይሰማሉ ፡ የጸፈጠች ፡ ናትና ፡፡
፯ ሰው ፡ በምድር ፡ እንደሚቈርጥና ፡ እንደሚሰነጥቅ ፡
እንዲሁም ፡ አጽንቶቻችን ፡ ወደ ፡ ሢኦል ፡ አፍ ፡ ተበተኑ ፡
፰ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ዓይኖቼ ፡ ወደንተ ፡ ናቸውና ፡፡
ባንተ ፡ አመንሁ ፡ ነፍሴን ፡ አታርቅ ፡፡
፱ ከሚያጸምዱኝ ፡ ወጥመድ ፡ ጠብቀኝ ፡፡
ኃጢአት ፡ ከሚያደርጉም ፡ መጽመጃ ፡፡
፲ ኃጢአተኞች ፡ በወጥመዳቸው ፡ ይውደቁ ፡፡
እኔ ፡ ልደን ፡ እስካልፍ ፡ ድረስ ፡፡



የማታ ፡ ጸሎት ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፵፪

፩ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮኻለሁ ፡፡
በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እለምናለሁ ፡፡
፪ ልመናዬን ፡ በፊቱ ፡ አፈሳለሁ ፡፡
ጻሬን ፡ በፊቱ ፡ እናገራለሁ ፡፡
፫ መንፈሴ ፡ ባለቀብኝ ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ መንገዴን ፡ አወቅኽ ፡፡
በዚችም ፡ በማልፍበት ፡ መንገድ ፡ ለኔ ፡ ወጥመድ ፡ ሰወሩልኝ ፡፡
፬ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ተመልክቼ ፡ አየሁ ፡ የሚያውቀኝንም ፡ አጣሁ ፡፡
የማመልጥበትም ፡ ስፍራ ፡ ጠፋብኝ ፡፡
ለነፍሴም ፡ የሚጠይቅ ፡ የለም ፡፡
፭ ወደንተ ፡ ጮኽሁ ፡ አቤቱ ፡፡ አንተ ፡ አለኝታዬ ፡ ነኽ ፡ አልሁ ፡፡
አንተም ፡ ፈንታዬ ፡ ነኽ ፡ በሕያዋን ፡ ምድር ፡፡
፮ ወደ ፡ ልመናዬ ፡ አድምፅ ፡ ችጋሬ ፡ በዝታለችና ፡፡
ከሚያሳድዱኝ ፡ አድነኝ ፡ በርትተውብኛልና ፡፡
፯ ነፍሴን ፡ ከግዞት ፡ አውፃ ፡ ለስምኽ ፡ አመሰግን ፡ ዘንድ ፡፡
ጻድቃንም ፡ ይከቡኛል ፡ አንተ ፡ ቸርነት ፡ ታደርግልኛለህና ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፵፫

፩ አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ፡፡ ልመናዬንም ፡ አድምፅ ፡፡
በውነትኽ ፡ መልስልኝ ፡ በጽድቅኽም ፡፡
፪ ከባርያኽ ፡ ጋራም ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ አትግባ ፡፡
ሕያው ፡ ሁሉ ፡ በፊትኽ ፡ ጻድቅ ፡ አይደለምና ፡፡
፫ ጸላት ፡ ነፍሴን ፡ አሳድዋታልና ፡፡
ሕይወቴንም ፡ ለምድር ፡ ደደቀሳታልና ፡፡
በጨለማም ፡ አኑሮኛልና ፡ ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ ሙታን ፡፡
፬ መንፈሴም ፡ በውሥጤ ፡ አለቀብኝ ፡፡ ልቤም ፡ ደነገፀብኝ ፡፡
፭ የቀደመውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ፡፡ በስራኽ ፡ ሁሉ ፡ ተናገርሁ ፡፡
የጅኽንም ፡ ስራ ፡ ደረስሁ ፡፡
፮ እጄን ፡ ወደንተ ፡ ዘረጋሁ ፡፡
ነፍሴም ፡ እንደ ፡ ድርቅ ፡ ምድር ፡ ወደንተ ፡ ተጸማች ፡፡
፯ ፈጥነኽ ፡ ስማኝ ፡ አቤቱ ፡፡ መንፈሴ ፡ ጠፍትዋልና ፡፡

ፊትኽን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ፡
ወደ ፡ ጉድጓድ ፡ እንደሚወርዱ ፡ እንዳልሆን ።
፰፤ ማልደ ፡ ምሕረትኽን ፡ አስማኝ ። አንተን ፡ አምኜለሁና ።
የምሔድባትን ፡ መንገድ ፡ አስታውቀኝ ፡
ነፍሴን ፡ ወደንተ ፡ አንሥቻለሁና ።
፱፤ ከጸላቶቼ ፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ። ወደንተ ፡ ተማጽኜለሁና ።
፲፤ ፈቃድኽን፡ለማድረግ፡አስተምረኝ።አንተ፡አምላኬ፡ነኽና።
በጎ ፡ መንፈስኽም ፡ በቀናች ፡ ምድር ፡ ይምራኝ ።
፲፩፤ ስለ ፡ ስምኽ ፡ አድነኝ ፡ አቤቱ ።
በጽድቅኽም ፡ ነፍሴን ፡ ከመከራ ፡ አውፃ ።
፲፪፤ በጸጋኽም ፡ ጸላቶቼን ፡ ሻር ፡
ነፍሴንም ፡ የሚያሳዝኑትን ፡ ሁሉ ፡ አጥፋቸው ።
እኔ ፡ ባርያኽ ፡ ነኝና ።

ሠሉስ ፡ ቀን ።

የጽዋት ፡ ጸሎት ።

መዝሙር ፡ ፻፵፫፤

፩፤ እግዚአብሔር ፡ አምባዬ ፡ ይባረክ ፡
እጆቼን ፡ ሰልፍ ፡ ጣቶቼንም ፡ ዘምቻውን ፡ የሚያስተምር ።
፪፤ ጸጋዬም ፡ መጸጊዬም ፡ መሸሸግያዬም ፡
ረጂም ፡ የታመንሁበትም ፡ ጋሻዬ ፡
ሕዝቤንም ፡ በታቼ ፡ የሚያስገዛ ።
፫፤ አቤቱ ፡ ሰው ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ እርሱን ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ።
የሰው ፡ ልጅስ ፡ ታስብለት ፡ ዘንድ ።
፬፤ ሰው ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ይመስላል ።
ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ጽላ ፡ ያልፋል ።
፭፤ አቤቱ ፡ ሰማዮችኽን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አድርግ ፡ ውረድም ።
ተራሮችን ፡ ዳስ ፡ ይጠሱም ።
፮፤ መብረቅኽን ፡ አብርቅ ፡ በትናቸውም ።
ፍላጾችኽን ፡ ላክ ፡ አጥፋቸውም ።
፯፤ እጅኽን ፡ ከላይ ፡ ላክ ፡ አድነኝም ፡
ከብዙ ፡ ውኃም ፡ አስጥለኝ ።



ከንግዶች ፡ ልጆች ፡ እጅ ።
፰፤ አፋቸው ፡ በምናምን ፡ የተናገረ ፡
ቀኛቸውም ፡ ያበተ ፡ ቀኝ ፡ ያለች ።
፱፤ አዲስ ፡ ቅኔን ፡ እቀኝልኻለሁ ፡ አቤቱ ፡
አሥር፡አውታር፡ባለውም፡በበገና፡እቃ፡እዘምርልኻለሁ።
፲፤ ለነገሥት ፡ መድኃኒት ፡ የምትሰጥ ።
ዳዊትን ፡ ባርያውን ፡ ከክፉ ፡ ሰይፍ ፡ ያደነው ።
፲፩፤ አድነኝ ፡ ታደገኝም ፡ ከንግዶች ፡ ልጆች ፡ እጅ ።
አፋቸው ፡ በምናምን ፡ የተናገረ ፡
ቀኛቸውም ፡ ያበተ ፡ ቀኝ ፡ ያለች ።
፲፪፤ ልጆቻችን ፡ እንደታክልት ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ።
በጕልማስነታቸው ፡ የበቀሉ ።
ሴቶች ፡ ልጆቻችንም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ እንደሉ ፡
እንደ ፡ ተጸረቡም ፡ እንደ ፡ ማዝን ፡ ደንጎች ።
፲፫፤ ጕተራችንም ፡ እኽል ፡ ሁሉ ፡ ይመላ ፡ ዘንድ ።
በጎቻችንም ፡ ባደባባያችን ፡ አእላፋትን ፡ ይወልዱ ፡ ዘንድ ።
፲፬፤ በሮቻችንም ፡ ፍርያሞች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ።
ፍራሽና ፡ መውጫም ፡ ልቅሶም ፡
ባደባባዮቻችን ፡ እንዳይኖር ፡
፲፭፤ እንዲህ ፡ ያለች ፡ ሕዝብ ፡ የተመሰገነች ፡ ናት ።
እግዚአብሔር ፡ አምላክዋ ፡ የሆነላት ፡ ሕዝብ ፡
እርስዋ ፡ የተመሰገነች ፡ ናት ።

መዝሙር ፡ ፻፵፬፤

፩፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግኻለሁ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ።
ስምኽንም ፡ እባርካለሁ ፡ ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ።
፪፤ ቀን ፡ ሁሉ ፡ እባርክኻለሁ ።
ስምኽንም ፡ ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ፡ አመሰግናለሁ ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ እጅግም ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።
ለታላቅነቱም ፡ ጫሪሽ ፡ የላትም ።
፬፤ ትውልድ ፡ ለትውልድ ፡ ስራኽን ፡ያመሰግናሉ ።
በጕልበትኽም ፡ ያወራሉ ።

፭፡ በምስጋናኽ ፡ ክብር ፡ ገናንነት ፡ በድንቅኽም ፡ ነገር ፡ እናገ ራለሁ ።
፮፡ የግርማኽንም ፡ ኃይል ፡ ይናገራሉ ።
ታላቅነትኽንም ፡ አጫውታለሁ ።
፯፡ የቸርነትኽን ፡ ብዛት ፡ መታሰብ ፡ ያወፃሉ ።
በጽድቅም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፰፡ እግዚአብሔር ፡ መሐሪና ፡ ሩሩ ፡ ነው ።
ቍጣው ፡ የዘገየ ፡ ምሕረቱም ፡ የበዛች ።
፱፡ እግዚአብሔር ፡ ለሁሉ ፡ ቸር ፡ ነው ።
ምህረቱም ፡ በስራው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ናት ።
፲፡ አቤቱ ፡ ስራኽ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግንሃል ።
ቅዱሳንኽም ፡ ይባርኩኻል ።
፲፩፡ የመንግሥትኽን ፡ ምስጋና ፡ ይናገራሉ ።
ኃይልኽንም ፡ ያወራሉ ።
፲፪፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ችሎቱን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ።
የመንግሥቱንም ፡ ምስጋና ፡ ጌጽ ።
፲፫፡ መንግሥትኽ ፡ የዘላለምና ፡ ሁሉ ፡ መንግሥት ፡ ናት ።
ግዛትኽም ፡ በትውልድ ፡ ሁሉ ፡ ናት ።
፲፬፡ እግዚአብሔር ፡ የሚወድቁትን ፡ ይደግፈቸዋል ።
ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ ያሉትንም ፡ ያነሣል ።
፲፭፡ የሁሉ ፡ ዓይን ፡ አንተን ፡ ይቈያል ።
አንተም ፡ ምግባቸውን ፡ በየጊዜያቸው ፡ ትሰጣቸዋለኽ ።
፲፮፡ አንተ ፡ እጅኽን ፡ ትከፈታለኽ ።
ሕያውንም ፡ ሁሉ ፡ ደስታ ፡ ታጸግባለኽ ።
፲፯፡ እግዚአብሔር ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ ጻዲቅ ፡ ነው ።
በስራውም ፡ ሁሉ ፡ ቸር ፡ ነው ።
፲፰፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚጸሩት ፡ ሁሉ ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
በውነት ፡ ለሚጸሩት ፡ ሁሉ ።
፲፱፡ የሚፈሩትን ፡ ፈቃድ ፡ ያደርጋል ።
ጩኸታቸውንም ፡ ይሰማል ፡ ያድናቸዋልም ።
፳፡ እግዚአብሔር ፡ የሚወዱትን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃል ።
ኃጢአተኞችንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋል ።



፳፩፡ አፌ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ይናገራል ።
ሥጋም ፡ ሁሉ ፡ የተቀደሰውን ፡ ስሙን ፡ ይባርክ ፡
ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ፡ ሁሉ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፮፡

፩፡ ሀሌሉያ ። ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ።
፪፡ እግዚአብሔርን ፡ በሕይወቴ ፡ አመሰግናለሁ ።
ላምላኬም ፡ እዘምራለሁ ፡ በምኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ።
፫፡ ተስፋችሁን ፡ ባለቆች ፡ አታድርጉ ።
በሰው ፡ ልጅም ፡ ማዳን ፡ በማይችል ።
፬፡ ነፍሱ ፡ ትወፃለች ፡ ወደ ፡ መሬቱም ፡ ይመለሳል ።
በዚያን ፡ ቀን ፡ ትምክሕቱ ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
፭፡ የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ረዳቱ ፡ የሆነ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፡
ተስፋው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ባምላኩ ፡ የሆነ ።
፮፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ የፈጠረ ፡
ባሕርን ፡ በርሳቸው ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡
እውነትንም ፡ ለዘላለም ፡ የሚጠብቅ ።
፯፡ ለተበደሉ ፡ የሚፈርድ ። ለተራቡም ፡ ምግብን ፡ የሚሰጥ ።
እግዚአብሔር ፡ የታሠሩትን ፡ ይፈታል ።
፰፡ እግዚአብሔር ፡ የዕውሮችን ፡ ዓይን ፡ ይከፍታል ።
እግዚአብሔር ፡ የጐነበሱትን ፡ ያነሣል ።
እግዚአብሔር ፡ ጻድቃንን ፡ ይወዳል ።
፱፡ እግዚአብሔር ፡ ስደተኞችን ፡ ይጠብቃል ።
አባትና ፡ እናት ፡ የሌላቸውንም ፡ ባልቴቲቱንም ፡ ይቀበላል ።
የኃጢአተኞችን ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ያስጠማል ።
፲፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ።
አምላክሽ ፡ ፅዮን ፡ ሆይ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ። ሀሌሉያ ።

የ ማ ታ ፡ ጸ ሎ ት ።
መዝሙር ፡ ፻፵፯፡

፩፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
ላምላካችን ፡ መዝመር ፡ መልካም ፡ ነውና ፡
ምስጋናውም ፡ ያምራልና ።

፪፤ እግዚአብሔር ፡ የሩሳሌምን ፡ ይሠራል ።
ከእሥራኤልም ፡ የተበተኑትን ፡ ይሰበስባል ።
፫፤ ልባቸው ፡ የተሰበረውን ፡ የሚፈውስ ።
ሕማማቸውንም ፡ የሚጠግን ።
፬፤ የከዋክብትን ፡ ብዛት ፡ የሚቈጥር ።
ለሁላቸውም ፡ ስም ፡ ያወጣላቸዋል ።
፭፤ ጌታችን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ጉልበቱም ፡ እጅግ ፡ ናት ።
ለብልሃቱም ፡ ቍጥር ፡ የላትም ።
፮፤ እግዚአብሔር ፡ ቸጋሮችን ፡ ያነሣል ።
ኃጢአተኞችንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ያዋርዳል ።
፯፤ ለእግዚአብሔር ፡ በምስጋና ፡ ዘምሩ ።
ላምላካችንም ፡ በመሰንቆ ፡ ዝማሬን ፡ አቅርቡ ።
፰፤ ሰማዩን ፡ በደመናት ፡ የሚሸፍን ።
ለምድርም ፡ ዝናም ፡ የሚያዘጋጅ ።
ሣርንም ፡ በተራሮች ፡ የሚያበቅል ።
፱፤ ለእንስሳይቱም ፡ ምግብዋን ፡ የሚሰጥ ።
ለሚጸሩትም ፡ ለቍሮች ፡ ጫጩቶች ።
፲፤ የፈረስ ፡ ኃይል ፡ ደስ ፡ አያሰኘውም ።
በሰው ፡ ጭንም ፡ አይወድም ።
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ በሚፈሩት ፡ ይወደል ፡ እንጅ ።
በምሕረቱም ፡ በሚታመኑ ።
፲፪፤ የሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ።
ፅዮንም ፡ ለአምላክሽ ፡ እልል ፡ በይ ።
፲፫፤ የደጆችሽን ፡ መወርወሪያ ፡ አጽንትዋልና ።
ልጆችሽንም ፡ በውሥጥሽ ፡ ባርኳልና ።
፲፬፤ በወሰንሽም ፡ ደህንነትን ፡ የሚሰጥ ።
የስንዴ ፡ ስብም ፡ የሚያጸግብሽ ።
፲፭፤ ነገሩን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ የሚሰድ ።
ቃሉም ፡ እጅግ ፡ ፈጥኖ ፡ ይሮጣል ።
፲፮፤ በረዶውን ፡ የሚሰጥ ፡ እንደ ፡ ባዘቶ ።
ውርጭን ፡ እንደመድ ፡ የሚበትነው ።
፲፯፤ ውርጩንም ፡ እንደ ፡ ቍራሾች ፡ የሚሰጥ ።



በብርዱ ፡ ፊትም ፡ ማን ፡ ይቆማል ።
፲፰፤ ቃሉን ፡ ይልካል ፡ ያቀልጠውማል ።
ነፋሱን ፡ ይመልሳል ፡ ውኆችም ፡ ይፈሳሉ ።
፲፱፤ ቃሉን ፡ ለያዕቆብ ፡ የነገረ ።
ሕጉንና ፡ ፍርዱንም ፡ ለእሥራኤል ።
፳፤ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንደሀ ፡ አላደረገም ።
ፍርዱንም ፡ አላወቁም ። እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ።

መዝሙር ፡ ፻፵፰፤

፩፤ ሀሌሉያ ። እግዚአብሔርን ፡ ከሰማዮች ፡ አመስግኑት ።
በከፍታዎችም ፡ አመስግኑት ።
፪፤ አመስግኑት ፡ መላእክቱ ፡ ሁሉ ።
አመስግኑት ፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ።
፫፤ አመስግኙው ፡ ፀሐይ ፡ ሆይ ፡ ጨረቃይቱም ።
አመስግኑት ፡ እላንት ፡ የብርሃን ፡ ከዋክብት ፡ ሁሉ ።
፬፤ የሰማዮች ፡ ሰማዮች ፡ አመስግኑት ።
ከሰማዮችም ፡ በላይ ፡ ያሉ ፡ ውኆች ።
፭፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑ ።
እርሱ ፡ ብልዋልና ፡ ተፈጠሩም ።
፮፤ ለዘላለሙም ፡ ለፍጻሜውም ፡ አቆማቸው ።
ትእዛዝ ፡ አኖረላቸው ፡ እርስዋንም ፡ አያልፏም ።
፯፤ እግዚአብሔርን ፡ ከምድር ፡ አመስግኑ ።
እባቦች ፡ ጥልቆችም ፡ ሁሉ ።
፰፤ እሳትና ፡ በረዶ ፡ ውርጭና ፡ ጽጋግም ።
ዓውሎ ፡ ነፋስም ፡ ነገሩን ፡ የምታደርግ ።
፱፤ ተራሮች ፡ ኮረፍቶችም ፡ ሁሉ ።
የሚያፈራ ፡ ዛፍም ፡ አረዝም ፡ ሁሉ ።
፲፤ አራዊትም ፡ እንስሶችም ፡ ሁሉ ።
ተንቀሳቃሾችም ፡ የሚበሩም ፡ ወፎች ።
፲፩፤ የምድር ፡ ንጉሦችም ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ።
ገዦችም ፡ የምድርም ፡ ፈራጆች ፡ ሁሉ ።
፲፪፤ ጕልማሶችም ፡ ቈነጃጅቱም ፡ ሽማግሎችም ፡ ከእሽከሮ
ች ፡ ጋራ ።

፲፫፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑ ።
ስሙ ፡ ብቻውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብልዋልና ።
ምስጋናውም ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ናት ።
፲፬፤ የሕዝቡንም ፡ ቀንድ ፡ ያነሣል ።
ምስጋና ፡ ለቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ ናት ።
ለእሥራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደርሱ ፡ ለቀረበች ፡ ለሕዝቡ ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ።

### መዝሙር ፡ ፻፵፱፤

፩፤ ሀሌሉያ ። ለእግዚአብሔር ፡ ባዲስ ፡ ቅኔ ፡ ቅኙለት ።
ምስጋናው ፡ በቅዱሳኑ ፡ ጉባዔ ፡ አለች ።
፪፤ እሥራኤል ፡ በፈጣሪው ፡ ደስ ፡ ይበለው ።
የፅዮንም ፡ ልጆች ፡ በንጉሣቸው ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፫፤ ስሙን ፡ በዘፈን ፡ ያመስግኑ ።
በከበሮ ፡ በመሰንቆም ፡ ያዝምሩለት ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ይወደልና ።
ችጋረኞችንም ፡ በመድኃኒት ፡ ያስጌጻል ።
፭፤ ቅዱሳን ፡ በክብር ፡ ይመካሉ ።
በምንጻፈቸው ፡ ላይ ፡ እልል ፡ ይላሉ ።
፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ከፍታ ፡ በጉሮሮቸው ፡ ነው ።
ሁለት ፡ አፍ ፡ ያለው ፡ ሰይፍም ፡ በጃቸው ።
፯፤ በአሕዛብ ፡ በቀል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ።
በሰዎችም ፡ መኻከል ፡ ይወቅሱ ፡ ዘንድ ።
፰፤ ንጉሦቻቸውን ፡ በሰንሰለት ፡ ያሥሩ ፡ ዘንድ ።
ታላላቆቻቸውንም ፡ በብረት ፡ ማሠርዮች ።
፱፤ የተጻፈውን ፡ ፍርድ ፡ ያደርጉባቸው ፡ ዘንድ ።
ለቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ ይኽ ፡ ክብር ፡ ይሆናል ። ሀሌሉያ ።

### መዝሙር ፡ ፻፶፤

፩፤ ሀሌሉያ ። እግዚአብሔርን ፡ በመቅደሱ ፡ አመስግኑት ።
አመስግኑት ፡ በጉልበቱ ፡ ጠፈር ።
፪፤ አመስግኑት ፡ በችሎቱ ። አመስግኑት ፡ በታላቅነቱ ፡ ብዛት ።
፫፤ አመስግኑት ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ።



አመስግኑት ፡ በበገና ፡ በመሰንቆም ።
፬፤ አመስግኑት ፡ በከበሮ ፡ በዘፈንም ።
አመስግኑት ፡ ባውታር ፡ በንቢልታም ።
፭፤ አመስግኑት ፡ ድምፁ ፡ መልካም ፡ ባለ ፡ ጸናጽል ።
አመስግኑት ፡ በልልታ ፡ ጸናጽል ።
፮፤ እስትንፋስ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግን ።
ሀሌሉያ ።

---

የመዝሙራት ፡ መጨረሻ ።

---